

# የሶቭየት ሕብረት ኮሚኒስት ፓርቲ ታሪክ

## ( ቦልሼቪክ )

ትርጉም

በኩራዝ

( ክፍል ፩ )

# የሶቭየት ሕብረት ኮሚኒስት ፓርቲ ታሪክ (ቦልሼቪክ)

## ክፍል ፩



ትርጉም በኩራዝ

፲፱፻፸፱ ዓ. ም.

# ማ ው ጫ

## ምዕራፍ ሶስት

## ሜንሼቪኮችና ቦልሼቪኮች በሩሲያና በጃፓን ጦርነት ወቅት የመጀመሪያው የሩሲያ አብዮት

(1904—1907)







## ምዕራፍ አራት

## ሜንሼቪኮችና ቦልሼቪኮች በስቶልፒን የአድህሮት እንቅስቃሴ ወቅት ፣ ቦልሼቪኮች ራሳቸውን ነጻ ማርክሳዊ ፓርቲ አድርገው ማቋቋማቸው

(1908—1912)

## ምዕራፍ 5

## የቦልሼቪኮች ፓርቲ ከመጀመሪያው የኢምፔሪያሊስት ጦርነት በፊት የሠርቶ አደሩ መደብ አዲስ እንቅስቃሴ ባደረገበት ወቅት

(1912—1914)



## ምዕራፍ 6

## የቦልሼቪክ ፓርቲ በኢምፔሪያሊስት ጦርነት ወቅት፣ ሁለተኛው አብዮት በሩሲያ





## ምዕራፍ ሰባት

## የቦልሼቪክ ፓርቲ በጥቅምቱ ሶሻሊስት አብዮት የዝግጅትና የተግባር መግለጫ ወቅት

(ሚያዝያ 1917—1918)

ምዕራፍ ስምንት

# የቦልሼቪክ ፓርቲ በውጪ ወታደራዊ ጣልቃ ገብነትና በርስ በርሱ ጦርነት ወቅት

(1918—1820)





## መግቢያ

የግል ንብረት ከተመሰረተበት ጊዜ ጀምሮ የሕብረተሰብ ታሪክ የመደብ ትግል ታሪክ ነው ። መደቦችን ስንል ፤ ሌኒን « መደቦች ሰፋ ያሉ የሕብረተሰብ ቡድኖች ሲሆኑ አንዱ ከሌላው የሚለየው በታሪክ በተወሰነ የማህበራዊ አመሰራረት ተግባር ውስጥእያንዳንዳቸውበሚኖራቸውስፍራ (ይበልጡን ጊዜ በሕግ የተደነገገ) ከማምረቻዎች ጋር በሚኖራቸው ግንኙነት ፣ በማህበራዊ የሥራ ድርጅት ውስጥ ባላቸው ሚና ፣ ከዚህም ጋር ተያይዞ ከሚያመነጩት ማህበራዊ ሀብት ውስጥ ድርሻቸውን የሚያገኙበት መንገድና መጠን ነው ። መደቦች በተወሰነ ማህበራዊ ኢኮኖሚ ውስጥ በሚኖራቸው የተለያየ ሥፍራ የተነሳ አንዱ መደብ የሌላውን የድካም ውጤት ንብረት የሚያደርግበት የሰዎች ቡድን ነው ። » ባለው መሰረት በመደቦች መሀከል መራራ መደባዊ ትግል ተደርጓል ፤ እየተደረገም ነው ።

መደቦች እንደ ምርት መሳሪያዎች የእድገት መጠን በተለያየ ገጽና ግንኙነት ሲገለጡ እንደኖሩ ከታሪክ ገድሎች እንረዳለን ። ይህም የመደቦች ህልውና የሚያገኙላልን እውነት ቢኖር በህብረተሰቡ ውስጥ ገዢና ተገዢ ፣ በዝባዥና ተበዝባዥ ፣ እንዲሁም የነዚህ ተቃራኒ ከስተቶች ሕሊናዊ ነጸብራቅ ፣ ርእዮተ-ዓለምና ፖለቲካ... መኖራቸውን ብቻ ሳይሆን በተለያዩ ወቅቶች የተለያዩ አብዮቶች የተለያዩ የትግል መልኮችን የአመራር ስልቶች ፣ የድርጅት ቅርፆችና የነዚህም ፍልሚያ የተለያዩ ውጤቶች እንደተከሰቱና ወደ ፊትም የእድገት ደረጃቸውን ጠብቀው እንደሚከሰቱ በገሀድ ያሳየናል ።

አብዮት ፤ አዲስ ሥርዓትን ላረገዘች ለያንዳንዷ ያረጀችና ያፈጀች ሥርዓት አዋላጅ ሀኪም ናትና ሥርዓተ-ማህበር ሲያረጅ የማምረቻ ሀይሎችን እድገት ይገታል ፤ የምርት ግኑኝነትን ያቃውሳል ። ይሁንና ፍላጎት አይገታምና የአስፈላጊ ነገሮች እጥረት ያስከትላል ። ነባራዊ ሁኔታዎች ፈርጅ እየያዙ ያድጋሉ ። ውሎ አድሮም የግል ጉምጉምታው የጋራ ሁካታ ፣ የግል ንዴት ፣ የአድማጩ ጩኸት ፣ የመንደር ብሽቀት ፣ የድርጅት ግጭት ፣ የንቃተ-ሕሊና ምጥቀት ያስከትላል ። ይህም ማለት ሕሊናዊ ሁኔታዎች በየመልካቸው አመቺ ሁኔታን ይፈጥራሉ ማለት ነው ።

ምዝብር ሕዝቦች ለኤኮኖሚያዊ ጥቅሞች ካደረጉት መራራ ትግል ትምህርት በመቅሰም ፖለቲካዊ ትግሎችን ማራመድ በጀመሩበት ጊዜ ሁሉ ቀድመው መኪናዎችን በመሰባበርና በአሰሪ ግለሰቦች ላይ ከማደም የትግል ዘዴአቸው ተላቀው የተቀነባበረ ፖለቲካዊ የሥራ ማቆም አድማና ትጥቃዊ አመጽ በማካሄድ ፖለቲካዊ ሥልጣን ለመጨበጥ ታግለዋል ።

ጭቁን ሕዝቦች በብዝበዛ ጥፍሮቻቸው ጉሮሮአቸውን አንቀው የሚቦጠ
ቡጧቸውን እፍኝ የማይሞሉ የገዢ መደቦች ገርሥሶ ለመጣል ያልታገ
ሉበት አንዳችም ሀገር፤ከተማ ወይም መንደር አይኖርም ። ይሁን እንጂ
ከንቃቱ ፣ ከድርጅቱና ከትጥቁ ብቃት ማነስ የተነሳ የትግላቸውን ዓላማ
ከግቡ ሳያደርሱ በፋብሪካ ደፎች ፣ በአውራ መንገዶችና በእርሻ ማሳዎች
ኢ-ሰብአዊ በሆነ ጭፍጨፋ ረገፉ ። ታጋዮች ይሙቱ እንጂ ፣ ደም ይፋ
ሰስ፣ መንደር ይታመስ እንጂ፣ አብዮቱ ደግሞ ላያንሰራራ ያከተመበት
አንዲት ጋት የምትሆን ሥፍራ በዓላማችን ከቶም አይኖርም ። ያነገቡት
የደም ሰንደቅ በዘመናዊው ማርክሳዊ-ሌኒናዊ የትግል ትጥቅ ደምቆ፤የማ
ይቀረውን የጭቁን ሕዝቦች አሸናፊነት ለማረጋገጥ ከትውልድ ወደ
ትውልድ ለአዲስና ለሌላ አብዮት ይሸጋገራል ።

እርግጥ ነው ፣ በአለፉት የትግል ሂደቶች በሠራተኛው መደብ ውስጥ
የተለያዩ አዝማሚያዎች በተለያዩ ቦታዎችና ጊዜዎች ውስጥ በተ
ለያዩ መልኮች ተከስተው የትግሉን ሂደት ይበልጥ አስቸጋሪና መራራ
አድርገውታል ። ቢሆንም ቅሉ ትልቁ ቁም ነገር አብዮት ማስተ
ማሩ ነውና ዘግየት ብለው የተካሄዱ አብዮቶች ከቀደምት አብዮቶች
አያሌ ነገሮችን ተምረዋል ። ያልተማሩም ቢኖሩ ፣ አብዮት የምልአተ
ህዝቡ እንቅስቃሴ እንጂ የጥቂት ሰዎች ወይንም ቡድኖች አሻፈረኝ ማለት
አለመሆኑን ያላጤኑ ሁሉ ፣ በዚያው አንጻር ተደምስሰዋል ። የሰው ዘሮ
ችን ለአሰቃቂ እልቂት ዳርገዋል ። አብዮት በራሱ ሕግ የሚመራ እንጂ
ሰዎች በዘፈቀደ የሚያካሂዱት ክስተት አይደለም ። ይህንን ስንል ግን
ሰዎች በአብዮት ላይ ምንም አይነት ተጽእኖ አያሳድሩም ማለታችን
አይደለም ።

ማናቸውም የሕብረተሰብ ለውጥና እድገት የሰፊው ሕዝብ አብዮታዊ
ትግል ውጤት ነው ። ማናቸውም ተራማጅ አስተሳሰቦችና ፍልስፍና
ዎች ከሠርቶ አደሩ ሕዝብ ትግል የመነጩ ሲሆን የሚያንጸባርቁትም
ሰፊው ሕዝብ ለሥርነቀል ለውጦች ያለውን ወደር የለሽ ፍላጐት ነው ።
ማናቸውም ሳይንስና ቴክኖሎጂ ተነጥሮ የወጣው ምዝብር ሕዝቦች በሥ
ራቸው ካገኙት ልምድ ነው ። ሰፊው ሕዝብ የሕብረተሰቡ ታሪክ መስራች
ጸዋሬ ሀይል ነው የምንለው በዚህ ምክንያት ነው ።

የወዝአደሩ መምህራን የሆኑት ካርል ማርክስና ፍሬደሪክ ኤንግልስ
ሕብረተሰብ የራሱ ሕግ እንዳለውና በዚህም ሕግ መሠረት እንደሚመራ
በመግለጽ ኮሚኒስት ማኒፌስቶን ለዓለም ምዝብር ሕዝቦች ትግል ማቅረ
ባቸው ራሱ የሰፊው ሕዝብ የትግል ደረጃ የቱን ያህል ከአለፉት ትግሎቹ
ተምሮ በአዲስ ሳይንሳዊ ትጥቁ ለአዲስና ለዘላቂው ግቡ ለመታገል እንደ
ተሰለፈ ብቻ ሳይሆን ለድል አድራጊነቱ ፣ ለሚታገልለት የኮሚኒስት
ሕብረተሰብ አስተማማኝ መሰረት የመጣሉን ጭምር የሚያበስር ነው ።

ይሁን እንጂ እነዚህ የወዝአደሩ ልሂቃን ትምህርታቸውም ሆነ የዓላ
ማቸው መሳካት ይበልጡን ያተኮረው በምእራብ አውሮፓና በመሀከለ



ኛው አውሮፓ ሠራተኞች ንቅናቄ ላይ ነበር ። ከማርክስ እረፍት በኋላ
የሩስያን ሁኔታ በአንክሮ ይከታተል የነበረው ፍሬደሪክ ኤንግልስ ምንም
እንኳ በሩስያ የከበርቴው ሥርዓት ሥር እየሰደደና እየተንሰራፋ ፣ ከዚሁም
ጋር የወዝአደሩ ቁጥር እያደገ በመሄዱ ከፍተኛ ንቅናቄ መጀመሩ ተስፋ
የሰጠው ቢሆንም የከበርቴው ሥርዓት በሚገባ የተንሰራፋበትን የምእ
ራብ አውሮፓ ወዝአደር ለሶሻሊዝም በር ሌላ ከፋች እንደሚሆን አልተ
ጠራጠረም ነበር ።

የታሰበው ሳይሆን ቀረ ። የጀርመን ከበርቴ አብዮቱን ማጠናቀ
ቁንና በትረ-መንግሥቱን መጨበጥ ትቶ ከባላባቱ ጋር እርቅ በመሻት
በወዝአደሩ ላይ መዶለቱን ቀጠለ ። አብዮት ከሸፈ ። በታሪክ መድረክ ላይ
ብቅ ካሉት የትግል ተውኔቶች የፓሪሱ ኮሚዩን ቀዳሚ የሌለው ይሁን
እንጂ በፈረንሳይ ከበርቴ ክህደትና በጀርመን ከበርቴ አጋርነት የፓሪስ
ሠራተኞች ሕዝባዊ መንግሥት ተደመሰሰ ። የምእራብ አውሮፓ ወዝአደር
የሶሻሊዝም መስራች መሆኑ ቀረና የዚህ ስርዓት አቅኚና መንገድ ከፋች
የሩስያው ወዝአደር ሆነ ። በምእራብ አውሮፓ ማርክሲዝም ሲበረዝ፤በሩ
ስያ ግን የሚያጐለምሰው ፣ የሚያበለጽገው ፣ ሀቀኛ ፍቺውን የሚሰጠው
ሰው አገኘ ። ይህ ታላቅ ሰው ቭላድሚር ኢሊች ኡሊያኖቭ ሌኒን ነበር ።

ሌኒን ፤ የከበርቴ ስርዓት እድገ ከመጨረሻው ደረጃው ከኢምፔሪያ
ሊዝም መድረሱን ቶሎ በመገንዘብ በአዲሱ ሁኔታ አንጻር ማርክሲዝምን
አሳደገው ፤ አበለጸገው ። ለዚህም ነው ሌኒኒዝም የዘመነ ኢምፔሪያሊዝም
ማርክሲዝም ነው የሚባለው ።

ሌኒን ፤ ምን መደረግ አለበት ? በተሰኘው መጽሀፉ ቀደምት ምሁራን
ስለ ወዝአደሩ ፓርቲ የጻፉትን በመመርኮዝ ፤ እንዲሁም የአውሮፓ ወዝአ
ደሮችን ትግል በመመርመርና ከሩስያ ወዝአደሮች ትግል ጋር በማገናዘብ ፤
ልዩነታቸውንና የሚመሳሰሉበትን ነገር በማጤን ፤ የወዝአደሩን ፓርቲ
ሳይንስ አረቀቀ ።

የጥቅምቱን የሩስያ አብዮት የመራው የቦልሼቪክ ፓርቲ በሌኒን
ትምህርት የተኮተኮተ ፣ በሌኒናዊ የፓርቲ ሳይንስ መሠረት የተደራጀ ፣
በአብዮታዊ ዲሲፕሊን የታነጸ የወዝአደር ፓርቲ ነበር ። የሩስያ ጭቁን
ሕዝቦች ትግል በተፋፋመበት ጊዜ በግንባር ቀደምትነት አዳዲስ የትግል
ስልቶችን በመቀየስ ፣ ከህዝቡ ጋር በመዋሃድና በመምራት ትግሉ ጋብ
በሚልበት ጊዜ በማፈግፈግና ሀይሉን ለመጪው ጊዜ ትግል በማዘጋ
ጀት ታላቁን የጥቅምት አብዮት መራ ።

የቦልሼቪክ ፓርቲ ታሪክ ከሌኒን ሕይወት ተገንጥሎ አይታይም ።
ስለሩሲያ ሕዝባዊ አብዮት ስናወሳ ስለቦልሼቪክና ስለሌኒን በአንድምታ
እንናገራለን ። ቦልሼቪክ ፣ ሌኒን ፣ የሩሲያ አብዮት ፣ ዲያሌክቲካዊ አን
ድነት ያላቸው ክስተት ናቸው ።

በዘመነ - ሶሻሊዝም በሌኒን የፓርቲ ሳይንስ የማይመራ ፓርቲ
ወይም አብዮተኛ ፤ የወዝአደሩ ሀቀኛ ፓርቲ ወይም ሀቀኛ አብዮተኛ
ከቶም ሊሆን አይችልም ።

የወዝአደር ፓርቲ በሙያ ዙሪያ ወይም በብሔረሰብ ጥያቄ ዙሪያ
ወዘተ ... የተሰባሰበ የሙያ ድርጅት ወይም ግንባር ፤ በአንድ ቃል የብዙ
ሀን ድርጅት አይደለም ። ርዕዮተ-ዓለማዊ አንድነት ሳይኖረው ለድርጅት
አንድነት ሲባል የተሰባሰበ የንዑስ-ከበርቴ ለዘብተኞች ድርጅትም ሊሆን
ከቶም አይችልም ። የወዝአደሩ ፓርቲ ፤ ማርክሲዝም-ሌኒኒዝምን ጠንቅ
ቀው ባወቁ ፣ በዚህም ሳይወሰኑ ርዕዮተ-ዓለሙን ከወዝአደሩ ትግል ጋር
በማዋሀድና ለማደራጀት ሁኔታው የሚጠይቃቸውን ማናቸውንም
ዓይነት መስዋዕትነት እስከመጨረሻዋ የደም ጠብታቸው ድረስ ለመከ
ፈል ራሳቸውን ባዘጋጁ ኮሚኒስት ምሁራንና ከወዝአደሩ መደብ ንቃተ-
ህሊናቸው በመጠቀ ወዝአደሮች ይመሰረታል ።

ሕይወታቸውን ከወዝአደሩ ትግል ጋር ያዋሀዱ ኑሮውን ኖረው ፤ ብሶ
ቱን ብሶቴ ብለው ፤ ከርሱ ተምረው ለትግሉ አስፈላጊ የሆኑትን መመሪያ
ዎች የሚሰጡ አብዮታዊ ምሁራን በትግሉ እሳት እየተፈተኑ ፤ ከብረት
ይልቅ እየጠነከሩ የሚወጡ የነጠሩ ኰሚኒስቶች ናቸው ። አብዮታዊት
ኢትዮጵያ እንደዚህ በትግል ተወልደው በትግል ያደጉ ለወዝአደሩ እው
ነተኛ አርነት በአብዮቱ የእሳት ወላፈን ነጥረው በወጡ ኰሚኒስቶች የሚ
መሰረተውን እውነተኛ ፓርቲ ትሻለች ። ለዚህም ነው « በኮሚኒስቶች
አንድነት የሠርቶ አደሩ ፓርቲ በትግላችን ይመሠረታል » የሚለውን
ወቅታዊና ታላቅ መፈክር ሌኒናዊ እውነት አለው የምንለው ።

በርግጥ ሕዝባዊ አብዮቶችን በመምራት ጥያቄ ላይ የተለያዩ ዝንባ
ሌዎች ይታዩ እንጂ ፤ ማርክሲስት ሌኒኒስት መሪዎች የግራና የቀኙን ማና
ቸውንም ዓይነት ዝንባሌዎች በመዋጋት ፤ ወቅቱ የጠየቀውን የትግል ዓይ
ነት የድርጅት መልክና ታክቲኮችን በመንደፍ አብዮት መርተው ድል
ተጐናጽፈዋል ፤ እየተጐናጸፉም ነው ።

በአንድ በተወሰነ የአብዮት ደረጃ ውስጥ ግለሰቦች ፣ ቡድኖች ፣ መደ
ቦችና የሕብረተሰብ ክፍሎች ፣ ድርጅቶች ፣ ግንባሮችና ፓርቲዎች በተ
ወሰነ ጊዜና ቦታ ውስጥ በማህበራዊ ኑሮ ፣ በኤኮኖሚና በፖለቲካው
ዙሪያ በሚይዙት አቋም መሠረት በአብዮትና በጸረ-አብዮት ቆዩ ። እን
ደሀገሪቱ ጊዜያዊ ሁኔታ በቅደም ተከተል የሚኖራቸውን የሀይል አሰላ
ለፍ ፣ በተወሰነ ሁኔታ ውስጥ በሚኖራቸው የርዕዮተ-ዓለም ፣ የድርጅትና
የወታደራዊ ጥንካሬአቸው መጠን የሚያነሱት የሀይል ሚዛን ማነስ ፣
መብለጥና መመጣጠን ፤ ብሎም የዓለም አቀፋዊውን የሀይል አሰላለፍና
ሚዛን ሌኒናዊ በሆነ መንገድ በመተንተንና ሀገር አቀፋዊውን ትግል ከዓ
ለም አቀፋዊው መልኩ ጋር በማገናዘብ ስትራቴጂዎችን ፣ ታክቲኮችን ፣
ፖሊሲዎችን ፤ አቋሞችን ወዘተ... ከዚህ ውስጥ ጨምቆ በማውጣትና



ከሰፊው ሕዝብ ትግል ጋር በማዋሀድ ፤ የወዝአደሩን ዘላቂ ግቦች በድል አድ
ራጊነት ለማረጋገጥ መታገልና ማታገል ፤ የአብዮታዊ መሪዎች ፖለቲካዊ
ችሎታ ብቻ ሳይሆን ጥበባዊ ችሎታቸውንም ጭምር የሚጠይቅ ይሆናል።
በሌኒን የተመራው የቦልሼቪክ ፓርቲ በዚህ የአመራር ሳይንስ የተራቀቀ
ነበር ።

የአንድን ነገር ወይም ሁኔታ ባሕርይ ስናጠና የተጸነሰበትን አካባቢ
የዕድገት ሁኔታ የሚያሳየውን ጠባይ ፤ ዓላማውን ለማሳካትና ሕልውና
ውን ለመጠበቅ የሚጠቀምበትን ዘዴና ስልቶች መረዳት ያስፈልጋል ።
ስለሆነም የሩሲያን አብዮት መርቶ ፤ በምድር ገጽ ላይ የወዝአደሩን አም
ባገነንነት መስርቶ ፤ ሶሻሊስት ሥርዓት ያነጸውን የቦልሼቪክ ፓርቲ ሙሉ
ባሕርይ ለማወቅ እንዲቻል መጽሐፉ የተጠቀሱትን ዓውደ-ሃሳቦች በመን
ተራስ ለማብራራት ይሞክራል ።

የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ በምን ሁኔታና በምን ዓይነት ትግል
ተቋቋመ ? በውስጥና በውጪ የተደረጉ ትግሎች ፣ ቦልሼቪክ ከዚህ ውስ
ጣዊና ውጪያዊ ትግል እንዴት ተፋልሞ እንደወጣና ሁለቱን የአብዮት
ደረጃዎች አልፎ የወዝአደሩን አምባገነንነት በመመስረት ለዓለም አቀፍ
ሶሻሊስት አብዮት ደጀን ሊሆን እንዴት እንደበቃ ይገልጻል ።

መጽሐፉ ለፍልስፍና ጥያቄ ፣ ለድርጅት ጥያቄ ፣ ለታክቲክና ለስት
ራተጂ ጥያቄ ፣ ለመንግሥት ጥያቄ ለትጥቃዊ አመጽ ጥያቄ ወዘተ...
የሚያመረቃ መልሶችን ይሰጣል ።

አብዮት እንደሚያስተምር ተደጋግሞ የተወሳ ሀቅ ነው ። የሚያስ
ተምረው ደግሞ መሪዎችን ብቻ ሳይሆን ሰፊውን ሕዝብ ጭምር ነውና
ሕብረተሰብ በመደብ ከተከፋፈለበት ጊዜ አንስቶ እስካሁን ድረስ የተ
ካሄዱትን የሕዝባዊ አብዮቶች ታሪክ ቢያንስ እንኳ ዋና ዋናዎቹን ማወቅ
እጅግ አስፈላጊ መሆኑን በመገንዘብ የሶቭየት ሕብረት ኮሚኒስት ፓርቲን
(የቦልሼቪክን) ታሪክ ስናቀርብላችሁ አያሌ ትምህርቶችን እንደምትቀ
ስሙ ተስፋ በማድረግ ፤ የሌላ አገር አብዮት ታሪክ ይዘንላችሁ እንደምን
ቀርብ ቃል እየገባን መጽሐፉን እንድታነቡ እንጋብዛችኋለን ።

# የሶሻል ዲሞክራቲክ የሰራተኞች ፓርቲን ለመ ፍጠር በሩሲያ ውስጥ የተደረገው ትግል

(1883—1901)

## 1. የገባርነት መወገድና የኢንዱስትሪያዊ ካፒታሊዝም በሩስያ ውስጥ ማደግ ፡ ዘመናዊ የኢንዱስትሪ ወዛደሮች መንሳሳት የሠራተኛ መደብ ንቅናቄ የመጀመሪያው እርምጃ ።

ዛሪስት ሩስያ በካፒታሊዝም የእድገት ጉዳና ውስጥ የገባችው ከሌሎች ሀገሮች ዘግየት ብላ ነው ። ከአለፈው ምእተ-አመት ስድሣዎቹ ቀደም ብሎ በሩስያ ጥቂት የእህል ወፍጮዎችና ፋብሪካዎች ነበሩ ። በገባርነት ላይ የተመሰረተው ሁዳዳዊ ባለቤትነት አስፈላጊውን የምጣኔ-ሀብት ቅርጾች ይቆጣጠር ነበር ። ገባርነት በሰፈነበት ሥርዓት እውነተኛ የኢንዱስትሪ እድገት ሊኖር አይችልም ። ገባሮች ከፍላጐት ውጭ በሆነ መንገድ በግብርና ላይ የሚያፈሱት ጉልበት ውጤቱ እጅግ ዝቅ ያለ ነበር ።የምጣኔ-ሀብታዊ እድገት መላ ሂደቶች የገባርነት አስፈላጊነት እንዲወገድ አደረጉ ። በ1861 ፣ ዛሪስት አገዛዝ ፤ በክሬሚያን ጦርነት በመሸነፉ ተዳከመ ። ገበሬዎችም በሚያካሂዱት ጸረ የመሬት ከበርቴ አመጻዎች ተብረከረኩ ። ይህም ለገባርነት መወገድ መልካም ግፊት ሆነ ።

ነገር ግን ገባርነት ከተወገደ በኋላ እንኳን የመሬት ከበርቴዎች ገበሬዎችን ከመጨቆን አልተቆጠቡም ። ለ «አርነት» በሚያደርጉት የትግል ሂደት ውስጥ ቀደም ብሎ ገበሬዎች ይጠቀሙበት የነበረውን አብዛኛውን የመሬት ክፍል በመከለል እና በማባረር ገበሬዎችን ዘረፏአቸው ።እነዚህ በመሬት ከበርቴዎች ተቆርጠው የወጡ የመሬት ክፍሎች ገበሬዎች ኦትሬዚክ (ጉማዶች) ብለው ይጠሩአቸው ነበር። ገበሬዎች በ2,000,000,000 የሚገመት ሩብል ለመሬት ከበርቴዎች «አርነት» ዋጋቸው በመቁጠር እንዲከፍሉ ተገደዱ ።

ገባርነት ከተወገደ በኋላ ገበሬዎች እጅግ አስቸጋሪ በሆነ ሁኔታ መሬትን ከመሬት ከበርቴዎች እንዲከራዩ ተገደው ነበር ። የኪራይ ገንዘብ ከመክፈላቸው ጋር ተዳምሮ ገበሬዎች የመሬት ከበርቴዎችን የተወሰነ መሬት በራሳቸው መሳሪያና ፈረሶች ያለአንዳች ክፍያ እንዲያለሙ ይደረጉ ነበር ። ይህ ድርጊት ኦትራቦትኪ ወይም ባርሽቺና (የማይከፈል የእለት ሥራ ፣ የጉልበት ኪራይ) በመባል ይጠራል ። በአብዛኛው ሁኔታ ገበሬዎች ለመሬት ከበርቴዎች የሚከፍሉት ኪራይ ከሚያገኙት ምርት ከፊሉን እንዲሆን ይገደዳሉ ። ይህ ሁኔታ ኢስፖሎ (ግማሽና የግማሽ ሥርዓት) በመባል ይታወቃል ።



ስለሆነም በገባርነት ሥር እንደነበረው ሁሉ ሁኔታው አልተለወጠም ለማለት ይቻላል ። ልዩነት አለው ቢባል ገበሬው አሁን በግሉ ነጻ መሆኑነው ። እንደ ተንቀሳቃሽ ንብረቶች የሚሸጥ ወይም የሚገዛ ሊሆን አይችልም ።

የመሬት ከበርቴዎች ኋላ ቀሩን ማሳዎች የተለያዩ ሀይላዊ ዘዴዎች (በኪራይ ፣ በገንዘብ መቅጣት) በመጠቀም አመሰቃቀሏቸው ። የመሬት ከበርቴዎች ጭቆና ስለሚሰማቸው በርካታ ገበሬዎች ማሳዎቻቸውን ለማሻሻል አልቻሉም ። ስለሆነም በቅድመ አብዮት ሩስያ የእርሻ ኋላቀርነት ከፍተኛ ደረጃ በመድረሱ ወደተለመደው የእህል እጥረትና ፡ ረሀብ አመራ።

የገባርነት ማንሰራራት ፣ ብዙውን ጊዜ ገበሬው ለቤቱ ከሚያውለው ገቢ የሚበልጠውን ለመሬት ከበርቴዎች የሚደረጉ በጣም የሚጉዱ የግብርና የመቀጫ ክፍያዎች ገበሬውን አዳከመው፣ ወደ ተመጽዋችነትም አወረዱት ፣ ሕይወቱንም ለማኖር መንደሩን ትቶ እንዲኰበልል አስገደዱት ። በመሆኑም በእህል ወፍጮዎችና በኢንዱስትሪዎች ውስጥ ለመስራት ተሰደደ ። ይህ ሁኔታ ደግሞ ለባለፋብሪካዎች ጥሩ የርካሽ ጉልበት ምንጭ ሆኖ ነበር ።

ከሠራተኞችና ከገበሬዎች በላይ ፣ የዛሩን ፣ የፋብሪካ ባለቤቶችንና የመሬት ከበርቴዎችን ከለፍቶ አደሩና ከጭቁኑ ሕዝብ የሚጠብቃቸው (የዘውዱ) ባለሚሎች ፣ ረዳት ባለስልጣኖች ፣ ገዳዮች ፣ ተራ የፖሊስ ወታደሮች ፣ የገጠር ፖሊሶች ባንድ ቃል የዘውዱ ታማኝ ሠራዊት ተቀምጠዋል ። እስከ1903 ድረስ የሰውነት ቅጣቶች ይካሄዱ ነበር ። ምንም እንኳ ገባርነት ቢደመሰስም ገበሬዎች ሕግ በመጣሳቸውና ግብር ባለመክፈላቸው ጀርባቸውን ይገረፉ ነበር ። በተለይም ባለፋብሪካዎች በሰራተኛው ኑሮ ላይ የሚያደርሱትን ሁኔታ መታገስ በማይችሉበት ጊዜ መሣሪያዎቻቸውን በማስቀመጥ ሠራተኞች የሥራ ማቆም አድማ በሚያደርጉበት ወቅት ፖሊሶችና ፣ የዛሩ ነጭ ለባሾች ሠራተኞቹን ያሰቃዩአቸዋል ። በዛሩ ዘውዳዊ አገዛዝ ሥር ምንም ዓይነት ሠራተኞችና ገበሬዎች ምንም ዓይነት የፖለቲካ መብቶች አልነበራቸውም ። የዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ የመጨረሻው የሕዝቡ ጠላት ነበር ።

ዛሪስት ሩስያ የብሔሮች ወህኒ ቤት ነበረች ። በርካታ የሩስያ ብሔረሰቦች መብት ስለአልነበራቸው ዘወትር ለማንኛውም ዓይነት ስድብና ውርደት ተጋልጠው ተሰጥተው ነበር ። የዛሩ መንግስት የሩስያ ሕዝብ የተለያዩ ብሔሮችን እንደ ዝቅተኛ ዘር እንዲቆጥሩዋቸው በማስተማር እንዲያውም በግልጽ እንደ ባእድ (ኢኖሮዲቲስ) በመቁጠር በነርሱ ላይ ጥላቻዎች እንዲዳብሩ አደረገ ። የዛሩ አገዛዝ ሆን ብሎ ብሔራዊ ብጥብጥ በመፍጠር አንድ ብሄር በሌላው ላይ እንዲነሳሳ ፣ የአይሁዳውያን የገዳይና የዘረፋ ቡድን እቅድ በመንደፍ ፣ እንዲሁም በትራንካውካሲያን ውስጥ ታታሮች ከአርሜኒያኖች ጋር እርስ በርሳቸው እንዲተላለቁ ይገፋፉ ነበር ።

ሁሉም ፣ ያም ማለት ባይቻል ፣ የብሔራዊ አካባቢዎች የአገዛዝ
ሥልጣኖች በሩስያውያን ባለሥልጣኖች በመያዝ ፤ መላው መንግስታዊ
የንግድ ተቋሞችና ፍርድ ቤቶች በሩስያ ቋንቋ ይመሩ ነበር ። የሩ
ስያዊ ብሔረሰብ ባልሆኑ ቋንቋዎች ጋዜጣዎችንና መጽሀፎችን ማተም ፣
ወይም በትምህርት ቤቶች ውስጥ በትውልድ ቋንቋዎች ማስተማር እን
ዲሁ የታገደ ነበር ። የዛሩ መንግስት እያንዳንዷን ብሔራዊ የባህል ፍን
ጣቂ እሳት ለማጥፋት በመሯሯጥ እንዲሁም በሀይል «የሩስያውያንን
ባህል መስፋፋት »መመሪያ በማራመድ፣ የሩስያ ዝርያ የሌላቸውን ሕዝ
ቦች የሚያሰቃይና የሚያስጨንቅ ነበር ።

ገባርነት ከተደመሰሰ በኋላ በሩስያ ውስጥ ኢንዱስትሪያዊ ካፒታሊ
ዝም ፣ ምንም እንኳ በገባርነት ማቆጥቆጥ ቢገደብም ፣ በጥሩ ፈጣን እርምጃ
ወደፊት ተጓዘ ። በ25ቱ ዓመታት ውስጥ ማለትም ከ1865—90 ዓ.ም.
በታላላቅ የእህል ወፍጮዎች ፣ በፋብሪካዎችና በባቡር መገናኛዎች ተቀ
ጥረው የሚሰሩ ሠራተኞች ቁጥር ከ1,706,000 ወደ 1,433,000 ወይም
ከእጥፍ በላይ ጨመረ ።

በሩስያ ውስጥ ታላላቅ የካፒታሊስት ኢንዱስትሪዎች በአሥራ ስምንት
ዘጠናዎቹ በበለጠ ፍጥነት ማደግ ጀመሩ ። በነዚያም ዓመታት መጨረሻ
ላይ በታላላቅ ፋብሪካዎች ወፍጮዎች ፣ በማእድን ፋብሪካዎችና በባቡር
መገናኛዎች ተቀጥረው ይሰሩ የነበሩ ሠራተኞች ቁጥር በሀምሳ የሩስያ
መስል የአውሮፓ ጠቅላይ ግዛቶች ብቻ ወደ2,207,000 ሲደርስ በመላው
የሩስያ ግዛቶች 2,792,000 ሰዎች ተጠጋ ።

ይህ ደግሞ በገባርነት ዘመን በፋብሪካዎች ውስጥ ተቀጥረው ይሰሩ
ከነበሩ ሠራተኞችና በትናንሽ የእደ ጥበባት እንዲሁም በተለያዩ የኢንዱ
ስትሪ ዓይነቶች ውስጥ ተቀጥረው ከሚሠሩ ሠራተኞች በዓይነት የተለየው
ዘመናዊው ወዝአደር ነበር ። በዚህም ሊለይ የቻለበት ምክንያት ወዝአደሩ
በነበረው የአንድነት የመንፈስ ጥራትና ቆራጥ አብዮታዊነት ነው ።

በአስራ ስምንት ዘጠናዎቹ የባቡር ሐዲድ መስመሮች ሕንጻ ተግባር
በሰፊው መከናወን የኢንዱስትሪውን እድገት አናረው ። በእነዚህ የአ
ሥር ዓመታት ሂደት ውስጥ (ከ1890—1900) ከ21,000 ቨርስቶች
(የሩስያ የርቀት መለኪያ ነው ፤ አንዱ ቨርስት 0.6629 ማይል ነው-ከተ
ርጓሚው) በላይ የሆኑ አዳዲስ የባቡር ሐዲዶች ተዘረጉ ። የነዚህ ሀዲዶች
መዘርጋት ደግሞ የብረትን ዋና አስፈላጊነት ለመኪናዎች ወዘተ . . . እን
ዲሁም የነዳጆችን መጠን መጨመር—የከሰልና የዘይትን—አስፈላጊነት
አስከተሉ ። ስለሆነም ይህ ሁኔታ ለብረትና ለዘይት ኢንዱስትሪዎች ማደግ
ምክንያት ሆነ ።



በቅድመ-አብዮት ሩስያ እንደካፒታሊስት አገሮች ሁሉ የኢንዱስት
ሪያዊ ፈጣን የእድገት ወቅቶች በተራቸው በኢንዱስትሪያዊ ፣ ቀውስና
እድገት የማያሳዩ ወቅቶች በመተካታቸው የሠራተኛውን መደብ በከፍ
ተኛ ሁኔታ ጐዱት ። በመቶ ሺህ የሚቆጠሩ ሠራተኞችን ያለ ሥራ እንዲ
ቀሩና ለድህነት እንዲጋለጡ አደረጋቸው ።

ይሁን እንጂ በሩስያ ውስጥ የካፒታሊዝም እድገት ገባርነት ከተደ
መሰሰ በኋላ በተፋጠነ ሁኔታ ቢራመድም በምጣኔ-ሀብታዊ እድገቷ ሩስያ
ከሌሎች የካፒታሊስት አገሮች ወደ ኋላ የቀረች ነበረች ። አብዛኛው የሀ
ገሪቱ ሕዝብ አሁንም በእርሻው የሚዳክር ነበር ። የካፒታሊዝም እድገት
በሩስያ በተሰኘው ክቡር ሥራው ሌኒን በአጠቃላዩ የ1897 ዓ.ም. የሕዝብ
ቆጠራ እንደተመለከተው ከጠቅላላው ሕዝብ አምስት ስድስተኛው በእርሻ
የሚኖርና አንድ ስድስተኛው ብቻ በታላላቅና ትናንሽ ኢንዱስትሪዎች ፣
ንግዶች ፣ በባቡርና በውሀ መገናኛዎች ፣ በሕንጻ ሥራዎችና በመሳሰሉት
እንደሚኖሩ አሳየ ።

ይህ የሚያሳየው ምንም እንኳ ካፒታሊዝም በሩስያ ቢያድግም አሁ
ንም ሩስያ ገና ከእርሻ ያልተላቀቀች ፣ በምጣኔ-ሀብቷ ወደ ኋላ የቀረች ፣
የንዑስ ከበርቴዎች አገር ናት ። በዝቅተኛ ባለቤትነት ላይ የተመሰረተው
የያንዳንዱ ገበሬ ዝቅተኛ የእርሻ ውጤት አሁንም የበላይነቱን እንደያዘ
ነው ።

ካፒታሊዝም በከተሞች ብቻ ሳይሆን በገጠሮችም ጭምር ተስፋፋ ።
በቅድመ-አብዮት ሩስያ በቁጥር በርካታ የነበረው የገበሬው መደብ እየተ
ከፋፈለ መጣ ። ከታታሪ ገባሩ መሐል የበላይነት ደረጃን የያዙ ሐብታም
ገበሬዎች ብቅ አሉ ። የገጠር ቡርዧዎችም ሲፈጠሩ በሌላው በኩል ደግሞ
በርካታ ገበሬዎች እየተዳከሙ ሄዱ ። በብዙ የሚቆጠሩ ደሀ ገበሬዎች ፣
የገጠር ወዛደሮችና ከፊል ወዛደሮች ቁጥራቸው እየጨመረ መጣ ። የመካ
ከለኛ ገበሬዎች የአመት ቁጥር እየቀነሰ ሄደ ።

በ1903 ዓ.ም. በሩስያ ውስጥ ወደ 10ሚሊዮን የሚጠጉ የገበሬ ቤተ
ሰቦች ነበሩ። ይድረስ ለገጠሬው ድሀ ፣ በተሰኘው በራሪ ወረቀቱ(Pamphlet)
ሌኒን እንዳሰበው ከዚህ ውስጥ ከሶስት ተኩል ሚሊዮን የሚያንሰው የገበሬ
ቤተሰብ ፈረሶች የሌሉት እንደሆነ ገምቷል ። እነዚህም አነስተኛውን
መሬት እያረሱ ሌላውን ለሐብታም ገበሬዎች የሚያከራዩና ለራሳቸውም
ሕይወት ሌላ የኑሮ ምንጭ የሚሹ የመጨረሻው ድሀ ገበሬዎች ነበሩ ።
የነዚህ ገበሬዎች ስፍራ ወዛደሩ ወዳለበት ሁኔታ እየተቃረበ መጣ ።
ስለዚህም ሌኒን የገጠር ወዛደሮች ብሎ ጠራቸው ።

በሌላ በኩል 1 አንድ ተኩል ሚሊዮን ሀብታም የሐብታም ገበሬ
ቤተሰቦች (ከጠቅላላው 10 ሚሊዮን የገበሬ ቤተሰብ ውስጥ) በገበሬዎች
እጅ ከነበረው አጠቃላይ ሥፍራ ከፊሉ (ግማሹ) በራሳቸው ይዞታ ሥር

ይገኝ ነበር ። እነዚህ የገጠር ቡርዧዎች ደሀውንና መሀከለኛውን ገበሬ
እያዳከሙ ፣ በእርሻዎች ላይ በሚፈሰው ጉልበት እያተረፉ ፣ ሀብታም
እየሆኑ ወደ ገጠር ካፒታሊስቶች አደጉ ።

የሩስያ ሰራተኞች በሰባዎቹ በተለይም ደግሞ በሰማኒያዎቹ መንቃት
በመጀመራቸው ጸረ-ካፒታሊስት የሆነ ትግል ማራመድ ጀመሩ ። ትልቁ
ጥንካሬ በርካታ ሰራተኞች በዛር ሩስያ ውስጥ በመኖራቸው ነበር ። በሰማ
ኒያዎቹ ዓመታት በወፍጮዎችና በፋብሪካዎች ውስጥ የእለት ሥራ ሰዓ
ቶች ከ$12\frac{1}{12}$ የሚያንሱ ፤ እንዲሁም በጨርቃጨርቅ ኢንዱስትሪ ከ14-15
ሰዓቶች የሚደርሱ ነበሩ ። የሴቶችና የሕጻናት ጉልበት መበዝበዝ ተስፋፋ ።
ህጻናት ከአዋቂዎች የስራ ሰዓት እኩል ይሰራሉ ፤ ነገር ግን እንደ ሴቶች
ሁሉ በጣም ዝቅ ያለ ክፍያ ይከፈላቸዋል ። ደሞዛቸው በማይመጣጠን
ሁኔታ ዝቅ ያለ ነበር ። አብዛኛው ሰራተኛ ሰባት ወይም ስምንት ሩብል
በየወሩ ይከፈለው ነበር ። እጅግ ከፍተኛ ክፍያ የሚደረግላቸው የብረት
ስራዎችና የብረት ማቅለጫ ሰራተኞች በወር ከ35 ሩብል በላይ አያገኙም ።
ለሰራተኞች እንክብካቤ የወጣ ሕግ ባለመኖሩ እጅግ ብዙዎቹ አካላቸው
ጉድሎና ሞተው ይገኙ ነበር ። ሰራተኞች ዋስትና አልነበራቸውም ፣
ለሁሉም የጤና አገልግሎቶች መክፈል ነበረባቸው ። የአኗኗር ሁኔታ
ቸው አስደንጋጭ ነበር ፣ በፋብሪካ ክልል ውስጥ ባሉ ቤቶች ሰራተኞች
በአንዲት ጠባብ «ክፍል» ከ10—12 በመሆን ተጨናንቀው ይኖሩ ነበር ።
ከዚህም በላይ ባለፋብሪካዎች በተዘጋጁት ሱቆቻቸው ውስጥ በከፍተኛ
ዋጋ እንዲገዙ በማስገደድና በገንዘብ በመቅጣት የሰራተኞችን ደሞዝ
ይቀናንሳሉ ።

ሰራተኞች ሊቋቋሙት የማይችሉትን ሁኔታ እንዲሻሻልላቸው አንድ
ዓይነት አቋም በመያዝና የጋራ ጥያቄዎችን ለፋብሪካ ባለቤቶች በማቅረብ
እንቅስቃሴዎችን ጀመሩ ። የፋብሪካ መሣሪያዎቻቸውንም እያስቀመጡ
የሥራ ማቆም አድማ መምታት ቀጠሉ ። በሰማኒያዎቹ ውስጥ የነበሩት
ቀደምት የስራ ማቆም አድማዎች ሊነሳሱ የቻሉት በመቀጮዎች መብዛት፤
ክፍያዎች በመቀነሳቸውና ከደሞዛቸው ላይ በመጭበርበራቸው ምክንያት
ነበር ።

ቀደም ባሉ ጊዜያት በተከናወኑት የስራ ማቆም አድማዎች ሰራ
ተኞች ወደ ተስፋ መቁረጡ በማምረታቸው አንዳንድ ጊዜ መኪናዎችን
በማበላሸት ፣ የፋብሪካ መስኮቶችን በመሰባበር ፣ እንዲሁም የፋብሪካው
ሱቆችንና ቢሮዎችን በማንኮታኮት ብሶታቸውን ይገልጹ ነበር ።

ከሠራተኞቹ የነቁት ክፍሎች ከካፒታሊስቶች ጋር በሚያደርጉት
ትግል አሸናፊ ለመሆን ድርጅት እንደሚያስፈልጋቸው ተገነዘቡ ። የሰ
ራተኞች ድርጅቶች ማበብ ጀመሩ ።



በ1875 ዓ.ም. የደቡብ ሩስያ የሰራተኞች ማህበር በኦዴሳ ውስጥ
ተመሠረተ ። ይህም የመጀመሪያው የሰራተኞች ድርጅት ለስምንት ወይም
ለዘጠኝ ወራት ከቆየ በኋላም በዛሩ አገዛዝ ተደመሰሰ ።

በ1878 ዓ.ም. በአናጢው ካህልቱሪን እና በእቃ ገጣጣሚው ኦብኖረስ
ኪይ የሚመራ የሰሜን ሩስያ የሰራተኞች ማኅበር በሴይንት ፒተርስበ
ርግ ተመሠረተ ። የማኅበሩም ፕሮግራም እንደሚገልጸው አላማዎቹና
ግቦቹ ከምእራቡ ሶሻል ዲሞክራቲክ የሰራተኞች ፓርቲ ጋር የሚመሳሰል
ነበር ። የማኅበሩ ዘላቂ ግብ የሶሻሊስት አብዮትን ማምጣት—«አሁን የሚ
ገኘውን አድሀሪ ፖለቲካዊና ምጣኔ-ሀብታዊ ሥርዓት ገርስሶ መጣል»
ነበር ። የማኅበሩ መሥራች አንዱ የሆነው ኦብኖርስኪ ከሀገር ውጪ ከማ
ርክሲስት የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲዎች ጋር ለጥቂት ጊዜ በመኖር ከፓ
ርቲዎቹ እንቅስቃሴዎች እራሱን በማዋሀድ በማርክስ ከተመራው የመ
ጀመሪያው ዓለም አቀፍ ብዙ ነገሮችን ገብይቷል ። ይህ ሁኔታ የሰሜን
ሩስያ የሰራተኞች ማኅበር አንድነት ፕሮግራም ተደናቂ እንዲሆን አድር
ጉታል ። የማኅበሩ የአጭር ጊዜ አላማ ለሕዝቡ ፖለቲካዊ እርነት ማቀዳ
ጀትና የፖለቲካ መብቶችን ማስጨበጥ (የንግግር ፣ የህትመት ፣ የስብሰባ
ነጻነት) እንዲሁም የሰራተኞችን የቀን የስራ ሰዓት ማስቀነስ ነበር ።

የማኅበሩ አባላት ቁጥር ወደሁለት መቶ በመድረስ ብዙ ደጋፊዎችን
አፈራ ። በሠራተኞች የስራ ማቆም አድማ ውስጥ በመሳተፍ መምራት
ጀመረ ። ይህንንም የሰራተኞች ማኅበር የዛሩ አገዛዝ አፈረሰው ።

ይሁን እንጂ የሰራተኛው መደብ ንቅናቄ አልተገታም ። ይልቁንም
ማደግ ጀምሮ ከአውራጃ ወደ አውራጃዎች ተስፋፋ ። በሰማንያዎቹ አመ
ታት ውስጥ ከፍተኛ የስራ ማቆም አድማዎች ቁጥር ተመዘገበ ። በአ
ምስት ዓመት ልዩነት (1881—86) 80,000 ሰራተኞች የተሳተፉባቸው
ወደ 48 የሚጠጉ የስራ ማቆም አድማዎች ተደረጉ ።

በአብዮታዊ እንቅስቃሴ ታሪክ ውስጥ የተለየ ክፍል የተጫወተው
በ1885 ዓ.ም. ኦሬኮሆቮ-ዙዬቮ (Orekhovo-Zuyevo) ውስጥ በሞሮዞቭ
ወፍጮ የፈነዳው ታላቅ የስራ ማቆም አድማ ነበር ።

በዚህ ወፍጮ ውስጥ 8,000 ሰራተኞች ተቀጥረው ይሰሩ ነበር ።
የመስራት ሁኔታው ከእለት ወደ እለት እየተበላሸ በመሄዱ በ1884 ዓ.ም.
አምስት ጊዜ የደሞዝ መቁረጥ ቅደረገ ። በኋለኛው ዓመትም ክፍያዎች
በአንድ ጊዜ25 በመቶ ቀነሱ ። በተጨማሪም የወፍጮው ባለቤት ሞሮዞቭ
በመቀጫዎች ሰራተኞችን አስጨነቃቸው ። ለሰራተኞች ከሚከፈለው
እያንዳንዱ ሩብል ከ30 እስከ 50 ኮፒክስ ሰራተኛ (የሩብል አንድ መቶኛ
መሆኑ ነው) ወደ ባለ ፋብሪካዎች ኪስ ውስጥ በመቀጫ ስም መግባቱ በመ
ጋለጡ የስራ ማቆም አድማን አስከተለ ። ሰራተኞች ይህንን ቅሚያ ለረ

ጅም ጊዜ ሊቋቋሙት አልቻሉምና በጥር 1885 የስራ ማቆም አድማ አደረጉ ። ይህ ቀደም ብሎ የተቀናበረው የስራ ማቆም አድማ በፖለቲካ ንቃተ-ህሊናው በተራመደውና የስሜን ሩስያ የሰራተኞች ማኅበር አባል በነበረው በፓዮተር-ሞኢሲዬንኮ የተመራ ነበር ። ይህ ግለሰብ ጥቂት አብዮታዊ ልምድ የነበረው በመሆኑ በስራ ማቆም አድማ ዋዜማ እሱና መሰል መደባዊ ንቃተ-ህሊና የነበራቸው ሰራተኞች በሚስጥር ስብሰባ ውስጥ ሰራተኞች ተስማምተውበት የተፈራረሙበትን ጥያቄ እንዲሟላላቸው ለወፍጮው ባለቤት አቀረቡ ። ከነዚህ ጥያቄዎች ውስጥ ሰራተኞችን ያዳቀቁ መቀጫዎች እንዲወገዱ የሚጠይቀው ዋነኛው ነበር ።

ይህ የስራ ማቆም አድማ በጦር ሀይሉ ተበተነ ። ከ600 የሚበልጡ ሰራተኞችም በእስር ቤት ታጉሩ ። ሌሎቹም ለፍርድ ቀረቡ ።

ይህንኑ ዓይነት የስራ ማቆም አድማ በኢቫኖቭ-ቮዝሚሲንስክ ወፍጮዎች በ1885 ዓ.ም. ፈነዳ ።

በሚቀጥሉት አመታት የዛሩ መንግስት የሰራተኛው መደብ የሚያካሂዳቸው ንቅናቄዎች ከእለት ወደ እለት በማደጋቸው ተደናግጦ የገንዘብ መቀጫዎችን ሕግ በአደባባይ አወጀ ። ይህም አዋጅ የመቀጮ ገንዘቦች በፋብሪካ ባለቤቶች ኪስ መግባት እንደሌለበትና ሰራተኞች ለራሳቸው ጥቅም እንዲያውሉት የሚያደርግ ነበር ።

የሞሮዞቭና ሌሎችም የስራ ማቆም አድማዎች ከዚህ የበለጡ ታላላቅ ድሎችን በተደራጀ ትግል ማግኘት እንደሚቻል አስተማሩ ። የሰራተኛው መደብ ትግል ብቁ መሪዎችን ፣ አደራጆችን የሰራተኛውን መደብ ፍላጐት ለድል የሚያበቁ ቆራጦችን ማፍራት ጀመረ ።

ከዚሁ ጋር የሰራተኛው መደብ ንቅናቄ እያደገ በመሄዱ ምክንያትና የምእራብ አውሮፓ የሰራተኛ መደብ ንቅናቄዎች በሚያደርጉት ግፊት የተነሳ የመጀመሪያው ማርክሲስት ድርጅት በሩስያ መቋቋም ጀመረ ።

## 2. ናሮዲዝም (ሕዝባዊነት) እና ማርክሲዝም በሩስያ ፣ ፕሌካሃኖቭና «የሰራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን ፤ የፕሌክሀኖቭ ጸረ-ናሮዲዝም ትግል ።

በሩስያ ውስጥ የማርክሲዝም መስፋፋት ቀደም ብለው ገና ማርክሳዊ ቡድኖች በሩስያ ውስጥ ሳይታዩ ፣ አብዮታዊ ስራዎች ይካሄዱ የነበሩት ጸረ-ማርክሲስት በሆኑት በናሮዳውያን ነበር ።

ፕሌክሃኖቭ በሚያካሂደው አብዮታዊ ተግባሩ የተነሳ የዛሩ አገዛዝ ይዞ ሊያሰቃየው በሚያሳድደው ወቅት ከሩስያ ውጭ ወደ ጄኔቭ በስደት ሄዶ የመጀመሪያውን ማርክሲስት ቡድን በ1883 ዓ.ም. «የሰራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን በሚል መጠሪያ መሠረተ ።



ቀደም ሲል የናሮዳውያን አባል የነበረው ፕሌክሀኖቭ ከሩስያ ውጪ ሆኖ ማርክሲዝምን በማጥናት እውቅ የማርክሲዝም ቀስቃሽ ሊሆን በቃ ።

የ «ሰራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን ማርክሲዝም በሩስያ ውስጥ እንዲስፋፋ ብዙ የጣረ ድርጅት ነበር ። የማርክስና የኤንግልስን ሥራዎች ወደ ሩስያኛ ቋንቋ በመተርጉም — የኮሚኒስት ማኒፌስቶ (መግለጫ) ፣ ደሞዝ — ስራና ወረት ፣ ተምኔታዊና ሳይንሳዊ ሶሻሊዝም ወዘተ . . . እያሳተሙ ከውጪ በምስጢር ወደ ሩስያ በመላክ እንዲሰራጩ ያደርጉ ነበር ። ፕሌክሀኖቭ ፣ ዛሱሌቹ ፣ አክዘሊሮድና ሌሎችም የዚህ ድርጅት አባሎች በርካታ የማርክስንና የኤንግልስን ስራዎች ፣ የሳይንሳዊ ሶሻሊዝም ሀሳቦችን በመጻፍ አስተምረዋል ።

የመጀመሪያዎቹ የወዛደሩ መምህሮች ማርክስና ኤንግልስ እንደገለጹት ፣ ሶሻሊዝም ተምኔታዊ ሶሻሊስቶች እንደሚያምኑት በሕልም ፣ በምኞት ሳይሆን በማይቀረው በዘመናዊ ካፒታሊዝም የሕብረተሰብ የእድገት ውጤት ነው ። ልክ የገባሩ ሥርዓት እንደወደቀ ሁሉ የካፒታሊስት ሥርዓትም በወዛደሩ መቃብሩ ተቆፍሮለት እንደሚንኰታኰት አሳይተዋል ። እንዲሁም በወዛደሩ የመደብ ትግልና ወዛደሩ በቡርዧው ላይ ድልን በመቀዳጀቱ ብቻ ሰዎች ከካፒታሊዝምና ከብዝበዛ ይላቀቃሉ በማለት አስረድተዋል ።

ማርክስና ኤንግልስ ወዛደሩ የራሱን ጥንካሬ እንዲያውቅ መደባዊ ጥቅሙን እንዲገነዘብና ከቡርዧው ጋር ለሚደረገው ወሳኝ ትግል እንዲተባበር አስተምረውታል ። የካፒታሊስት ሕብረተሰብን የእድገት ሕግጋት ያገኙና የካፒታሊስት ሕብረተሰብን እድገት ፣ በውስጡ ስለሚካሄደው የመደብ ትግል ፣ በማይቀር ሁኔታ ወደ ካፒታሊዝም ውድቀት ፣ ወደ ወዛደሩ ድል አድራጊነት ፣ ወደ ወዛደራዊ አምባገነንነት እንደሚያመራ ሳይንሳዊ በሆነ መንገድ ካርል ማርክስና ፍሬደሪክ ኤንግልስ አረጋግጠዋል ።

ማርክስና ኤንግልስ ሲያስተምሩ በሰላማዊ መንገድ የወረትን ስልጣን ለማስወገድና የባለወረቶችን ንብረት ወደ ሕዝባዊ ንብረት ለመለወጥ አይቻልም ። ይህንን ድል ወዛደሩ ሊጐናጸፍ የሚችለው በቡርዧው ላይ በሚያደርገው አብዮታዊ አመጽ ፣ በወዛደራዊ አብዮት ፣ የራሱን ፖለቲካዊ አገዛዝ ሲመሰርትና ፡ የወዛደሩ አምባገነናዊ መንግስት ፡ — የበዝባዦችን ቅስም ሲሰብር ነው አዲስ መደብ አልባ ኮሚኒስት ሕብረተሰብ መመስረት የሚችለው ።

ማርክስና ኤንግልስ እንዳስተማሩት የኢንዱስትሪ ወዛደር እጅግ አብዮታዊ ነውና በካፒታሊስት ሕብረተሰብ ውስጥ እጅግ ተራማጅ መደብ ነው ። እንደዚህ ያለው መደብ ብቻ ነው ከካፒታሊዝም ጋር ግንኙነት የሌላቸውን ሀይላት በዙሪያው በማሰባሰብ ካፒታሊዝምን ለመ

ደምሰስ የሚደረገውን ጉዞ ሊመራ የሚችለው ። ይሁን እንጂ አሮጌውን ዓለም አስወግዶ አዲስ መደብ አልባ ሕብረተሰብ ለመፍጠር ፥ ወዛደሩ የራሱ የሆነ የሰራተኞች መደብ ፓርቲ ፥ ማለትም ማርክስና ኤንግ.\ስ የኮሚኒስት ፓርቲ ብለው የጠሩት እንዲኖረው ያስፈልጋል ።

የፕሌክሀኖቭ «የሰራተኞች ነጻ እውጪ» ቡድን የሆነው የመጀመሪያው የሩስያ ማርክሲስት ቡድን የማርክስና የኤንግልስም አመለካከቶች እንዲስፋፉ በማለት ራሱን መስዋዕት አድርጓል ።

በሩስያ ገና አንድም የሶሻል ዲሞክራቲክ እንቅስቃሴ ባልነበረበት ወቅት «የሠራተኞች ነጻ እውጪ» ቡድን ከውጪ በሩስያኛ እትመቱ የማርክሲዝምን ሰንደቅ አነገበ ። እንደዚህ ላለ ተግባር ከሁሉም በፊት ንድፈ-ሀሳባዊ ፥ ርእዮተ-ዓለማዊ ቡድኖችን ማዘጋጀት የግድ አስፈላጊ ነበር ። ለማርክሲዝም መስፋፋት ትልቁ እንቅፋት የሆነውና ለሶሻል ዲሞክራቲክ ንቅናቄ መሰናክል የነበረው በዚያን ወቅት በሰራተኛው የነቁ ክፍሎችና አብዮታዊ አመለካከት ባላቸው ምሁራን መሀከል ተሰራጭቶ የነበረው የናሮዳውያን አስተሳሰብ ነበር ።

ካፒታሊዝም በሩስያ ውስጥ እየዳበረ ሲመጣ ሰራተኛው መደብ ጠንካራና የተደራጀ አብዮታዊ ትግሉን የሚያንቀለቅል ፥ የማይበገር ሀይል እየሆነ መጣ ። ይሁን እንጂ ናሮዳውያን የሰራተኛውን መደብ የመሪነት ሚና አልተገነዘቡምና ዋንኛው አብዮታዊ ሀይል የሰራተኛው መደብ አይደለም ፤ ትልቁና ዋናው ሀይል ገበሬው ነው ፤ በመሆኑም የዛሩ አገዛዝና የመሬት ከበርቴዎች በገበሬው አመጻዎች ብቻ መገርሰስ አለባቸው በሚል የተሳሳተ መመሪያ ውስጥ ሰጠሙ ። ናሮዳውያን የሰራተኛውን መደብ አላወቁትምና ገበሬዎች ብቻቸውን የዛሩን አገዛዝና የመሬት ከበርቴዎችን ከወዛደሩ ጋር ሳያብሩና በወዛደሩ ሳይመሩ ገርስሰው ለመጣል እንደማይችሉ አልተገነዘቡም ። በተጨማሪም የሰራተኛው መደብ እጅግ አብዮታዊና የሕብረተሰቡ የመጠቀው መደብ መሆኑን አልተረዱም ነበር ።

በመጀመሪያ ናሮዳውያን ገበሬዎችን በዛሩ አገዛዝ ላይ ለማስነሳት እጅግ ሞክረው ነበር ። ይህን ዓላማም ከግቡ ለማድረስ ወጣት አብዮታዊ ምሁራን የገበሬዎችን ልብስ እየለበሱ ገጠር ዘመቱ ፤ —ይህንንም «ወደ ሕዝቡ» ብለው ይጠሩታል ፤— ስለሆነም «ናሮዲክ» የሚለው ቃል ናሮድ ፥ ሕዝብ ከሚለው የመጣ ነው ። ነገር ግን የገበሬዎችን ሁኔታ ባለመገንዘባቸው የተነሳ ምንም ድጋፍ አላተረፉም ። አብዛኛዎቹ በፖሊሶች ተይዘው ታሰሩ ። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ በዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ላይ ብቻቸውን ፥ ካለ ሕዝቡ ተሳትፎ ፥ ትግል ለማካሄድ ወስነው ተነሱ ፥ ይህ ደግሞ ይበልጥ ከድባ ስህተት ውስጥ ጣላቸው ።



«ናሮድንያቮሊያ» («የሕዝቡ ፍላጐት») በሚል የሚታወቀው የናሮዳውያን የሚስጥር ማኅበር ዛሩን ለመግደል አቅዶ ተነሳ ። ታህሣሥ 1/1881 የዚሁ «የናሮድንያቮሊያ» አባሎች ዛር አሌክሳንደር ዳግማዊን ቦምብ ወርውረው ለመግደል በቁ ። ይሁን እንጂ ከዚህ ድርጊታቸው ሕዝቡ አንዳችም አልተጠቀመም ። ግለሰቦችን መግደል የዛሩን ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ወይንም የመሬት ከበርቴዎችን መደብ መደምሰስ አልቻለም ነበር ። የተገደለው ዛር በአሌክሳንደር ሳልሳዊ ተተካ ፤ ለወዛደሩና ለገበሬው ያለው ሁኔታ አሁንም የከፋ ነበር ።

የዛርን አገዛዝ ለመቃወም በናሮዳውያን የተመረጠው ፥ በግለሰብ አሸባሪነት ፥ ግለሰቦችን የመግደል ዘዴ ስህተት ከመሆኑም በላይ አብዮቱን የሚጐዳ ነበር ። የግለሰብ አሸባሪነት መርህ ንቁ «ጀግኖች» እና «ጀግኖች» የ ሚጠበቀው ተከታይ «ጀሌ» ከሚለው የተሳሳተ ንድፈ-ሀሳብ ላይ የተመሰረተ ነበር ። ይህ የተሳሳተ ንድፈ-ሀሳብ የታወቁ ግለሰቦች ብቻ ታሪክን የሚሰሩ እንጂ ሰፊው ሕዝብ ፥ ሕዝቡ ፥ መደቦች ፥ «ጀሌዎች» ናሮዳውያን በጽሁፎቻቸው እንደሚጠሯቸው ለመንቃት ለድርጅታዊ እንቅስቃሴ የማይችሉና እንዲሁ በጭፍን «ጀግኖችን » የሚከተሉ ታሪክን ሊፈጥሩ አይችሉም የሚል ነበር ። በዚህም ምክንያት የተነሳ ናሮዳውያን በገበሬዎች ፥ በሠራተኛ መደብ መሀከል የሚሠሩትን የሰራተኛውን ሕዝብ አብዮታዊ ሥራ ወደ ግለሰብ አሸባሪነት በመለወጥ ለመጥፎ ሁኔታ አሳልፈው ሰጡት ። በወቅቱ ከነበሩት ታላላቅ አብዮታውያን አንዱ ስቴፓም ካሃልፋሪን (stepam-khalfarin) የተደራጀውን የሰራተኞች አብዮታዊ ማኅበር እንዲተውና ራሱን ለአሸባሪነት አሳልፎ እንዲሰጥ አደረጉ ።

የበዝባዥ መደብ ተወካይ ግለሰቦችን በመግደል ፥ ለአብዮቱ አንዳችም የማይፈይደውን ግድያ በማካሄድ ፥ ናሮዳውያን የሰራተኛውን ሕዝብ ከዚህ መደብ ጋር ከሚያደርገው መራራ ትግል አቅጣጫውን አስለወጡት ። የአብዮታዊ መነሳሳትንና የሰራተኛውን መደብ እንዲሁም የገበሬውን የእንቅስቃሴ እድገት አደናቀፉት ።

የሰራተኛው መደብ በአብዮቱ ውስጥ የራሱን የመሪነት ሚና እንዳያውቅና ነጻ የሆነ የሰራተኛው መደብ ፓርቲ እንዳይፈጠር አዘገዩት ።

ምንም እንኳ የናሮዳውያን የሚሥጥር ድርጅት በዛሩ አገዛዝ ቢደመሰስም ፥ ናሮዳዊ አስተሳሰቦች አብዮታዊ አመለካከት ባላቸው ምሁራን መሀከል ለረጅም ጊዜ ቆይቷል ። የተረፉት ናሮዳውያን የማርክሲዝምን በሩስያ መስፋፋት በጽኑ ተከላከሉ ። እንዲሁም የሰራተኛውን መደብ ድርጅት አደናቀፉ ።

ስለሆነም በሩስያ ውስጥ ማርክሲዝም ያደገውና ጥንካሬ ሊያገኝ የቻለው ከናሮዳዊነት ጋር ባደረገው ተጋድሎ ነበር ።

«የሰራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን በናሮዳውያን የተሳሳተ አመለካከት ላይ ትግሉን ያቀጣጠለና የነርሱ አመለካከትና የትግል ስልቶች የሰራተኛውን መደብ ንቅናቄ ጭፍን ያደረጉ መሆናቸውን አሳይቷል ።

ፕሌክሀኖቭ ናሮዳውያንን በመቃወም በጻፈው ጽሁፍ ምንም እንኳ ሶሻሊ.ስት ብለው ራሳቸውን ቢጠሩም ቅሉ አስተሳሰባቸውን ከሳይንሳዊ ሶሻሊዝም ጋር አንድ የሚያደርገው ምንም ነገር እንደሌለ አመልክቷል ።

ለናሮዳውያን የተሳሳተ አስተሳሰብ የመጀመሪያውን ማርክሳዊ ሂስ ያቀረበው ፕሌክሀኖቭ ነበር ። በእነርሱ ላይ ባለመው መልካም ምቱ የማርክሲዝምን አስተሳሰብ በሚገባ የመከላከል እድገት አሳየ ።

ፕሌክሀኖቭ የተዋጋቸው የናሮዳውያን አይነተኛ ስህተቶች ምን ነበሩ?

መጀመሪያ ፣ ናሮዳውያን «ካፒታሊዝም» በሩስያ ውስጥ በአጋጣሚ የመጣ እንጂ ፣ የሚያድግ አይደለም ፣ በመሆኑም ወዛደሩ ሊያድግም ፣ ሊሰፋም አይችልም በማለት ይናገራሉ ።

ሁለተኛ ፣ የሰራተኛውን መደብ በአብዮቱ ውስጥ እንደዋነኛው መደብ አድርገው አይመለከቱም ። ሶሻሊዝም ያለወዛደሩ ተሳቅፎ ግቡን ይመታል ብለው ያልማሉ ። በመሆኑም ዋነኛው የአብዮቱ ሀይል አርሶ አደሩ — በምሁራን የሚመራና የገበሬዎችን ኮሚዮኖችም (commune) የሶሻሊዝም ጽንስና መሰረት አድርገው ይመለከቱ ነበር ።

ሶስተኛ ፣ የሰዎችን ታሪካዊ ጉዞ ሁሉ ናሮዳውያን የሚመለከቱት በተሳሳተና ጉጂ በሆነ ሁኔታ ነበር ። የአንድን ሕብረተሰብ ምጣኔ-ሀብታዊና ፖለቲካዊ የእድገት ሕግጋት አያውቁትምና በዚሁ ሁኔታ እጅግ ኋላ የቀሩ ነበሩ ። እንደነሱ አባባል ታሪክ የሚሰራው በመደብ ወይም በመደብ ትግል ሳይሆን «በጀሌዎች» ፣ ሕዝቡ ፣ መደቦች በጭፍን በሚከተላቸው በታወቁ ግለሰቦች «በጀግኖች» ነው ።

ፕሌክሀኖቭ ናሮዳውያንን ሲወጋና ሲያጋልጥ ብዙ ማርክሳዊ ስራዎችን በመጻፉ በሩስያ ውስጥ ማርክሲዝምን አስተምሯል ፣ አስፋፍቷል ። ሶሻሊዝምና ፖለቲካዊ ትግል ፣ የእኛ ልዩነቶች ፣ አንድ ጉነኛ የታሪክ አመለካከት እድገት በተሰኙ ጽሁፎች ፤ ፕሌክሀኖቭ በሩስያ ውስጥ ለማርክሲዝም ድል አድራጊነት ጥርጊያ መንገድ ከፈተ ።

በጽሁፉ ፕሌክሀኖቭ መሰረታዊ የማርክሲዝምን መመሪያ ግልጽ አድርጎታል ። በተለይም የተለየ ጠቀሜታ የነበረው አንድ ጉነኛ የታሪክ አመለካከት እድገት የተሰኘው በ1895 ዓ.ም. የታተመው ጽሁፉ ሲሆን ፤ ሌኒን ይህ መጽሐፍ «መላውን የሩስያ ትውልድ ማርክሲስቶች ያጉለም ሳል» ብሏል ።



በናሮዳውያን ላይ በቷለመው ጽሁፉ ናሮዳውያን እንዳደረጉት ሁሉ ፣ ካፒታሊዝም በሩስያ ያድጋል ወይስ አያድግም ? የሚል ጥያቄ ማንሳት ምኝነት ነው በማለት ፕሌክሀኖቭ አሳይቷል ። እንደ እውነቱ ከሆነ ሩስያ በካፒታሊዝም የእድገት ጉዳና ውስጥ ገብታለች ። ይህንንም ጉዳና ሊያስቀይራት የሚችል ምንም ኃይል እንደሌለ ፕሌክሀኖቭ ተናግሯል ።

የአብዮታውያን ተግባር ካፒታሊዝም በሩስያ እንዳያድግ መግታት አልነበረም — ያም ቢሆን ሊያደርገቅ አይችሉም ። ትልቁ ተግባራቸው በካፒታሊዝም እድገት የተፈጠረውን አብዮታዊ ሀይል ማዳበርና መንከባከብ ፤ በሌላ አባባልም የሰራተኛውን መደብ ፣ የመደብ ንቃተ-ህሊናውን ማሳደግ ፣ ማደራጀትና የራሱን የሰራተኛ መደብ ፓርቲ እንዲመሰርት መርዳት ነበር ።

ፕሌክሀኖቭ ሁለተኛውን የናሮዳውያን ዓይነተኛ ስህተት ማለትም የወዛደሩን በአብዮታዊ ትግል ውስጥ ግንባር ቀደም ሚና መካድ አጋልጧል ። ናሮዳውያን የወዛደሩን በሩስያ መፈጠር እንደ አንድ «ታሪካዊ መጥፎ እድል» አድርገው በመመልከታቸው ስለ «የወዛደራዊነት መመርቀዝ» ያወሩ ነበር ። የማርክሲዝም ቀደምት አስተማሪ ፕሌክሀኖቭ ፣ ምንም እንኳ ገበሬው በቁጥር ቢበልጥና ወዛደሩ በአንጻሩ ሲታይ በቁጥር ቢያንስ ፣ አብዮታውያን ትልቁ ተስፋቸው መመስረት ያለበት በወዛደሩ ታዳጊነት ላይ እንደሆነ አሳይቷል ።

ለምን ተስፋቸው በወዛደሮች ላይ ይሆናል ?

ምክንያቱም ምንም እንኳን ወዛደሩ በቁጥሩ ሲታይ አነስተኛ ቢሆንም እጅግ ዘመናዊ ከሆነው የምጣኔ-ሀብት ፣ ከከፍተኛ የምርት ይዞታዎች የተያያዘ በመሆኑ የተነሳ ብሩህ ተስፋ ይጣልበታል ።

ምክንያቱም ወዛደሩ ፣ እንደ አንድ መደብ ፡ ከአመት ወደ አመት እያደገ የሚሄድ ፣ በፖለቲካም የሚዳብር ፣ በከፍተኛ ደረጃ ምርት ውስጥም የሚሳተፍ በመሆኑ በቀላሉ ሊደራጅ ይችላል ። እንዲሁም በአብዮቱ ውስጥ ከባርነት ሰንሰለት በቀር ምንም የሚያጣው ነገር ባለመኖሩ እጅግ አብዮታዊ መደብ ነው ።

ለገበሬው ግን ሁኔታው የተለየ ነበር ።

ገበሬው ማለትም በግል የሚያርሱትን ግለሰቦች ከቁጥር መብዛት የተነሳ ከሚኖረው ጥንካሬ ሌላ እጅግ ወደ ኋላ ከቀረው የምጣኔ-ሐብት ይዞታ ፣ ከቅናንሽ ደረጃ ምርቶች ጋር የተያያዘ በመሆኑ ምንም መልካም ተስፋ ከፊቱ አይኖርም ።

እንደ መደብ ሆኖ ካለማደጉም በላይ ገበሬው ወደ ቡርዧነትና (ኩላኮች) ወደ ደሀ ገበሬዎች መደብ ወዛደርና ከፊል ወዛደር እጅግ እየተከፋፈለ የሚመጣ ነበር ። ከዚህም በላይ ከወዛደሩ አንጻር ሲታይ ለመደራጀት የሚያስቸግር በመሆኑና የግል ሀብት ስላለውም አብዮታዊውን ንቅናቄ ከወዛደሩ ባነሰ ሁኔታ ይቀላቀላል ።

ናሮዳውያን ሶሻሊዝም በሩሲያ ውስጥ የሚመሰረተው በወዛደሩ አምባገነንነት ሳይሆን በገበሬዎች ኩሚዩን ፡— ማለትም ለሶሻሊዝም ጽንስ ወይም መሰረት ሊሆን ይችላል ብለው በሚያምኑት መንገድ ነበር ። ይሁን እንጂ ይህ የሚሉት ኮሚዩን ለሶሻሊዝም ጽንስ ወይንም መሰረት ከቶ ሊሆን አይችልም ። ምክንያቱም ኮሚዩኑ የድሀውን ገበሬ ደም በሚመጡ ኩላኮች ቁጥጥር ሥር ያለ በመሆኑ ነበር ። ዓይነተኛው የጋራ የመሬት ባለቤትነትና እንደ እያንዳንዱ የገበሬ ቤተሰብ ቁጥር የተደረገው የመሬት ወቅታዊ ክፍፍል በምንም ዓይነት ሁኔታውን አለወጠውም ። መሬቱንም የሚጠቀሙበት የኩሚዩኑ አባላት ከብት ማሰሪያና ዛፍም የሚያቀርቡ ሲሆኑ ፤ ይህንን ማድረግ የሚችሉት ደግሞ መሀከለኛ ገበሬዎችና ሐብታም ገበሬዎች ነበሩ ። ምንም ፈረስ የሌላቸው ድሀ ገበሬዎች ፣ በአጠቃላይ አነስተኛ ገበሬዎች በሙሉ መሬታቸውን ለሐብታም ገበሬ በመልቀቅ የእርሻ ተቀጣሪዎች መሆን ነበረባቸው ። እንደ እውነቱ፡ ከሆነ የገበሬ ኮሚዩን የሐብታም ገበሬዎችን የበላይነት ለመሸፈን የሚጠቀምበት አመቺ ዘዴ ከመሆኑም በላይ በጋራ ሀላፊነት ላይ በተመሠረተው መንገድ ከገበሬው ግብር ለመሰብሰብ የዛሩ አገዛዝ የሚጠቀምበት በእጁ ያለ መሳሪያ ነበር ። ለዚህ ነው የዛሩ ዘውዳዊ አገዛዝ የገበሬውን ኮሚዩን አንዳችም ጥቃት ሳያደርስበት እንዳለ የተወው ። እንደዚህ ዓይነቱን ኮሚዩን የሶሻሊዝም ጽንስ ወይም መሰረት ነው ብሎ መቀበሉ ፍጹም የተሳሳተ ነበር ።

የጀግኖች ፣ ታላላቅ ግለሰቦችና አስተሳሰባቸው ከሰፊው ሕዝብ ማለትም «ከጀሌው» ፣ ከሕዝቡ ፣ ከመደቦች ሚና ጉልቶ በሕብረተሰብ እድገት ተቀዳሚውን ሚና ይጫወታል የሚለውን ሶስተኛውን የናሮዳውያንን ዋንኛ ስሕተት ፕሌክሀኖቭ መሰረት አሳጥቶታል ። ፕሌክሀኖቭ የናሮዳውያንን ሀሳባዊነት አውግዞ እውነቱ፡ በሀሳባዊነት ላይ የሚያርፍ ሳይሆን በማርክስና በኤንግልስ ቁስ አካላዊነት ላይ ነው በማለት የማርክሲስት ቁስአካላዊነትን አስረድቷል ።

ማርክሳዊ ቁስ አካላዊነትን በመከተል የኅብረተሰብ እድገት ለዘላቂው የሚወሰነው በታላላቅ መሪዎች ፍላጎትና አስተሳሰብ ሳይሆን ፣ ለሕብረተሰብ ህልውና በሚያስፈልገው በስልተ-ምርቱ፡ ውስጥ በቁሳዊ ሀብት መለወጥ ፣ በኅብረተሰብአዊ ሕልውና ቁሳዊ ሁኔታዎች ማደግ ፣ በቁሳዊ ምርት ውስጥ በመደቦች የጋራ ተዛምዶ መለወጥ ፣ በምርቱ፡ ከመደቦች ለቦታና ለስልጣን በሚያደርጉት ትግል እንዲሁም በቁሳዊ



የሀብት ክፍፍል ሁኔታ የሚወሰን ነው ። የሰዎችን ምጣኔ-ሀብታዊና ማኅበራዊ ደረጃ የሚወስኑት ሀሳቦች አይደሉም ። ነገር ግን የሰዎች ማህበራዊና ምጣኔ ሀብታዊ ደረጃዎቻቸው አስተሳሰባቸውን ይወስናሉ ። የታላላቅ ሰዎች አስተሳሰባቸውና ፍላጎታቸው የኅብረተሰቡን ምጣኔ-ሀብታዊ እድገት ፤ የተራመደውን መደብ ፍላጎት የሚቃረን እስከሆነ ድረስ ሕልውናቸው ይወገዳል ። በተገላቢጦሽ ፤ አስተሳሰባቸውና ፍላጎታቸው በትክክል የሕብረተሰቡን ምጣኔ-ሀብታዊ እድገት ፤ የአይነተኛውን መደብ ፍላጎት በሚገባ ከገለጹ በእርግጥ ምርጥ ግለሰቦች ይሆናሉ ።

ሰፊው ሕዝብ ጀሌ እንጂ ሌላ ምንም ነገር ሊሆን አይችልም ፣ ጀግኖች ብቻ ናቸው ታሪክን የሚሰሩትና ጀሌውን ሕዝብ የሚለውጡት ፣ ለሚሉት ናሮዳውያን ማርክሲስቶች ታሪክን የሚሰሩት ጀግኖች አይደሉም እንዲያውም ጀግኖችን የሚፈጥረው ታሪክ ነው ። እንዲሁም በመቀጠል ሕዝቡን የሚፈጥሩት ጀግኖች ሳይሆኑ ጀግኖቹን የፈጠረ ሕዝብ ታሪክን ወደፊት ሊያንቀሳቅስ ይችላል በማለት የጸና መልስ ይሰጣሉ ። ጀግኖችና የታወቁ ግለሰቦች በኅብረተሰብ ኑሮ ውስጥ ጠቃሚ ሚና ሊጫወቱ የሚችሉት የሕብረተሰብን የእድገት ሁኔታ በሚገባ የመረዳት ችሎታ ሲኖራቸውና የሚለወጡበትን መንገድ ጠንቅቀው እስከተረዱ ድረስ ብቻ ነው ። ጀግኖች ፣ የታወቁ ግለሰቦች ፣ የሕብረተሰብን የእድገት ሁኔታ በሚገባ ካልተገነዘቡና የታሪክ «ሰሪዎች» ነን በሚለው እምነታቸው ከሕብረተሰቡ ታሪካዊ ፍላጎት በተቃራኒው ከቆሙ የሚፌዝባቸውና መጥፎ አወዳደቅ የሚገጥማቸው ይሆናሉ ።

በዚህ ዓይነቱ ዋጋ ቢስ የጀግንነት ዘርፍ ናሮዳውያን ይመደባሉ ።

ፕሌክሀኖቭ በናሮዳውያን ላይ ባካሄደው ትግሉና በጻፋቸው ጽሁፎች ናሮዳውያን በአብዮታዊ ምሁራን መሀከል የሚያደርሱትን ተጽእኖ ዝቅ አድርጎታል ። ይሁን እንጂ የናሮዳውያን የርእዮተ-ዓለም ብከላ ገና ጥራት አላገኘምና እንደማርክሲዝም ጠላትነቱ ሌኒን የማከተሚያ ሞት ሰጥቶታል ።

«የናሮድንያቮሊያ» ፓርቲ በዛሩ አገዛዝ መታፈን ከጀመረ በኋላ ወዲያውኑ የሚያካሂዱትን ጸረ-ዛር አገዛዝ አብዮታዊ ትግል በመክዳት የመታረቅና የመስማማት መርህ መስበክ ጀመሩ ። በሰማንያዎቹና በዘጠናዎቹ ዓመታት ናሮዳውያን የሐብታም ገበሬዎችን ፍላጎት ማስተጋባት ቀጠሉ ።

«የሰራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን ለሩስያ ሶሻል ዲሞክራቶች ሁለት መርሀ-ግብር ነደፉ (የመጀመሪያው በ1884 ሁለተኛው በ1887) ። ይህ ደግሞ በሩስያ ውስጥ የማርክሲስት የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ለመመስረት እጅግ ጠቃሚ የመሰናዶ እርምጃ ነበር ።

ይሁን እንጂ ከዚሁ ጋር «የሠራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን አንዳንድ ከባድ ስህተቶችን ፈጽሟል ። የነደፈው የመጀመሪያ መርሀ-ግብር የናሮዳውያን አመለካከት ቅሪቶችን የያዘ ሲሆን ፣ የግለሰብ አሸባሪነት ታክቲክም

ትውስ የሚለው ነበር ። ከዚህምበላይ ፕሌክሀኖቭ በአብዮታዊ ሂደት ውስጥ ወዛደሩ ገበሬውን ለመምራት መቻሉንና መሆንም እንዳለበት ፣ እንዲሁም ከገበሬው ጋር በሚፈጥረው አጋርነት ብቻ የዛሩን አገዛዝ በማውደም ፣ ድልን መቀዳጀት እንደሚችል አልተቀበለም ነበር ። ፕሌክሀኖቭ ምንም እንኳን ለዘብተኛው ቡርዧ ወላዋይ ድጋፍ የሚሰጥ ቢሆንም ቅሉ ልክ እንደ አንድ አብዮታዊ ኃይል በመቁጠር ፣ በአንዳንድ ጽሑፎች እንዲያውም ገበሬውን ቦታ አሳጥቶት እንደነበረ ከሚከተለው ጽሑፉ መረዳት ይቻላል ።

«ከቡርዧውና ከወዛደሩ በቀር በሀገራችን ውስጥ ምንም የተቃዋሚ ወይም የአብዮታዊ አሰላለፎች ድጋፍ የምናገኝበት እንዳችም ማኅበራዊ ኃይል የለም»

የፕሌክሀኖቭ ፤ ሥራዎች ፤ የሩሲያ እትም ቅጽ 3 ገጽ 119

ይህ የተሳሳተ የፕሌክሀኖቭ አመለካከት ለሜንሼቪኮች አመለካከት መነሻ ጀርም ነበር ።

«የሰራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን ወይም በወቅቱ የነበሩ ማርክሳዊ ክበቦች ገና እንዳችም ግንኙነት ከሰራተኛው መደብ ንቅናቄ ጋር አልነበራቸውም ። ወቅቱ የማርክሲዝም ንድፈ-ሀሳብ ፣ የማርክሲዝም አስተሳሰብና የሶሻል ዲሞክራቲክ መርሀ-ግብር የታየበትና የተቆናጠጠበት ወቅት ነበር ። በአስሮቹ አመታት ውስጥ (1884—94) የሶሻል ዲሞክራቲክ ንቅናቄዎች የተነጣጠሉ ትናንሽ ቡድኖችና ግንኙነት የሌላቸው ክበቦች ወይም በጣም ጥቂት ግንኙነት ያላቸው ፣ ክበቦች ከሠራተኛው መደብ ንቅናቄዎች ጋር ይገኙ ነበር ። ገና እንዳልተወለደ ነገር ግን በናቱ ማህጸን ውስጥ እንዳደገ ሕጻን ሁሉ የሶሻል ዲሞክራቲክ ንቅናቄ ሌኒን እንዳለው «በእንጻራዊ የእድገት ሂደት» ውስጥ ነበር ።

«የሠራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን ሌኒን እንዳለው ለሶሻል ዲሞክራቲክ ንቅናቄ ንድፈ-ሀሳባዊ መሰረት ከመጣሉም ሌላ ለሰራተኛው መደብ ንቅናቄ የመጀመሪያ እርምጃ ሆነ ።

በሩስያ ውስጥ ማርክሲዝምንና የሰራተኛውን መደብ ንቅናቄ የማዋሀዱና «የሰራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን የሰራቸውን ስህተቶች የማረሙ ተግባር በሌኒን ጫንቃ ላይ ወደቀ ።

## 3. የሌኒን አብዮታዊ ተግባራት መጀመር ።

## የቅዱስ ፔተርስበርግ ሊግ ለሰራተኛው መደብ ነጻነት ያደረገው ትግል ።

የቦልሼቪዝም መሥራች የሆነው ቭላድሚር ኢሊች ኢሊያኖቭ (ሌኒን) በ1870 ዓ.ም. በሲምብራስክ (አሁን ኢሊያኖቭስኪ ተብሎ በሚጠራው) ከተማ ተወለደ ። በ1887 ዓ.ም. ሌኒን ወደ ካዛን ዩኒቨርስቲ ገባ ። ይሁን እንጂ በአብዮታዊ የተማሪዎች ሰላማዊ ሰልፍ ውስጥ በመሳተፉ በዛሩ ወታደሮች ተይዞ ታሰረ ፣ ከዩኒቨርስቲውም ተባረረ ። ሌኒን ፣



በካዛን ውስጥ ፌዲሴቭ በመሠረተው አንድ የጥናት ክበብ ውስጥ ገባ ። በኋላም ወደ ሳማራ በመሄድ በከተማው ውስጥ የመጀመሪያውንና እንደ ማእከላዊው የሚታየውን ማርክሳዊ የጥናት ክበብ መሠረተ ። በዚያን የእንቅስቃሴ ወቅቶች በትምህርቱ ስለማርክሲዝም ያለው እውቀት ብዙዎችን ያስገርም ነበር ።

በ1893 ዓ.ም. መጨረሻ ሌኒን ወደ ቅዱስ ፒተርስ በርግ ተጓዘ ። በከተማው ውስጥ ላሉት ማርክሲስት የጥናት ክበቦች የመጀመሪያውንና በአባሎቹም ላይ ታላቅ ስሜት ያሰፈነ ንግግር አደረገ ። የማርክሲዝምን ጠሊቅ እውቀት ከማወቁም በላይ ማርክሲዝምን በወቅቱ ከነበረው የሩስያ ፖለቲካዊና ምጣኔ-ሀብታዊ ሁኔታ ጋር የማገናዘብ ችሎታው ፣ በሠራተኛው ድል አድራጊነት ላይ ያለው ዘሊቅ ስሜትና ፣ የማይናወጥ እምነቱ ፣ የማደራጀት ተሰጥእው ሌኒንን የቅዱስ ፒተርስበርግ ማርክሲስቶች እውቅ መሪ አድርጎታል ።

ሌኒን በጥናት ክበብ ባስተማራቸውና ፖለቲካዊ ንቃት ባላቸው ሠራተኞች ዘንድ ከፍተኛ ድጋፍና ተቀባይነት አተረፈ ።

«የሚደረጉልን ገለጻዎች» ይላል ሠራተኛው ባቡሽኪን በሠራተኞች የጥናቱ ክበብ ውስጥ የሌኒንን የማስተማር እንቅስቃሴዎች ፤ በማስታወስ ፣ «እጅግ የሚጥሙና የማነሳሳት ጸባያት ነበራቸው ። በነዚህ ገለጻዎች በጣም እንረካ ነበርና ዘወትር የመምህራችንን ጥበብ እናደንቃለን» ።

በ1895 በቅዱስ ፒተርስበርግ የሚገኙትን የሠራተኞች ማርክሳዊ የጥናት ክበቦችን በሙሉ (ሀያ ያህል የሚሆኑትን) የሠራተኛውን መደብ ነጻ ለማውጣት ወደሚታገል አንድ ሊግ አዋሀዳቸው ፤ በመሆኑም ለአብዮታዊ የሠራተኞች ማርክሳዊ መፈጠር መንገድ አዘጋጀ ።

ሌኒን ፤ ሊጉ ከሰፊው ሠራተኛ መደብ እንቅስቃሴ ጋር የጠበቀ ግንኙነት እንዲኖረው ፖለቲካዊ አመራሩንም እንዲይዝ የሚያስችለውን ተግባር አመጣ ። ሌኒን ፖለቲካዊ ቅስቀሳ በፕሮፓጋንዳ ክበቦች ውስጥ ከተሰበሰቡ ጥቂት ከነቁ ሠራተኞች አልፎ ወደ ሰፊው የሰራተኛ መደብ በመሸጋገር ፣ የወቅቱን ጥያቄ በማንሳት ፤ መቀስቀስ አለብን ሲል አሳሰበ ። ይህ ሰፊውን ሠራተኛ ለመቀስቀስ የተደረገው ትኩረት በሩስያ ውስጥ በመከታተል ለተነሱት የሠራተኛው መደብ ንቅናቄ እድገት ታላቅ ጠቀሜታ ነበር ።

በዘጠናዎቹ አመታት ውስጥ ኢንዱስትሪዎች በፍጥነት ያደጉበት ወቅት ነበርና ወዛደሮች በቂ ቁጥር ጨመሩ ። የሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ጥንካሬ እያገኘ መጣ ። በ1895—99 ባሉት ወቅቶች ፣ ባልተሟላ መረጃ መሰረት ፣ ከ221,000 የማያንሱ ሠራተኞች በሥራ ማቆም አድማዎች ውስጥ ሲሳተፉ የሠራተኛው መደብ ንቅናቄም በሀገሪቷ ፖለቲካዊ ሕይወት ውስጥ ጠቃሚው ኃይል ሊሆን በቃ ። የድርጊቶች ሂደት ማርክሲ

ዝም በናሮዳዊያን ላይ ያለውን አሸናፊነት በተጨማሪ መረጃዎች ሊያረጋግጥ በቃ ። በሌላም አባባል የሰራተኛው መደብ በአብዮታዊ ንቅናቄ ውስጥ መሪ ሀይል መሆኑን አረጋገጠ ። የሰራተኛው መደብ ነጻ አውጪ የትግል ሊግ በሌኒን መመሪያ መሰረት ሠራተኞች ለምጣኔ-ሀብት ጥያቄዎች የሚያደርጉትን ትግል ፤—የሥራ ሁኔታዎች መሻሻል ፤ የሥራ ሰዓት መቀነሥና የደሞዝ መጨመር በዛሩ መንግሥት ላይ ከሚያደርጉት ፖለቲካዊ ትግል ጋር በማቀ ናጀት ሰራተኞችን በፖለቲካዊ መስክ በማስተማር አዘጋጁት ።

በሌኒን መመሪያ መሰረት ሶሻሊዝምን ከሰራተኛው መደብ ጋር ለማዋሀድ የተነሳ የመጀመሪያ አካል የቅዱስ ፒተርሰበርግ የሰራተኛ መደብ ነጻ አውጪ የትግል ሊግ ነበር ። የሥራ ማቆም አድማዎች በአንዳንድ ፋብሪካ ሲፈነዱ ሊጉ ፣ በፋብሪካው ውስጥ በሚገኙ የጥናት ክበቦች አባላት አማካይነት ጥያቄዎችን የያዙ በራሪ ወረቀቶችንና ሶሻሊስታዊ ይዘቶችን የያዙ ጽሁፎችን ወዲያውኑ ይበትናል ። እነዚህ በራሪ ወረቀቶች ወዝአደሮች በፋብሪካ ባለቤቶች የሚደርስባቸውን ጭቆና ያጋልጣሉ ፣ ሠራተኛው ለዓላማው እንዴት አድርጐ መታገል እንዳለበት ያብራራሉ ፣ የሰራተኛውን አንገብጋቢ ጥያቄዎች ያነሳሉ ። የካፒታሊዝምን የመረቀዙ ቁስሎች ፣ የሠራተኛውን ድህነት ፣ ከ12 —14 ሰዓት የሚሰሩትን አድካሚና አሰልቺ ሥራዎች እንዲሁም የመናገር መብት የመነፈጋቸውን እውነት ይገልጻሉ ። ከዚህም አልፈው የሠራተኛውን የፖለቲካ ጥያቄዎች ይጠይቃሉ ። በ1894 ዓ. ም. መጨረሻ ከሠራተኛው ባቢሽኪን ጋር በመተባበር ሌኒን የመጀመሪያውን ይህንን መሰል ቀስቃሽ በራሪ ወረቀት ጽፎ በቅዱስ ፒተርስበርግ በሥራ ማቆም አድማ ላይ ለነበሩት የሴምያኒኮ ሠራተኞች ጥሪ በማድረግ ጻፈላቸው ። በ1895 ዓ.ም. የበልግ ወራት በቶርንቶን ፋብሪካዎች ሥራ ላቆሙ ወንዶችና ሴቶች ሌኒን በራሪ ወረቀቶችን ጻፈላቸው ። እነዚህ ፋብሪካዎች በሚሊዮን የሚቆጠር አንጡራ ትርፍ የሚያካብቱት የእንግሊዝ ባለንብረቶች ነበሩ ። በነዚህ ፋብሪካዎች ውስጥ የሥራ ጊዜ ከ14 ሰዓቶች የበለጠ ሲሆን ፣ ለአንድ ሸማኔ የሚከፈለው ደሞዝ ግን በአንድ ወር ሰባት ሩብል ያህል ብቻ ነበር ። ሠራተኞቹ በአደረጉት የሥራ ማቆም አድማ ድልን ሲጐናጸፉ በአጭር ጊዜ ውስጥ የትግሉ ሊግ እንደዚህ ያሉ በደርዘን የሚቆጠሩ በራሪ ወረቀቶችን በማተም በተለያዩ ሙያ ለተሰማሩ በርካታ ሠራተኞች ጥሪ አደረገ ። እያንዳንዱ በራሪ ወረቀት የሠራተኞችን መንፈስ ለማጠንከር የሚረዳ በመሆኑ ሶሻሊስቶች ሠራተኛውን እንደሚረዱና አብረዋቸው እንደሚታገሉ በግልጽ ማየት ቻሉ ።

በበጋው 1896 ዓ. ም. 30,000 የሚሆኑ የጨርቃ ጨርቅ ሠራተኞች በሊጉ እየተመሩ በቅዱስ ፒተርስበርግ ውስጥ የሥራ ማቆም አድማ አደረጉ ። ጥያቄያቸውም የሥራ ሰዓት ስለመቀነስ ነበር ። ይህ ከባድ እንቅስቃሴ የዛሩ አገዛዝ በሰኔ 1897 ዓ.ም. በቀን የሥራ ሰዓት



ወደ 11½ ሰዓቶች ዝቅ የሚያደርገውን ሕግ እንዲያወጣ ተገደደ ። ከዚህ ቀደም የሥራ ሰዓቶች ፍጹም አልተወሰኑም ነበር ።

በታህሣሥ 1895 ዓ.ም. ሌኒን በዛሩ አገዛዝ ተይዞ ታሠረ ። ይሁን እንጂ እስሩ የሌኒንን አብዮታዊ ተግባር አላገደውም ። ዘወትር ለትግሉ ሊግ ምክርና መመሪያ ከመስጠቱም በላይ ጽሁፎችን እያዘጋጀ ያቀርብ ነበር ። በእስር ቤት እያለ ስለ ሥራ ማቆም አድማ በሚል ርዕስ አንድ ጽሁፍ እንዲሁም ለዛሩ አገዛዝ በሚል ርዕስ በራሪ ወረቀት በመጻፍ አውሬአዊ አገዛዙን አጋለጠ ። ሌኒን ለፓርቲው መርሀ-ግብር የነደፈው ወተት እያጠቀሰ በያዘው የሕክምና መጽሐፍ መስመሮች መሀከል በመጻፍ ነበር ።

በቅዱስ ፒተርስበርግ የሚገኘው የትግል ሊግ በሌሎች ከተሞችና በሩሲያ አካባቢዎች የሚገኙ የጥናት ክበቦች በቅናንሽ ሊጎች እንዲዋሀዱ ጠንካራ ግፊት ሰጣቸው ። በዘጠናዎቹ ዓመታት አጋማሽ ላይ በትራንስካውካሲያን ውስጥ ማርክሲስት ድርጅቶች ተመሠረቱ ። በ1894 በሞስኰ ውስጥ የሠራተኞች አንድነት ተመሠረተ ። በዘጠናዎቹ መጨረሻ ላይ የሶሻል ዲሞክራቲክ አንድነት በሳይቤሪያ ውስጥ ተመሠረተ ። በዘጠናዎቹ ውስጥ በኤቫኖቮ-ቮዝኔሴንስክ ፣ በያሮስለቭና በኮስትሮማ ማርክሲስት ቡድኖች ተመሠረቱ ። ከዚህም ጋር የሰሜን አንድነት በመያዝ የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲን ለመፍጠር ተዋሀዱ ። በዘጠናዎቹ ዓመታት ሁለተኛው አጋማሽ ላይ የሶሻል ዲሞክራቲክ ቡድኖች በሮስቶቭ—ኦን—ዶን በኢካቶሪኖስላቭ ፣ በኩዮቭ ፣ በቭኩላየቭ ፣ በቱላ ፣ በሳማራ ፣ በካዛን ፣ በኦሬኮሆቭ ፣ በዘዩናና በሌሎችም ከተሞች ተመሠረቱ ።

የቅዱስ ፒተርስበርግ የትግል ሊግ ለሰራተኛው መደብ ነጻነት የያዘው ጠቀሜታ ሌኒን እንዳለው በእውነተኛ የሠራተኛው መደብ እንቅስቃሴ ለሚደገፍ አብዮታዊ ፓርቲ የመጀመሪያ እርምጃ ነበር ።

ከቅዱስ ፒተርስበርግ የትግል ሊግ አብዮታዊ ልምድ ላይ በመነሳት ሌኒን በሩሲያ ውስጥ ማርክሲስት የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ የመፍጠር ተግባሩን ነደፈ ።

ሌኒንና የቅርብ የትግል ጓዶቹ ከታሰሩ በኋላ የቅዱስ ፒተርስበርግ የትግል ሊግ አመራር ሊተኰርበት በሚገባ ሁኔታ ተለወጠ ። ራሳቸውን «ወጣት» ፣ ሌኒንንና ግብረአበሮቹን «ጥንታዊያን» ብለው የሚጠሩ አዲስ ሰዎች ብቅ አሉ ። እነዚህ ሰዎች የተሳሳተ የፖለቲካ መስመር ያራምዱ ነበር ። ሠራተኞች አሰሪዎቻቸውን የደሞዝ ጥያቄን በመጠየቅ በምጣኔ-ሀብቱ ትግል ላይ ብቻ ማትኰር አለባቸው ሲሉ ለፈፉ ። የፖለቲካው ትግል የወዝ አደሩ ተግባር ሳይሆን የለዘብተኛው ቡርዧ ተግባር በመሆኑ ለእርሱ መተው አለበት አሉ ።

እነዚህ ሰዎች «ኢኰኖሚስቶች» በመባል ይጠሩ ጀመር ።

እነርሱም በሩሲያ የሚገኙ የማርክሲስት ድርጅቶችን አመራር የያዙ የመጀመሪያዎቹ አጕብዳጆችና አድርባዮች ቡድን ነበሩ ።

**4. ሌኒን ከናሮዲዝምና ከ «ሕጋዊ ማርክሲስቶች» ጋር ያደረገው ትግል ፤ የወዝአደሩና የገበሬው አጋርነት የሚለው የሌኒን ሀሳብ ፤ የመጀመሪያው የሩሲያ የሶሻል ዲሞክራቲክ የሰራተኞች ፓርቲ ኰንግሬስ**

ምንም እንኳን ፕሌክሀኖቭ የናሮዳውያንን አመለካከት በስማኒያዎቹ ውስጥ ደህና አድርጐ ቢመታውም በዘጠናዎቹ መግቢያ ላይ የናሮዳውያን አስተሳሰብ የሚያስተናግዱ ደጋፊዎች በአብዮታዊ ወጣቶች አካባቢ አሁንም አልጠፉም ። አንዳንዶቹ ሩሲያ ለእድገቷ የምትከተለውን የካፒታሊዝም ፈለግ ማስወገድ አለባት ፤ እንዲሁም በአብዮቱ ውስጥ ቅልቁን ሚና የሚጫወቱት ገበሬዎች ናቸው እንጂ የወዝአደሩ መደብ አይደለም በማለት ፈለጋቸውን ማንገብ ጀመሩ ። የናሮዳውያን ርዝራዦች ማርክሲዝም እንዳይስፋፋ የሚችሉትን ያህል ሁሉ ተከላከሉ ፤ ማርክሲስቶችን ታገሉ ፣ በማናቸውም ሥፍራ ዋጋ ለማሳጣት የቻሉትን ሁሉ ሞከሩ ። በርግጥም ማርክሲዝምን ለማስፋፋትና የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲን ለመፍጠር ከተፈለገ ናሮዲዝም በሚገባ በርዕዮተ-ዓለም መመታት ይኖርበት ነበር ።

ይህም ተግባር በሌኒን ተከናወነ ።

«የሕዝቡ ወዳጆች» እነማናቸው ፣ እንዴትስ አድርገው ነው ሶሻል ዲሞክራቶችን የሚታገሉት በሚለው መጽሀፉ (1894) ናሮዳውያን አስመሳይ «የሕዝቡ ወዳጆች» መሆናቸውንና እንዲያውም በሕዝቡ ላይ የተነሱ መሆናቸውን በሚገባ አሳየ ።

በመሰረቱ ፣ በዘጠናዎቹ ውስጥ ናሮዳውያንን በዛሩ ላይ የሚደረገውን መላውን አብዮታዊ ትግል ለዘብተኛ ናሮድኒካውያን ከዛሩ አገዛዝ ጋር እርቅን ይሰብኩ ነበር ። «እነርሱ እንደሚያስቡት» ይላል ሊኒን ፣ በዚያ ወቅት በቀላሉ በዛሩ ስለነበሩት ናሮዳውያን አስመልክቶ ሲጽፍ «ወደፊት መሆኑ ለማይቀረው ሁኔታ በቅድሚያ በቀላሉ ከዛር አገዛዝ ጋር በጥሩ ሁኔታ ከተስማሙና ቅን አገልጋይነታቸውን ካረጋገጡለት ሁሉንም ነገር በሚገባ ይፈጽማል ። » («የሕዝቡ ወዳጆች»እነማን ናቸው ፣ እንዴት ነው ሶሻል ዲሞክራቶችን የሚታገሉት ፣ ከሚለው የሌኒን ጽሑፍ የተወሰደ ፣ እንግሊዝኛ እትም ሞስኮ 1946 ገጽ 157 )

የዘጠናዎቹ ዓመታት ናሮድኒካውያን የደሀ ገበሬውን ሁኔታ ፣ በገጠር የሚደረገውን የመደብ ትግልና ደሀ ገበሬዎችን በሀብታም ገበሬዎች መበዝበዝ እያዩ አይናቸውን ጨፍነው ለሀብታም ገበሬዎች እርሻ ማደግ የምስጋና መዝሙር ይዘምራሉ ።



ከዚሁ ጋር በሚያወጡት እቅዎች በናሮድኒካውያን ማርክሲስቶችን አጠመዷቸው ። ሆን ብለው የሩሲያን ማርክሲስቶችን አመለካከት በማውገርገርና ውሸት በማስመሰል ፡—ማርክሲስቶች ገጠሩን በማፍረስ «መላውን የሩሲያ ገበሬ የፋብሪካ ሠራተኞች ሊያደርጓቸው ነው» አሉ ። ሌኒን ይህንን የናሮድኒካውያንን ሂስ ውሸት መሆኑን በማጋለጥ ይህ በማርክሲስቶች «ፍላጐት» የሚሆን ሳይሆን ካፒታሊዝም በሩሲያ ውስጥ የማደጉና ዕድገቱም በማይቀር ሁኔታ ከወዝአደሩ ዕድገት ጋር በመጣመሩ ስለሆነ ወዝአደሮች የካፒታሊዝም መቃብር ቆፋሪ ይሆናሉ በማለት አብራራ ።

የሕዝቡ እውነተኛ ወዳጆች ማርክሲስቶች እንጂ ናሮድኒካውያን እንዳልሆኑ ሌኒን አሳየ ፤ ማለትም ፣ ማርክሲስቶች ብቻ ናቸው ካፒታሊዝም እንዲወድምና የመሬት ከበርቴዎች ቀንበር እንዲንኰታኰት በአንድ ቃልም የዛሩ አገዛዝ እንዲወድቅ የሚፈልጉት ።

« የሕዝቡ ወዳጆች » እነማን ናቸው በሚለው መጽሐፉ ሌኒን ለመጀመሪያ ጊዜ የወዝ አደሩንና የገበሬውን አጋርነት የዛሩን አገዛዝ ፣ የመሬት ከበርቴዎችንና ቡርዧዎችን ለማስወገድ ዋነኛ መንገድ ነው የሚለውን አብዮታዊ አስተሳሰብ አራመደ ።

በዚህ ወቅት ሌኒን በጻፋቸው በርካታ ጽሁፎች ዋነኞቹ የናሮድኒካ ቡድኖች «ናሮድናያቮሊያ» ና ኋላም የናሮድኒክ ተከታዮች ሶሻሊስት አብዮተኞች የሚጠቀሙበትን ፡— በተለይም የግለሰብ አሸባሪነት—ፖለቲካዊ የትግል ዘዴአቸው ላይ ሂስ አቀረበ ። ሌኒን የሰፊውን ሕዝብ ትግል በግለሰብ ጀግኖች ትግል የተኩትን የናሮዳውያን ታክቲኮች ለአብዮታዊ ንቅናቄ እጅግ ጐጂ መሆናቸውን አበክሮ አጤነ ። በሕዝቡ አብዮታዊ ንቅናቄዎች ላይ ምንም እምነት እንደሌላቸው ተገነዘበ ።

«የሕዝቡ ወዳጆች» እነማን ናቸው በሚለው መጽሐፉ ሌኒን የሩሲያ ማርክሲስቶችን ዓይነተኛ ተግባር ነድፎ አወጣ ። በርሱ አስተያየት የሩሲያ ማርክሲስቶች የመጀመሪያ ተግባር የተበታተኑትን የማርክሲስቶች የጥናት ክበብ ወደ ተዋሀደ የሠራተኞች ሶሻሊስት ፓርቲ ማደራጀት መሆኑን ጠቆመ ። ከዚህም በመዝለቅ በሩስያ ውስጥ የወዛደሩን መደብ ከገበሬው ጋር በመተባበር ነው የዛሩን ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ሊያወድም የሚችለው ። የሩሲያ ወዝአደሮች ፣ ከገበሬው ፣ ከምዝብሩ ሰፊ ሕዝብና ከሌላ አገር ወዛደሮች ጋር በመሆን ግልጽ የፖለቲካ ትግል ትክክለኛ ጐዳና በመከተል ብቻ ለድል አድራጊው የኮሚኒስት አብዮት መብቃት ይችላል ።

ስለሆነም ከ40 ዓመታት በፊት ሌኒን የሠራተኛው መደብ የሚከተለውን የትግል ፈለግ ፣ በኅብረተሰቡ ውስጥ ከሁሉም መደብ በላይ አብዮታዊ ኃይል መሆኑን ገበሬውም የወዝአደሩ ዓይነተኛ አጋር መሆኑን በትክክል ገለጸ ።

በሌኒንና በተከታዮቹ የተደረገው ጸረ-ናሮዳዊነት ትግል በዘጠናዎቹ ዓመታት ውስጥ የናሮዳውያንን ርዕዮት-ዓለማዊ ሽንፈት አስከትሏል ።

ሌላው የማይዘነጋው ትልቁ የሌኒን ተግባር «ከህጋዊ ማርክሲስቶች» ጋር ያደረገው መራራ ትግል ነው ። በታሪክ እንደሚታየው በትላልቅ ኅብረተሰብአዊ ንቅናቄዎች ውስጥ እግደው የሚይዙ «መንገደኞች» እንዳሉ ሁሉ ሕጋዊ ማርክሲስቶችም እንደመጠሪያቸው እንደነዚህ «መንገደኞች» ነበሩ ። ማርክሲዝም በሩሲያ ውስጥ በሰፊው መሰራጨት ጀምሮአልና የቡርዧው ምሁሮች በማርክሲስት ሽማ ራሳቸውን አጋጊጠው እናገኛለን ። የዛሩ አገዛዝ ስለፈቀደላቸው የራሳቸውን ጽሁፎች በጋዜጦችና በልሳኖቻቸው ላይ ይጽፋሉ ። ለዚህም ነው «ሕጋዊ ማርክሲስቶች» የሚል መጠሪያ ያገኙት ።

በራሳቸው የአስተሳሰብ ክልል ናሮዳዊነትን በሚገባ ተዋግተዋል ። ይሁን እንጂ ያካሄዱት ጸረ-ናሮዳውያን ትግልና የማርክሲዝም ሰንደቅ ፥ የሠራተኛውን መደብ ንቅናቄ ለቡርዧው ሕብረተሰብ ፍላጐት ፥ ለቡርዧው ዓላማ አገልጋይና ተስማሚ እንዲሆን ሞክረዋል ። የማርክሲዝም ማእከል የሆነውን የወዝአደር አብዮትና የወዛደሩን አምባገነንነት አስተምህር ገንጥለው አወጡት ። አንድ የተከበረ ሕጋዊ ማርክሲስት ፔተር ስትሮቭ በካፒታሊዝም ላይ አብዮታዊ ትግል እንዲካሄድ ጥሪ ከማድረግ ፈንታ ቡርዧውን በማወዳደስ «የባሕላችንን ደካማነት አውቀን ለትምህርት ወደ ካፒታሊዝም እናመራለን» በማለት ይቀሰቅስ ነበር ።

ከናሮዳውያን ጋር በሚደረገው ትግል ሌኒን «ሕጋዊ ማርክሲስቶችን» ሊጠቀምባቸው በማሰብ — ለምሳሌ በሚደረገው ጸረ-ናሮድኒክስ ትግል የጋራ የሆነ የጽሁፍ እትም ለማዘጋጀት ጊዜአዊ ስምምነት ማድረግ እንደሚቻል ተገንዝቦ ነበር ። በተጨማሪም ሌኒን ባቀረበው ሂስ «የሕጋዊ ማርክሲስቶችን» የለዘብተኛ ቡርዧው ጸባይ አጋልጧል ።

ከነዚህ መንገደኞች አብዛኛዎቹ ዘግየት ብለው የሕገ-መንግስታዊ ዲሞክራት( የሩሲያ ቡርዧዎች ትልቁ ፓርቲ) ና በሕዝባዊ ጦርነት ወቅት የለየላቸው ነጭ ዘቦች ሆኑ ።

በቅዱስ ፔተርስበርግ ካሉት ሊጐች መሀከል በሞስኮ ፥ በኪቭና በሌሎች ሥፍራ የሩሲያ የጠረፍ ምዕራባዊ ዳርቻ ዲሞክራቲክ ድርጅቶች አበቡ ። በዘጠናዎቹ ዓመታት በፖሊሽ ብሔረተኛ ፓርቲ ውስጥ የሚገኙ ማርክሲስቶች የፖላንድና የሊቱዋኒያ ሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ለመፍጠር ተገንጥለው ወጡ ። በዘጠናዎቹ ዓመታት መጨረሻ የላቲቪያ ሶሻል ዲሞክራቲክ ድርጅት ተመሥርቶ ነበር ። እንዲሁም በጥቅምት 1897 ዓመታት የአይሁዳውያን አጠቃላይ የሶሻል ዲሞክራቲክ ሕብረት በንድ ተብሎ የሚታወቀው በሩሲያ ምዕራባዊ ግዛቶች ተመሠረተ ።



በ1898 በርካታ የትግል ሊግ ፡— በቅዱስ ፔተርስበርግ ፥ በሞስኮ ፥ በኪቮና በኢኳቶሪናስላቭ ከበንድ ጋር በመዳመር ለማዋሀድና የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ለመፍጠር የመጀመሪያውን ሙከራ አደረጉ ። በዚህም የተነሳ የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቲክ የሠራተኞች ፓርቲ(R.S.P.L.P.) የመጀመሪያ ኮንግሪስ በመጋቢት ወር 1898 በሚንስክ ውስጥ ተካሄደ ።

የመጀመሪያው የሩሲያ የሶሻል ዲሞክራቲክ የሰራተኞች ፓርቲ ኩንግረስ የተካሄደው በዘጠኝ ሰዎች ነበር ። ሌኒን በዚያን ጊዜ በሳይቤሪያ ውስጥ በግዞት ላይ ስለነበር በኩንግረሱ አልተገኘም ። በኩንግረሱ ላይ የተመረጡት የማዕከላዊ ኰሚቴ አባላት ወዲያውኑ ታሰሩ ። በኩንግረሱ ስም የወጡት መግለጫዎች የሚያረኩ አልነበሩም ። የፖለቲካ ሥልጣን በወዝአደሩ እጅ የመሆኑን ጥያቄ በማዳፈን ፥ እንዳችም ስለወዝአደሩ የበላይነት የሚያወሳ ነጥብ ካለመኖሩም በላይ ከዛሩ አገዛዝና ከቡርዧው ጋር በሚያደርገው ትግል ከገበሬው ጋር ሊኖረው ስለሚገባው አጋርነት እንዳችም ነጥብ አላነሳም ።

ኩንግረሱ በውሳኔዎቹና በመግለጫዎቹ የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቲክ የሰራተኞች ፓርቲ መመሥረቱን አበሰረ ።

በዚህ ተለምዶአዊ ተግባር ነው የመጀመሪያው የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቲክ የሰራተኞች ፓርቲ (ሩ.ሶ.ዲ.ሠ.ፓ) ኩንግረሱ ታላቅ አብዮታዊ የቅስቀሳ ሚና የተጫወተው ።

ይሁን እንጂ የመጀመሪያው ኩንግረስ ቢካሄድም እንደ ዕውነቱ ከሆነ ምንም ማርክሳዊ ሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ገና በሩሲያ አልተመሠረተም። ኩንግረሱ የተበታተኑትን የማርክሲስት የጥናት ክበቦችና ድርጅቶች ለማዋሀድና በአንድ ድርጅት ሥር ለማስተሳሰር አልቻሉም ። በአካባቢ ድርጅታዊ ተግባራት ፥ በፓርቲ ፕሮግራም ፥ በፓርቲ ሕጐች ወይም በአንድ ብቸኛ የአመራር ማዕከል ላይ አንድ የሚያደርጋቸው የጋራ የድርጊት መግለጫ ገና አልተመሠረተም ።

በዚህና በሌሎችም በርካታ ምክንያቶች ርዕዮተ-ዓለማዊ ውዥንብር በአካባቢ ድርጅቶች ውስጥ እየጨመረ በመሄድ በሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ውስጥ እንደ «ኢኮኖሚዝም» ላለ የአድርባይነት ዝንባሌ ማደግ ጥሩ ሁኔታን ፈጠረ ።

ይህን ውዥንብር ለመቋቋም የሚያዘጋጁት ኢስክራ የበርካታ ዓመታትን ጥረት ጠይቋል ። ሌኒን የአድርባዮች መዋዠቅን መደምደሚያ በመስጠት የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቲክ የሠራተኞች ፓርቲን ለመፍጠር ጥርጊያ መንገድ ሊከፍት ችሏል ።

## 5. ሌኒን «ከኢኮኖሚዝም» ጋር ያደረገው ትግል

### የሌኒን ጋዜጣ «ኢስክራ» እየታተመ መውጣት መጀመሩ

የመጀመሪያው የ.ሩ.ሶ.ዲ.ሠ.ፖ ኩንግረስ ሲካሄድ ሕጋዊ ተቃውሞ
ያራምዱ ከነበሩት ከትግል ሊጉ ጋር በተያያዘ ሁኔታ ሌኒን በቅዱስ ፒተር
ስበርግ ውስጥ በዛሩ አገዛዝ ተይዞ በመታሰሩና ኋላም በሳይቤሪያ ውስጥ
በምትገኝ ሹሼንስኩይ በምትባል መንደር በግዞት በመቀመጡ በኩንግ
ረሱ ውስጥ ሊሳተፍ አልቻለም ።

ይሁን እንጂ አብዮታዊ ግዴታውን በግዞት ላይ እያለም ቢሆን ተወ
ጥቶታል ። የካፒታሊዝም እድገት በሩሲያ በሚል ርዕስ የጻፈው የናሮዳው
ያንን የርዕዮተ-ዓለም ማጠቃለያ የሚሰጥ ከፍተኛ ጠቀሜታ ያለውን ሳይን
ሳዊ ሥራ አጠናቋል ። የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቶች ተግባር የሚለው
እውቅ ጽሑፉንም የጻፈው በዚያው በግዞት ላይ እያለ ነበር ።

ምንም እንኳን ሌኒን ከቀጥታ አብዮታዊ ተሳትፎ ቢቋረጥም ፣ በአብ
ዮቱ ውስጥ ከሚሳተፉት ጓዶች ጋር መገናኘቱን አላቋረጠም ። ይህም በመ
ጻጻፍ ፣ ዜናዎችን በመለዋወጥና ምክር በመስጠት ይሳተፍ ነበር ። በዚህኑ
ወቅት ሌኒን «በኢኮኖሚስቶች» ላይ ሙሉ ትኩረት ያደርግ ስለነበረ ከማ
ንኛውም ሰው ይልቅ «ኢኮኖሚያዊነት» የአጕብዳጅነትና የአድርባይነት
ዋነኛው አስኳል መሆኑንና «ኢኮኖሚያዊነት» በሠራተኛው መደብ ንቅ
ናቄ ውስጥ የበላይነትን ቢያገኝ የወዝአደሩን አብዮታዊ ንቅናቄ ዝቅ
አድርጐ ስለሚመለከት ማርክሲዝም ወደ ሽንፈት እንደሚያመራ አረጋ
ገጠ ።

ስለሆነም ሌኒን «የኢኮኖሚስቶች» ድርጊትም በሚታይበት አካባቢ
ሁሉ ጠንካራ ተቃውሞ ማካሄድ ጀመረ ።

«ኢኮኖሚስቶች» ሠራተኞች በኢኮኖሚው ትግል ውስጥ ብቻ መሳ
ተፍ አለባቸው፤የፖለቲካው ትግል ሠራተኞች ሊደግፉት ለሚገባቸው ለለ
ዘብተኛው ቡርዧው መተው አለበት ይላሉ ። በሌኒን ዓይን ይህ አስተ
ምህር ማርክሲዝምን ማራቆት ነው ፣ ነጻ የሆነ የሠራተኞች የፖለቲካ
ፓርቲ አስፈላጊነትን መካድ ነው ፣ የሰራተኛውን መደብ የቡርዧው ፖለ
ቲካዊ ተቀጥላ ለማድረግ መሞከር ነው ።

በ1899 «የኢኮኖሚስቶች» ቡድን—ፕሮኮፖቪች ፣ ኩስኩቫና
ሌሎችም በኋላም ሕገ-መንግስታዊ — ዲሞክራቶች የሆኑት—አብዮታዊ
ማርክሲዝምን የሚቃወሙበትን መግለጫ አወጡ ፣ እንዲሁም ነጻ የሆነ
የሰራተኞች የፖለቲካ ፓርቲ የሚለውን አስተሳሰብና የሰራተኞች ነጻ የፖ
ለቲካ ጥያቄዎች እንዲወገዙ አሳሰቡ ። «ኢኮኖሚስቶች» የፖለቲካ ትግሉ
የለዘበተኛው ቡርዧው ሲሆን ፣ ሠራተኞች ከአሰሪዎቻቸው ጋር የሚያደ
ርጉት የኢኮኖሚ ትግል በቂያቸው ነው የሚለውን አባባል አነገቡ ።

ሌኒን ከነዚህ ከአድርባዮች ሰነድ ጋር ራሱን ካስተዋወቀ በኋላ በጣም
የሚቀራረቡ ማርክሲስት የፖለቲካ ስደተኞችን ስብሰባ ጠራ ። አስራ ሰባት
ማርክሲስቶች የተገናኙበትና በሌኒን መሪነት የተካሄደው ይህ ስብሰባ



«የኢኮኖሚስቶችን» አስተሳሰብ በሰፊው ሕዝብ መሀከል በሰፊው በማ
ጋለጥ ተቃወመ ።

ይህ በሌኒን የተጻፈው ጠንካራ ተቃውሞ በአገሪቷ በሚገኙ ማርክሲ
ስት ድርጅቶች ሁሉ እንዲዳረስ በማድረግ ለማርክሲስት አስተሳሰቦችና
ለሩሲያ ማርክሲስት ፓርቲ እድገት ታላቅ ሚና ተጫውቷል ።

የሩሲያ «ኢኮኖሚስቶች» በሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ውስጥ
በርንስቴናውያን በመባል የሚታወቁት የአድርባዩ በርንስቴይን ተከታ
ዮች የሚያራምዱትን አስተሳሰብ ዓይነት ይሰብካሉ ።

ስለሆነም ሌኒን «ከኢኮኖሚስቶች» ጋር ያደርገው ትግል በዓለም
አቀፍ ደረጃ ከአድርባዮች ጋር ያደረገው የአንድ ወቅት ትግል ነበር ።

«ኢኮኖሚዝምን» የመቋጋቱና ለነጻ የወዝአደሩ ፖለቲካ ፓርቲ
መፈጠር የመታገሉ ዋንኛ ተግባር የተካሄደው በሌኒን በሚዘጋጀው
ሕቡዕ ጋዜጣ በኢስክራ ነበር ።

በ1900 ዓ.ም. መጀመሪያ ላይ ሌኒንና ሌሎችም በሳይቤሪያ በግዞት
ላይ የነበሩ የትግል ሊግ አባሎች ወደ ሩሲያ ተመለሱ ። ሌኒንም በሩሲያ
አቀፍ ደረጃ ሕቡዕ የማርክሲስት ጋዜጣ ለማዘጋጀት አሰበ ። በሩሲያ ውስጥ
የሚገኙ በርካታ ማርክሲስት ክበቦችና ድርጅቶች አልተዋሀዱም ነበር ፣
በዚያን ሁኔታ ፣ ጓድ ስታሊን «ርእዮተ-ዓለማዊ ውዥንብር በፓርቲው
ሕይወት ውስጥ ሲሰፍን የክበቦች አማተራዊነትና ጠባብ አመለካከት
ፓርቲውን ከላይ እስከታች ይቦረቡረዋል» ባለበት ወቅት ሩሲያ አቀፍ
የሆነ ሕቡዕ ጋዜጣ ማዘጋጀቱ ዓይነተኛው የሩሲያ አብዮታውያን ማርክ
ሲስቶች ተግባር ነበር ። በእንደዚህ ያለ ጋዜጣ ብቻ ነው የተበታተኑ
ማርክሲስት ድርጅቶችን ሊያገናኝና እውነተኛው ፓርቲ እንዲፈጠር
ጥርጊያ መንገድ የሚከፍተው ።

ይሁን እንጂ በዛራዊት ሩሲያ ውስጥ ከፖሊሶች አረመኔአዊ ድርጊት
በመሸሸግ ጋዜጣዎችን ማተም የሚቻል አልነበረምና በአንድና በሁለት
ወር ውስጥ አሳዶ በመያዝ ሕትመቱን ሊገቱ በቁ ። ስለዚህም ሌኒን ጋዜ
ጣው ከሩሲያ ውጪ እንዲታተም በመወሰኑ በጣም ስስ ነገር ግን ቶሎ
በማይቀደዱ ወረቀቶች እየታተሙ በሚስጥር ወደ ሩሲያ እንዲሰርጉ ተደ
ረገ ። ጥቂቶቹም የኢስክራ እትሞች በሩሲያ ውስጥ በሚስጥራዊ የማተሚ
ያ ሥፍራዎች በባኩ ፣ በሺኔቭ ፣ በሳይቤሪያ እንደገና ይታተሙ ነበር ።

በ1900 ዓ.ም. በልግ ወራት በሩሲያ አቀፍ ደረጃ ፖለቲካዊ ጋዜጣ
ማውጣት እንዲቻል ውጪ አገር ካሉት «የሠራተኞች ነጻ አውጪ»
ቡድን ጋር አስፈላጊውን ዝግጅት ለማሟላት ሌኒን ከሀገር ወጣ ። ወደ
ውጪ አገር ከመሄዱም በፊት ገና ከግዞት ላይ ሳለ በጥልቀት የተለመ
ውን በተግባር ለማዋል ወዲያው ከግዞት እንደተመለሰ በኡፋ ፣ ፐስኮቭ ፣
በሞስኮና በቅዱስ ፒተርስበርግ በርካታ ስብሰባዎችን በማካሄድ በየአካ

ባቢው ከፖለቲካዊ ጓዶች ጋር የምስጢራዊ አጻጻፍ ፣ ደብዳቤዎች የሚደርሱበትን የአድራሻ ኰዶች አጠናቅሮ ስለወደፊቱ የትግል ንድፍ ተወያይቶ አስፈላጊውን ዝግጅት አሟልቶ ነበር ።

የዛሩ አገዛዝ እጅግ አደገኛ ጠላት በሌኒን ላይ አሰማርቶ ነበር ። የአክሀራና የዛረስት ሩሲያ የፖለቲካዊ ፖሊሲ መምሪያ ጉዳዮች ሹም የነበረ ዙባቶቭ በሚያስተማምን መረጃ «በአሁኑ አብዮት ውስጥ ከኡሊያኖቭ (ሌኒን) የሚበልጥ ማንም የለም» በማለት የሌኒንን መገደል ከሁሉም በላይ አስፈላጊ እንደሆነ አስረዳ ።

በውጪ አገር ሌኒን ተልእኰውን ለማጠናቀቅ ከ «ሠራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን አባላት ማለትም ከፕሌክሃኖቭ ከአክሴልሮድና ከቪ— ዛሶሊች ጋር በመረዳዳት ኢስክራን ለማተም ተዘጋጀ ። የሕትመቱ ንድፍ ከመጀመሪያ እስከመጨረሻ በሌኒን የተሠራ ነበር ።

በ1900 ዓ.ም. በታህሣሥ ወር ውስጥ የመጀመሪያዋ የኢስክራ እትም ከሩሲያ ውጪ ልትታይ ቻለች ። ርእሱን የያዘው ገጽ «ፍንጣቂ እሳት ቋያ ታስነሳለች» በሚለው ጥቅስ በመንደርደር ይጀምራል ። እነዚህ ቃላት ታህሳሳውያን (Decemberists) በግዞት ላይ በነበሩበት ወቅት ገጣሚው ፑሽኪን ለላከላቸው ሰላምታ ከመለሱት መልስ የተወሰዱ ነበሩ ።

በርግጥም በሌኒን የተጀመረው ፍንጣቂ እሳት (ኢስክራ) የማያቋርጥ አብዮታዊ ቋያ በማቀጣጠሉ የዛሩን ዘውዳዊ አገዛዝ ከነግሳንግሱ ቡርዧውንም አዳምሮ ወደ አመድ ለውጧቸዋል ።

## አጭር ድርሞ

ማርክሳዊ የሶሻል ዲሞክራቲክ የሠራተኞች ፓርቲ በሩሲያ ውስጥ የተገነባው ከናሮዳዊነት ፣ ከተሳሳተውና ለአብዮታዊ ሁኔታ ጐጂ ከሆነው አመለካከታቸው ጋር መራራ ትግል በማድረግ ነበር ።

ለናሮድኒካውያን አስተሳሰብ ርእዮተ-ዓለማዊ ሽንፈት በማስከተል ብቻ ነው በሩሲያ ውስጥ ማርክሳዊ የሰራተኞች ፓርቲ ለመፍጠር ጥርጊያ መንገድ መክፈት የሚቻለው ። በሰማኒያዎቹ ዓመታት በናሮዳዊነት ላይ ዓይነተኛ ምት የሰጣቸው ፕሌክሀኖቭና የርሱ « የሰራተኞች ነጻ አውጪ » ቡድን ነበሩ ።

በዘጠናዎቹ ዓመታት ለናሮዳውያን ርእዮተ-ዓለማዊ ሽንፈት ግፊትና የማከተሚያ ምት በመስጠት ሌኒን ደመደመው ።

«የሰራተኞች ነጻ አውጪ» ቡድን በ1883 ተመሰረተ ። ማርክሲዝም በሩሲያ ውስጥ እንዲሰራጭ ታላቅ አስተዋጽኦ አበረከተ ። ለሶሻል-ዲሞክራሲ ንድፈ-ሀሳባዊ መሰረት ጣለ ፤ እንዲሁም በሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ግንኙነቶችን ለመመሥረት የመጀመሪያ እርምጃ ወሰደ ።



በሩሲያ ካፒታሊዝም ከማደጉ ጋር የኢንዱስትሪ ወዛደሮችም ቁጥር እየጨመረ ሄደ ። በሰማኒያዎቹ አመታት አጋማሽ ላይ ሠራተኞች ድርጅታዊ የትግል ፈለግ ተላመዱና በተደራጀ የሥራ ማቆም አድማ መልክ የኅብረት እርምጃ ወሰዱ ። ይሁን እንጂ ማርክሳዊ ክበቦችና ቡድኖች የፕሮፓጋንዳ ሥራዎችን ከማካሄድ በቀር በሠራተኛው መደብ መሀከል ቅስቀሳን የማድረጉን አስፈላጊነት አልተገነዘቡም ነበር ። ስለሆነም እስከዚያ ድረስ አንዳችም ተግባራዊ ተሳትፎ ከሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ጋር አልነበራቸውም ፣ ሠራተኛውንም አልመሩትም ።

በ1895 ሌኒን የመሰረተው የቅዱስ ፔተርስበርግ የሠራተኞች ነጻ አውጪ የትግል ሊግ በሰፊው ሠራተኞች መሀከል ቅስቀሳ በመጀመርና የሥራ ማቆም አድማ በመምራት አዲስ ምዕራፍ ከፈተ ። በሠራተኞች መሀከል ቅስቀሳ ወደ ማድረጉ ሽግግር እንዲጠናቀቅና በሠራተኛ መደብ ንቅናቄም ውስጥ ማርክሲዝም እንዲዋሀድ አደረጉ ። የቅዱስ ፔተርስበርግ የሠራተኛ መደብ ነጻ አውጪ የትግል ሊግ በሩሲያ ውስጥ ለአብዮታዊ የወዝአደሮች ፓርቲ የመጀመሪያ ደረጃ እርምጃ ነበር ። የቅዱስ ፔተርስበርግ የሰራተኛ መደብ ሊግ መመስረት ማርክሲስት ድርጅቶች በመላው ኢንዱስትሪያዊ ማዕከሎች ፣ በዳር አገሮች እንዲፈጠሩ አስችሏል ።

በ1898 የሩ.ሶ.ዲ.ሠ.ፓ. ስብሰባ ምንም እንኳን የመጀመሪያ ቢሆንም ማርክሲስት ሶሻል ዲሞክራቲክ ድርጅቶችን ለማስተባበር ጠቃሚ ድርሻ ቢያበረክትም ቅሉ የተካሄደው ስብሰባ ገና ፓርቲ ለመፍጠር አልበቃም ነበር ። እንዲያውም አንዳችም የፓርቲ ፕሮግራም ወይም የፓርቲ ሕግጋት አልነበሩም ። ከዚህም አልፎ አንድ የአመራር ማዕከል ባለመኖሩ በተበታተኑ ማርክሳዊ ክበቦችና ቡድኖች መሀከል አንዳችም ግንኙነት አልነበረም።

የተበታተኑትን ማርክሳዊ ድርጅቶች ወደ አንድ ብቸኛ ፓርቲ ለማዋሀድና ለማገናኘት እንዲቻል ሌኒን ኢስክራን ለማዘጋጀት ያቀደውን ንድፍ ተግባራዊ በማድረግ በመላው ሩሲያ የመጀመሪያውን አብዮታዊ የማርክሲስት ጋዜጣ አሰራጨ ።

አንድ ብቸኛ የሠራተኛው መደብ የፖለቲካ ፓርቲ እንዳይፈጠር በዚያን ወቅት ታላቅ ተቃውሞ ያራምዱ የነበሩት «ኢኮኖሚስቶች» እንደዚህ ያለ ፓርቲ አስፈላጊነቱን በመካድ ይቃወሙ ነበር ። እንዲያውም የተበታተኑ ቡድኖች እንዳይዋሀዱና አማተራዊ የአሰራር ዘዴዎች እንዲሰፍኑ ከፍተኛ ጥረት አድርገዋል ። በነርሱና በተግባራቸው ላይ ነበር በሌኒን የተደራጀው የኢስክራ ጋዜጣ የአላማ ቀስቱን የደገነው ።

የመጀመሪያው የኢስክራ እትም ገጽታ (1900—01) ወደ አዲስ ወቅት የተደረገውን ሽግግር አበሰረ ። ከተበታተኑ ቡድኖችና ክበቦች ወደ ብቸኛ የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቲክ የሰራተኞች ፓርቲ እውነተኛ ሕይወት የሚከትበት ወቅት ነውና ።

## ምዕራፍ ሁለት

# የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቲክ የሠራተኛ ፓርቲ መፈጠር ፣ በፓርቲ ውስጥ የቦልሼቪክና የሜንሼቪክ ቡድኖች መታየት

### 1. ከ1901-1904 ዓ.ም. በሩሲያ ውስጥ አብዮታዊ ንቅናቄ መነሳሳት

አሥራ ዘጠነኛው ምእተ ፣ ዓመት መጨረሻ በአውሮፓ ውስጥ ኢንዱስትሪያዊ ቀውስ የ ሰፈነበት በመሆኑ ይታወሳል ። ይህ የኢንዱስትሪያዊ ቀውስ ማእበል በዚያው በአውሮፓ ብቻ ተወስኖ አልቀረም ። ወዲያው ሞገዱ ዛሪስት ሩሲያን አጥለቀለቀ ። ከ1900-03 ባሉት ዓመታት ብቻ ከ 3.000 የሚበልጡ ትላልቅና ትናንሽ ኢንዱስትሪዎች ሲዘጉ ፤ ከ100,000 በላይ የሚሆኑ ሠራተኞች ከየፋብሪካው በመባረር በየመንገዱ ተጣሉ ። በፋብሪካው ውስጥ ለጊዜው የቀሩትም ቢሆኑ የሚከፈላቸው ክፍያ እጅግ ቀነሰ ። ቀደም ብለው የተደረጉት ድርድሮች በአሁኑ ወቅት ዋጋ አጡ ።

ኢንዱስትሪያዊ ቀውስና ሥራ አጥነት የሠራተኛውን መደብ ንቅናቂ ሊገታው ወይም ሊያደክመው ከቶም አልቻለም ። በተለይም በከተሞች ውስጥ የሠራተኞች አብዮታዊ ንቅናቂ እያደገ መምጣቱ ጉልህ እውነት ነበር ። ሠራተኞች ለምጣኔ-ሀብት ከሚያደርጉት ትግል ወደ ፖለቲካው የሥራ ማቆም አድማዎች በመሸጋገር ለሕዝባዊ አርነት የሚታገሉ መፈክሮችን አንግበው ። «የዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ይውደም!» የሚሉ መፈክሮችን በመያዝ ፖለቲካዊ ጥያቄዎችን በማንሳት ታላላቅ ሰላማዊ ሰልፎችን አካሄዱ ።

በ1909 ዓ.ም. በቅዱስ ፒተርስበርግ በአቡኮሆቭ ውስጥ ለሚይዶይ በተደረገው የሥራ ማቆም አድማ ምክንያት በሠራተኞችና በወታደሮች መሀል ከፍተኛ የደም መፋሰስ ደረሰ ። ሠራተኞቹ የታጠቀውን ወታደራዊ ሀይል በያዙት ድንጋይና የብረት ዘንጎች ብቻ ተቋቋሙት ። ይሁን እንጂ አይዘልቁት ነገር ሆነና ያ በወዝ አደራዊ ሞራል የተሞላው መቋቋም በአረመኔያዊ ፍጅት ተፈታ ። ኢ-ሰብአዊ የበቀል እርምጃ ደርቶ ከ800 ሠራተኞች በላይ በእሥር ቤት ታጐሩ ። ከፊሉም ፣ በዛሩ አረመኔያዊ ጥይት ተደብድበው በፋብሪካ ደፎች ወደቁ ። ታላቁ የ«አቦክሆቭ ሽንፈት» ላይንሰራራ ያከተመ አልነበረም ። ይሁን እንጂ በሩሲያ ሰራተኞች ሕይወት ውስጥ የአመጽ ሲቃ ፣ የትዝታ ንዳድ አሳደረ ። ሠራተኞች ከመቼውም ጊዜ ይልቅ በመሀከላቸው የመተሳሰብና የመደጋገፍ ፍላጐት እያደገ መጣ ።

በመጋቢት ወር 1902 ዓ.ም. በባቱም በሚገኙ የሶሻል ዲሞክራቲክ ኰሚቴ የተደራጁ ትልቅ የሥራ ማቆም አድማና ሠላማዊ ሰልፎች ተደረጉ ። ይህ አብዮታዊ ሞገድ የትራንስካውካሲያን ሰራተኞችና ገበሬዎች አነሳሳ ።



በ1902 ዓ.ም. በሮስቶቭ ኦን ደን ሌላ የሥራ ማቆም አድማ ተደረገ ። የአመጹው ችቦ በምድር ባቡር ሠራተኞች ይቀጣጠል እንጂ የብዙ ፋብሪካ ሠራተኞች ወዲያውኑ ተባበሩት ። የአለፉት አመጹዎች ሠራተኞችን አስተምረዋልና በ30,000 የሚገመቱ ሠራተኞች ከከተማዋ ክልል ውጭ በመውጣት በተከታታይ ስብሰባ ያካሂዱ ነበር ። በነዚህ ስብሰባዎች ሶሻል ዲሞክራቲክ ክልል ውጭ በመውጣት በተከታታይ ስብሰባ ያካሂዱ ነበር ። በርግጥም የሠራተኛው ቁጥር እጅግ ብዙ በመሆኑ የዛሩ ፖሊሶችና ነጭ ለባሾች ስብሰባውን ሊበትኑት አልቻሉም ። ሠራተኞች በተገደሉ ማግሥት ወዛደሮች በታላላቅ አጀቦች የጓዶቻቸውን የቀብር ሥነ-ሥርዓት ሲያከብሩ ፣ የዛሩ መንግስት በአካባቢው ከሚገኙ ከተሞች የታጠቁ ኃይሎችን አሰባሰቦ በማምጣት ብቻ ነበር ይህን የወዝአደሮች የሥራ ማቆም አድማ ለመምታት የቻለው ። የሮስቶቭ ሠራተኞች ትግል የተመራው በሩ.ሶ.ዲ.ሠ.ፓ. የደን ኰሚቴ ነበር ።

በ1903 ዓ.ም፡ የፈነዱት የሥራ ማቆም አድማዎች ሞገዳዊ መጠናቸው ትልቅ ነበር ። በዚያው ዓመት በደቡብ የተደረገው የሰፊው ሠራተኛ ፖለቲካዊ የሥራ ማቆም አድማ በትራንስካውካሲያ ማለትም በባኩ ፣ በቲፍሊስ ፣ በባቱምና በዩክሬኒያን ታላላቅ ከተሞች ማለትም በኦዲስ ፣ በኪይቭ ፤ በኤሌካቶሪኖስለቭ ተዳረሰ ። የተደረጉት የሥራ ማቆም አድማዎች ከጊዜ ወደጊዜ የማይፈቱና በሚገባ የተደራጁ እየሆኑ መጡ ። ሠራተኛው መደብ በአለፉት ትግሎቹ እንደወሰደው እርምጃ ሳይሆን ፖለቲካዊ ትግላቸው በሁሉም አካባቢ በሶሻል ዲሞክራቲክ ኰሚቴዎች ነበሩ ።

የሩሲያ ሠራተኞች የጸረ-ዛሪስት አገዛዝ ትግሉን አጋጋሉት ።

ትግላቸው በገበሬዎች ላይ ከፍተኛ ግፊት አሳደረና በ1902 ጸደይና በጋ ወራት በኡክሬኒያን በፖልታቫና በካሀርኮቭ ጠቅላይ ግዛትና በቮልጋ አካባቢ የገበሬዎች ንቅናቄ ፈነዳ ። ገበሬዎች የመሬት ከበርቴዎችን ግዙፍ የመኖሪያ ቤቶች በእሳት አጋዩት ፣ መሬቶቻቸውን ነጠቁ ፣ የተጠሉትን (ዘምስኪይናቻልኒካስች) የገጠር ሹማምንቶችና የመሬት ከበርቴዎችን ገደሏቸው ። ይህንን የገበሬዎች አመጽ ለማብረድ በታኝ ጓዶች ወደአካባቢው ተላኩ ። እጅግ በርካታ ገበሬዎች ተገደሉ ፣ በመቶ የሚቆጠሩት ታሰሩ ። መሪዎቻቸውና አደራጆቻቸው ተለቅመው ተጋዙ ። ዳሩ ግን አብዮትን በሀይል መግታት አይቻልምና የአርሶ አደሮች ንቅናቄ ማደጉን ቀጠለ ።

እንደ እውነቱ ከሆነ የወዝአደሮችና የገበሬዎች አመጸ በየቦታው መነሳሳት በሩሲያ ውስጥ አብዮታዊ ሁኔታው መብሰሉን የሚጠቁም ነበር ።

የሠራተኛው አብዮታዊ ትግል በአሳደረው ከፍተኛ ግፊት የተነሳ ተማሪዎች የዛሩን አገዛዝ በመቃወም የሚያደርጉት እንቅስቃሴ እየተጋጋለ መጣ ። በአካሄዱአቸው ሰላማዊ ሰልፎችና የሥራ ማቆም አድማዎች መቀናጀት ምክንያት የዛሩ መንግስት ዩኒቨርሲቲዎችን ዘጋ ፣ በመቶ የሚ

ቆጠሩ ተማሪዎችን አጋብሶ እስር ቤት አመቀ ፣ በመጨረሻም የሚያስቸ
ግሩ ተማሪዎችን እንደተራ ወታደር በሠራዊቱ ውስጥ መልምሎ የማስገ
ባት ሀሳብ ወጠነ ። ለዚህም መልስ የዩኒቨርሲቲ ተማሪዎች በ1901-02
የክረምት ወራት አጠቃላይ የትምህርት ማቆም አድማ አዘጋጁ ፤ በአድማ
ውም ላይ 30,000 ተማሪዎች ተሳትፈው ነበር ።

የወዝአደሮችና የገበሬዎች አብዮታዊ ንቅናቄ በተለይም በተማሪ
ዎች ላይ የደረሰው መሳደድ ለዘብተኛ ቡርዧዎችንና ለዘብተኛ የመሬት
ከበርቴዎችን ማለትም ዜምስትቦስ በመባል የሚታወሱትን የዛሩ መንግ
ሥት በተማሪ ልጆቻቸው ላይ የሚያደርሰውን «ከልክ ያለፈ» ድርጊት
«በመቃወም» ድምጻቸውን ለማሰማት ተደራጁ ።

የዚምስቶቭ ለዘብተኞች በዚምስቶቭ ቦርዶች ውስጥ ጠንካራ ድጋፍ
ነበራቸው ። እነዚህ የዜምስቶቭ ቦርዶች የገጠር ሕዝቦችን የአካባቢ ጉዳ
ዮች ብቻ የሚያከናውኑ መንግስታዊ አካሎች ናቸው ። (ለመንገድ ሥራ
ዎች ለሆስፒታልና ትምህርት ቤቶች) በዚምስቶቭ ቦርድ ውስጥ የመሬት
ከበርቴዎች ዓይነተኛ ሚና ተጫውተዋል ፤ በቅርበት ከለዘብተኛው ቡር
ዧው ጋር ተባብረዋል ይበልጥም ተዋህደው ነበር ። በገባርነት ላይ የተ
መሠረቱትን ዘዴዎች በመተውና አትራፊነቱን በመገንዘብ የካፒታሊስት
የእርሻ ዘዴዎች በሁዳዶቻቸው ላይ ጀምረዋል ። በርግጥ ሁለቱም ለዘብ
ተኛ ቡድኖች የዛሩን አገዛዝ ይደግፋሉ፤ይሁን እንጂ አገዛዝ «መረን የለቀቀ
እርምጃው» አብዮታዊ ንቅናቄን ያስከትላል በሚል ስጋት የተነሳ ይቃወ
ሙ ። የዛሩን «መረን የለቀቀ እርምጃ» ቢፈሩም ቅሉ አብዮትን ደግሞ
የበለጠ ይፈራሉ ። በመጀመሪያ ፣ የዛሩ አገዛዝ መረን ከለቀቀው እርምጃ
ው እንዲቆጠብ ይህን መረን የለቀቀ እርምጃ ለመቃወም አብዛኛዎቹ
ሁለት ዓላማዎችን ያራምዱ ነበር ። በመጀመሪያ ፣ የዛሩን «መረን የለቀቀ
እርምጃ» ቢፈሩም ቅሉ ፣ አብዮቱን ደግሞ የበለጠ ይፈራሉ ። ሁለተኛ ፤
ከዛሩ አገዛዝ ጋር «ፍጹም አለመርካታቸውን» በማስከ ሽፍነው የሕዝቡን
እምነት ለማግኘትና ቢቻል ሁሉንም አሊያም ከፊሉን በቁጥጥራቸው
ሥር አድርገው አብዮቱን ለማገድ ነው ።

እንደ እውነቱ ከሆነ የዚምስቶቭ ለዘብተኛ ንቅናቄ ስለ ዛሩ አገዛዝ
መናር አንዳችም አስደንጋጭ እርምጃ አልወሰደም ። ይሁን እንጂ ሁሉም
የዛሩ «ዘላለማዊ» ምሰሶዎች ጤነኛ አለመሆናቸውን ለማስረዳት አገልግ
ሏል ።

በ1902 ዓ.ም. የዜመስቶቭ ለዘብተኛ ንቅናቄ ወደ ቡርዧ «ነጻ
አውጪ» ቡድን ምሥረታ አመራ ። ይህ ደግሞ በሩሲያ ውስጥ የቡርዧው
ዋነኛ ፓርቲ ለሆነው ሕገ መንግስታዊ ዲሞክራቲክ ፓርቲ ጽንስ ሆነ ።

የሠራተኞችና የአርሶ አደሮች ንቅናቄ ከተማዋን በሚያስፈራ ማዕ
በል እናወጣት ። የዛሩ አገዛዝ ይህንን አብዮታዊ ማዕበል ለማገድ ያልፈነ



ቀለው ድንጋይ ያልበጠሰው ቅጠል አልነበረውም ። ሁሉንም በመደጋ
ገምና ሀይል በመጨመር ተጠቅሟል ። ሠራተኞችና ገበሬዎች ለሚወስዱ
ቸው እርምጃዎች ሁሉ ምላሹ የጥይት ናዳ ሲሆን እስር ቤቶችና የግዞት
ሥፍራዎችም እጅግ በርካታ በሆኑ ታጋዮች ተጣበው ይታዩ ነበር ።

ገዥዎች ሥልጣናቸውን ለማሰንበት ሁሉንም ዘዴዎች ይጠቀማሉና
ከማሰር ፣ ከመግደሉ ዘዴ ለየት ባለ ሁኔታ ሠራተኞችን ከአብዮታዊ ተሳ
ትፎአቸው፣ከአመጽ ግለታቸው ለመመለስና አቅጣጫ ቸውን ለማስለወጥ
ከሁኔታው ጋር «የሚጣጣሙ» ዘዴዎችን ከዚሁ ጋር ተጠቅመው ነበር ።
በፖሊሶችና በገዳዮች ቁጥጥር ሥር የሆነ የይስሙላ ድርጅት ማደራጀት
ጀመሩ ። የገዳዮች እውቅ ጀኔራል የነበረው ዙባቶቭ ይህንን ጠቃሚ ነው
ተብሎ የተደከመበትን በፖሊሶች ቁጥጥር ሥር ያለ የሠራተኞች ድርጅት
መሰረተ ። ከዚህ በኋላ እነዚህ ድርጅቶች የ «ፖሊስ ሶሻሊዝም» ወይም
በዙባቶቭ ድርጅት የሚመስሉ ነበሩ ። በአክራና ሰላዮቹ አማካይነት የዛ
ሩ መንግስት ሠራተኛውን በሀሰት ለማሳመን «የሠራተኛውን የምጣኔ-
ሀብት ፍላጎት እንዲሟላ ለማድረግ ነው የዛሩ መንግስት ከናንተ ጋር
የመደበን» በማለት ሠራተኞችን ለማሳመን ከፍተኛ ጥረት አድርጐ
ነበር ። «እራሱ የዛሩ መንግስት ከሰራተኛው መደብ ጐን ከቆመ ለምን
በፖለቲካው ውስጥ እጃችንን እንነከራለን ? ለምን አብዮት እናካሂዳለን?»
በማለት ይሰብኩ ነበር ። የዙባቶቭ ድርጅቶች በብዙ ከተሞች ተቋቋሙ ።
በነዚህ ድርጅቶች ሞዴል በሩሲያ የቅዱስ ፔተርስበርግ የፋብሪካ ሠራ
ተኞች ስብሰባ በመባል የታወቀው ድርጅት በ1904 በቄስ ጋፖን ተመ
ሠረተ ።

ይሁን እንጂ ዛሪስት አክራሀና በሠራተኞች ማኅበር ላይ ቁጥጥር
ለማግኘት ያደረገው ከፍተኛ ጥረት አልሰመረም ። የዛሩ መንግስት ከዚህ
ዓይነት እርምጃው የሠራተኛውን መደብ ንቅናቄ ሊገታው እንደማይችል
አረጋገጠ ። የተነሳሳው የሠራተኛው መደብ ንቅናቄ በድርጅቱ ላይ ያለ
ውን የፖሊስ ቁጥጥር ከመንገዱ ላይ እየመነጠረ አጸዳው ።

## 2. ማርክሳዊ ፓርቲ ለመገንባት ሌኒን ያወጣው ፕላን «የኢኰኖሚስቶች» አድርባይነት ፤ ለሌኒን ፕላን ኢስክራ ያደረገው ትግል

### «ምን መደረግ አለበት ?» የተሰኘው የሌኒን መጽሐፍ ፤ የማርክሳዊ ፓርቲ ርዕዮተ ዓለማዊ መሰረት

በ1898 ዓ.ም. በሩሲያ ውስጥ የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ የመጀ
መሪያ ስብሰባ ላይ ፓርቲ መፈጠሩ ቢገለጽም እውነተኛው ፓርቲ ገና
አልተመሰረተም ። ይህ የመጀመሪያው ስብሰባ አንዳችም የፓርቲ መርሀ-

ግብር ወይም የፓርቲ ደንቦች (ሕጐች) አልነበሩትም ። በመጀመሪያው ስብሰባ ላይ የተመረጡት የማዕከላዊ ኰሚቴ አባሎች እንዳሉ ታሰሩ ። በምትካቸውም ሌሎች አልተተኩም ። ከመጀመሪያው ስብሰባ በኋላ የርዕዮተ-ዓለም ውኽንብርና ድርጅታዊ አንድነት በፓርቲው ውስጥ ከመቼውም ጊዜ በላይ ፀንቶ ነበር ።

ምንም እንኳ 1884-94 ያሉት ዓመታት በናሮዲዝም ላይ ድል የተገኘበትና ለሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ መፈጠር ርዕዮተ-ዓለማዊ ዝግጅት የተደረገበት ወቅት ቢሆንም ከ1894-98 ያሉት ሁለት ዓመታት የተበታተኑ ማርክሲስት ድርጅቶችን ወደ ሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ለማዋሀድ የተደረገው ጥረት ፍሬ አልባ የሆነበት ወቅት ነበር ። ከ1898 ዓ.ም. ወዲያውኑ ተከታትለው ባሉት ዓመታት በፓርቲው ውስጥ ርዕዮተ-ዓለማዊና ድርጅታዊ ውኽንብር የሰፈነበት ሆነ ። ማርክሲስቶች በናሮዲዝም ላይ የተጐናጸፉት ድልና የሠራተኞች አብዮታዊ ተግባር የማርክሲስቶችን እውነተኞች በሚገባ በማረጋገጡ ማርክሲዝም አብዮታዊ ወጣቶችን በዙሪያው ለማሰባሰብ በቃ ። በውጤቱም ማርክሲዝም የዘወትር ተግባር በመሆን በንድፈ-ሀሳባዊ ግንዛቤአቸው ዝቅ ብሎና ድርጅታዊ ልምድ በሌላቸው በ «ሕጋዊ ማርክሲስቶች» አድርባይ ጽሁፎች ሕትመቶች ሲሞሉ ፤ የተድበሰበሰውንና አብዛኛው ጐን ትክክል ያልሆነውን የማርክሲዝም አስተሳሰብ በርካታ አብዮታዊ ወጣት ምሁራን የማርክሲስት ድርጅቶችን አጣበቡ ። «በሕጋዊ ማርክሲስቶች» አድርባይ አዝማሚያዎች መመረዝ ፤ በርዕዮተ-ዓለማዊ ውኽንብር ፣ በፖለቲካዊ ውኽቀትና በድርጅታዊ ቀውሶች መወረር የተነሳ የማርክሲስት ድርጅቶች የርዕዮተ-ዓለምና የፖለቲካዊ ደረጃቸው እንዲያቆለቁል ተደረገ ።

የተነሳሳው የሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ማዕበልና በገሀድ እንደሚታየው ለአብዮት ፍንዳታ መቃረብ አብዮቱን ለመምራት ብቃት ያለው ፣ የተዋሀደና የተመአከለ የሠራተኛው መደብ ፓርቲ ከፍተኛ የወቅቱ ጥያቄ ነበር ። ይሁን እንጂ በእንደዚህ ያለ ከፍተኛ ወቅት የአካባቢ የፓርቲ ድርጅቶች ፣ የአካባቢ ኰሚቴዎች ፣ ሕዋሶች ፣ የጥናት ክበቦች ገና እንደዚህ ባለ ዝቅተኛ ደረጃ ላይ ቢገኙም ድርጅታዊ አንድነት ጠፍቶና ርዕዮተ-ዓለማዊ ልዩነት ተፈጥሮ ባለበት ሁኔታ የተፈለገውን ዓይነት ፓርቲ ለመፍጠር የሚደረገው ጥረት እጅግ አስቸጋሪ ነበር ።

አብዮታዊውን ንቅናቄ የሚመራ አብዮታዊ ፓርቲ ለመፍጠር የሚደረገው ትግል በጸረ-አብዮት ሀይላት በዝምታ የሚታለፍ አይሆንምና የዛሩ መንግስት አብዮታዊ ንቅናቄዎችን «ለማጥፋት» ኢ-ሰብአዊ ጭፍጨፋ አካሂዷል ። ይሁን እንጂ የተፈለገውን ፓርቲ የማነጹ ተግባር በዛሩ አረመኔያዊ ፍጅት ሥር ማደራጀት የማስችገሩ እውነትነት ላይ ብቻ የሚያርፍ አይደለም ። ሌላው ትልቁ ችግር በርካታ የሆኑ የአካባቢ ኰሚቴዎችና አባሎቻቸው በፓርቲው ሕይወት ውስጥ ድርጅታዊና ርእዮተ-ዓለማዊ



መነጣጠል መኖሩ የሚያስከትለውን ካለማጤናቸው የተነሳ የአካባቢያቸውን ጥቃቅን ተግባራዊ እንቅስቃሴዎች ከመሥራት በቀር አንዳችም ነገር ከምንም ጋር ስለማይሰሩ በድርጅቱ ውስጥ የተከሰተውን መነጣጠልና ርዕዮተ-ዓለማዊ ውኽንብር ተላምደውታል ። አንድነት በሌለውና ባልተመአከለ ፓርቲ ያለአንዳች ችግር ዓላማቸውን ከግብ ማድረስ እንደሚችሉ አምነው ተቀብለዋል ፤ ይህ ሌላው ትልቁ ችግር ነበር ።

የተመአከለ ፓርቲን ለመፍጠር ካስፈለገ የአካባቢ አካሎችን ኋላቀርነትና ጠባብ አመለካከት ማስወገድ የግድ ያስፈልግ ነበር ።

ይሁን እንጂ ይህ ብቻም በቂ አይሆንም ። በርካታ ሕዝብ አቅፈው የራሳቸውን እትሞች የሚያወጡ ቡድኖች በፓርቲው ውስጥ ይገኙ ነበር ። እነዚህም በሩሲያ ውስጥ ራብቺያ ማይስል (የሠራተኞች አስተሳሰብ) ና ከሩሲያ ውጪ ደግሞ ራብቺያ ዲሎ (የሠራተኞች ዓላማ) የተባሉት ሲሆኑ በየእትሞቻቸውም ምንም እንኳ በመደጋገም የዛሩን ጉዳዮች በማንሳት ድምጻቸውን ከፍ አድርገው ቢጮሁም ፣ ድርጅታዊ አንድነት እንደሌለና በፓርቲው ውስጥ ርዕዮተ-ዓለማዊ ውኽንብር እንደ ሰፈነ ቢናገሩም ፤ የተወከለ የሰራተኛው መደብ ፖለቲካ ፓርቲ እቅድ ማውጣቱ የማያስፈልግና ሰው ሰራሽ መሆኑን ንድፈ-ሀሳባዊ መሠረት በመስጠት ለማሳየት ሞክረዋል ።

እነዚህ «ኢኰኖሚስቶችና» የነርሱ ተከታዮች ነበሩ ።

አንድነት ያለው የወዝአደሩ የፖለቲካ ፓርቲ ከመፈጠሩ በፊት «ኢኰኖሚስቶች» በሚገባ መንበርከክ ነበረባቸው ።

ለዚህ ተግባርና የሰራተኛውን መደብ ፓርቲ ለመገንባት ነበር ሌኒን ይህንን የገለጸው ።

አንድነት ያለው የሰራተኛውን መደብ ፓርቲ ለመገንባት እንዴት ይጀመር የሚለው ጥያቄ የተለያዩ አስተሳሰቦችን ፈጥሮ ነበር ። አንዳንዶች የፓርቲው ግንባታ የአካባቢ ድርጅቶችን ሊያዋህድና ፓርቲን ሊፈጥር የሚያስችለውን ሁለተኛውን የፓርቲ ኰንግረስ በመጥራት መጀመር ይገባናል አሉ ። ሌኒን ግን ይህን አስተሳሰብ ተቃወመ ። ስብሰባውን ከመጥራታችን በፊት የፓርቲውን ዓላማና ግቦች በግልጽ ማሳወቁ ምን ዓይነት ፓርቲ እንደሚያስፈልግ ለማረጋገጥ ያስችላል ። «ከኢኰኖሚስቶች» ርዕዮተ-ዓለማዊ ግድበት ለማላቀቅ ፣ የፓርቲውን ዓላማና ግቦች አስመልክቶ ሁለት የተለያዩ አመለካከቶች መኖራቸው በታማኝነትና በእርግጠኝነት ለፓርቲው ለመግለጽ ያስፈልጋል ። «ኢኰኖሚስቶች» በአብዮታዊ ሶሻል ዲሞክራቶች ዘመቻ እንዳደረጉት ሁሉ አብዮታዊ ሶሻል ዲሞክራሲም በራሳቸው አመለካከት ሰፊ ዘመቻ በእትሞቻቸው ላይ ማካሄድ አለባቸው ፣ ይህም የአካባቢ ድርጅቶች በነዚህ በሁለቱ አዝማሚያዎች መሀከል እንዲጉን ተገንዝበው የመምረጥ እድል ለመስጠት እጅግ

ጠቃሚ ይሆናል በማለት ሌኒን አስገነዘበ ። ይህ የማይታለፍ ቀደምትና አዘጋጅ ተግባር ከተከናወነ በኋላ ብቻ ነበር የፓርቲውን ኰንግረስ መጥራት የሚቻለው ።

ሌኒን በግልጽ እንዳስቀመጠው «ከመዋሀዳችን በፊትና እንድንዋሀድም ከተፈለገ ከሁሉም በፊት በመስመር ልዩነቶቻችን ላይ ጠንካራና ወሳኝ አቋም መውሰድ አለብን»

(ሌኒን ምርጥ ስራዎች የእንግሊዝኛ ዕትም ሞስኮ 1947 ቅጽ 1 ገጽ 162)

ሌኒን በዚህ ሁኔታ የሠራተኛውን መደብ የፖለቲካ ፓርቲ ለማነጽ በሩሲያ አቀፍ ደረጃ የአብዮታዊ ሶሻል ዲሞክራሲን አመለካከት የሚያራምድ ቅን ፖለቲካዊ ጋዜጣ በማዘጋጀት ፕሮፓጋንዳና ቅስቀሳ ማካሄዱን በመደገፍ እንደዚህ ያለ ጋዜጣ መመስረት ፓርቲውን በማነጽ ተግባር ውስጥ የመጀመሪያ እርምጃ መሆኑን አመለከተ ።

ሌኒን «ከየት ይጀመር» በሚለው ታዋቂ ጽሁፉና በኋላም «ምን መደረግ አለበት?» በሚለው መጽሐፉ ተስፋፍቶ የተገለጸውን ለፓርቲው ግንባታ ተጨባጭ እቅድ ነደፈ ።

«በኛ አስተሳሰብ» ይላል ሌኒን በጽሁፉ፤«በኛ አስተሳሰብ የተግባሮቻችን መነሻ ነጥብ ፥ የተፈለገውን ድርጅት ለመፍጠር የወሰድነው የመጀመሪያ ተግባራዊ እርምጃ በመጨረሻም ይህንን ዓላማ የወሰድነው በመከተል ድርጅቶቻችንን ለማስፋት ያልተቆጠበ ጥረት ለማድረግ እንድንችል በሩሲያ አቀፍ ደረጃ ፖለቲካዊ ጋዜጣ ማቀም ይኖርብናል—ካለፊው ጋዜጣ ዘዴያዊ በሆነ መንገድ ሁሉን አቀፍ የሆነ ፕሮፖጋንዳና ቅስቀሳ ማካሄድ ፥ በአጠቃላይ የሶሻል ዲሞክራቶችን ዋነኛና ተዘውታሪ ተግባር የመመሪያ አንድነት ለመቅረጽ አይቻልም ። በተናጥላ ደግሞ የፖለቲካና የሶሻሊዝም ጥያቄ ፥ ስሜቶች በአብዛኛው የሕብረተሰብ ክፍሎች መሀከል ሰፍኖ እንዲታይ የጋዜጣው አጣዳፊ ተግባር ይሆናል»።

(ሌኒን ስብስብ ሥራዎች የራሽያ እትም ፣ ቅጽ 4 ገጽ 110)

ሌኒን ሲያሳስብ፦ እንደዚህ ያለ ጋዜጣ ርዕዮተ-ዓለማዊ አንድነት በፓርቲው ውስጥ እንዲፈጠር የሚያገለግል ብቻ ሳይሆን የአካባቢ አካሎችን በፓርቲው ሥር ለማሰባሰብም ጭምር ነው ። የጋዜጣው ወኪሎችና ጽሁፎች ዓይነተኛ ሥራ ፓርቲው የአካባቢ ድርጅቶችን በመወከልና በድርጅቶች ሊገነባ የሚችልበትን አውታር መሻት ነው ። ለዚህም ነው «ጋዜጣ ለፕሮፖጋንዳና ለቅስቀሳ ብቻ ሳይሆን ለማደራጀትም ጭምር ነው» በማለት ሌኒን የተናገረው ።

«ይህ የቀስቃሾች አውታር»ይላል ሌኒን በዚህ ጽሁፉ«የሚያገለግልመሣሪያ» በርግጥ መላውን አገር ለማቀፍ የሚያስችል ብቃት ያለውን የምንፈልገውን ድርጅታዊ መዋቅር ያዘጋጃል ፥ በሚበቃ ሁኔታ ሰፊና ፥ በርካታ ጐኖች ያሉት ጥብቅና የሰፋ የሥራ ክፍፍል እንዲኖር ያስችላል ። በተለያዩ ሁኔታዎች ፥ « አዝማሚያዎች » ና አጋጣሚዎች በቂ በሆነ ሁኔታ



መስመሩን በመያዝ የራሱን ሥራ ለማካሄድ እንዲጥርና በነገሩ እንዲሳተፍ ያበቀዋል ። መላው ሀይሉን በአንድ ቦታ አከማችቶ ፥ የጠላትን የተሳሳተ አቅጣጫ ገና መጠቀም ባልተቻለበትና መቼም ቢሆንና የትም ቢሆን በመጨረሻ ጠላቱን ለማንበርከክ በቂ በሆነ መንገድ ከሁኔታው ጋር በማመሳሰል ከፍተኛውን ሀይል ከያዘው ጠላት ጋር የፊት ለፊት ውጊያን ለማስወገድ ያስችለዋል ። (ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ ፣ 112)

ኢስክራም እንደዚህ ያለ ጋዜጣ መሆን ነበረባት ።

ኢስክራ በርግጥም በመላው ሩሲያ ለፓርቲው ርዕዮተ-ዓለማዊና ድርጅታዊ መጠናከር ጥርጊያ መንገድ በመክፈት የቀፈለገው ዓይነት ጋዜጣ ሆናል ።

የፓርቲውን መዋቅርና ቅንጅት በሚመለከት ረገድ ሌኒን ሁለት ፈርጆች መኖራቸውን አስገነዘበ ፦— ሀ—መላውን ጊዜአቸውን ለፓርቲው ሥራ የወሰኑ ፥ ንድፈ-ሃሳባዊ እውቀት ፥ ፖለቲካዊ ልምድ ፥ ድርጅታዊ ሥራንና የዛሩን ፖሊሲ የመዋጋት ጥበብ ያዳበሩ ፥ ራሳቸውን የመሸፈን ችሎታ አስፈላጊነት በሚገባ የተረዱ ፕሮፌሽናል አብዮተኞች-የመሪው ፓርቲ ሠራቂኞች—መደበኛ የካድሬዎች ከበብ ። ለ—የአካባቢ ድርጅቶች ሰፊ አውታሮችና በብዙ ሽህ የሚቆጠረውን የሰራተኛውን ሕዝብ ድጋፍ የተጐናጸፉ በርካታ የፓርቲ አባላት ያስፈልጋሉ ።

«እኔ የምለው» ይላል ሌኒን ሲጽፍ «1/ ለረጅም ጊዜ መቆየት የሚችል የመሪዎች ድርጅት ከሌለ ችግርን መቋቋም የሚችል አብዮታዊ ንቅናቄ ሊኖር አይችልም ። 2/ ይበልጥ ሰፊው ሕዝብ በግብታዊነት እየተሳተፈ በሄደ ቁጥር የዚህ ዓይነቱ ድርጅት አስፈላጊነት በጣም አንገብጋቢና ድርጅቱም በጣም ጠንካራ መሆን አለበት ።3/ እንደዚህ ያለው ድርጅት በይበልጥ መላውን ሕይወታቸውን ለአብዮታዊ ንቅናቄ የሰጡ ሕዝቦች እንዲኖሩት ያስፈልጋል ። 4/ በፈላጭ ቆራጭ መንግስት ውስጥ ሕይወታቸውን በሙሉ ለአብዮታዊ ንቅናቄ የሰጡና ፖለቲካዊ ፖሊሲዎችን በመቋቋም ፕሮፌሽናል ልምድ ያካበቱትን በድርጅታችን ውስጥ በአባልነት ይበልጥ መሰብሰብ ስንችል እንደዚህ ያለውን ጠንካራ ድርጅት ለማጥፋት ይበልጥ አድካሚና አስቸጋሪ ይሆናል ። 5/በዚህ ንቅናቄ ውስጥ የሚገቡና ተግባራዊ ተሳትፎ የሚያደርጉ የሠራተኛው መደብና የሌላው ሕብረተሰብ ክፍሎች ቁጥር እየበዛ ይሄዳል ነው ።»

(ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 456)

ስለሚገነባው ፓርቲ ባሕርያትና ከሠራተኛው መደብ ጋር የሚኖረውን ቀዛምዶ ፥ እንዲሁም ስለ ዓለማዊና ግቦቹ ሌኒን ሲገልጽ ፓርቲው የሠራተኛው መደብ ግንባር ቀደም ይሆናል ። የወዝአደሩን የመደብ ትግል የሚያስተባብርና የሚመራ የሠራተኛው መደብ ንቅናቄ መሪ ሀይል መሆን አለበት ። የፓርቲው ዘላቂ ግብ ካፒታሊዝምን አስወግዶ ሶሻሊዝምን መገ

ንባት ሲሆን ጊዜያዊ ዓላማው ደግሞ የዛሩን አገዛዝ በማውደም ዲሞክራሲያዊ ሥርዓትን ማስፈን ነበር ። ይሁን እንጂ የማይዘለለውና ለሚቀጥለው ዓላማ አዘጋጅ የሆነው የዛሩን አገዛዝ የማውደም ተግባር ሳይጠናቀቅ ካፒታሊዝምን ማስወገድ ፍጹም የሚቻል አይደለም ። ስለሆነም የፓርቲው ዓይነተኛ ተግባር በተወሰነ ሁኔታ ውስጥ ሰፊውን ሠራተኛ ሕዝብና መላውን ሕዝብ በማንሳሳት ፣ አብዮታዊውን እንቅስቃሴ ማሳደግና ወደ ሶሻሊዝም በሚደረገው ጉዞ ላይ በዋንኛ ደረጃ እስቸጋሪ የሆነውን እንቅፋት ማለትም የዛሩን አገዛዝ አሽቀንጥሮ መጣል ነበር ።

« ታሪክ » ይላል ሌኒን ሲጽፍ «አጣዳፊ ከሆነ ተግባር ጋር ገጥሞናል ፤ ይህም ከማንኛውም አገር ወዛደር ከገጠመው ሁኔታ እጅግ አብዮታዊና ከሁሉም በላይ አጣዳፊ ተግባር ነው ። የዚህ ተግባር መሟላት ማለትም የአውሮፓን ኃይል አገዛዝ የመደምሰሱ ብቻ ሳይሆን (አሁንምእንደሚባለው) የእስያን አድህሮት ኃይል እንኮታኩቶ መጣሉ የሩሲያን ወዝአደር የዓለም አቀፍ አብዮታዊ ወዛደር ግንባር ቀደም መሪ ያደርገዋል»። (ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ውስጥ ገጽ 50፤ )

በተጨማሪም ሲገልጽ ፦— «ልንገነዘበው የሚገባን ከመንግስቱ ጋር ለከፊል ጥያቄ የምናደርገው ትግል ፣ በከፊል ድርድሮች ድል ለማግኘት ከጠላቶቻችን ጋር የምናደርጋቸው ጥቃቅን ሽኩቻዎችና ጥቃቅን ግጭቶች ብቻ ሲሆኑ ዋናውና ወሳኙ ገና ወደፊት ይገጥመናል ። ከፊት ለፊታችንም በመላው ሀይሉ ሁሉ የጥይት ውርጅብኝ የሚያዘንብብንና ምርጥ ታጋዮቻችንን የሚያጭድ የጠላት ምሽግ ተደቅኗል ። ይህን ምሽግ መያዝ ይኖርብናል ። ይህንንም ምሽግ ለመያዝ የምንችለው መላውን የነቁ ወዝአደሮችን ሀይል ከመላው የሩሲያ አብዮታዊ ሀይሎች ጋር በአንድ ሥር በማዋሀድና በሩስያ ውስጥ ያሉትን ደጋፊዎች ሁሉ ከዚህ ድርጅት ሥር ማሰባሰብ ስንችል ብቻ ነው . . . . . . እንዲሁም ታላቁ የትንቢት ሰው ፣ የሩሲያ አብዮተኛ ፒተር አሌክሲየቭ እንዳለው ሲፈጸም ብቻ ነው በወታደሮች አረመኔያዊ ሳንጃ የሚጠበቀውን የፈላጭ ቆራጩን የአገዛዝ ቀንበር በሚሊዮን ሠራተኞች ጠንካራ ጡንቻ የሆሳንሳ ተነስቶ ወደ አቧራነት የሚለወጠው !» (ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ ፣ 59)

በፈላጭ ቆራጩ ዛሪስት ሩስያ ውስጥ የሰራተኛውን መደብ ፓርቲ ለመፍጠር ሌኒን የነደፈው ንድፍ ይህ ነበር ።

«ኢኮኖሚስቶች» በሌኒን ንድፍ ላይ ቀቃውሞ ለመሰንዘር ጥቂትም አልቆዩም ነበር ።

«ኢኮኖሚስቶች» የዛሩን አገዛዝ በመቃወም የሚደረገው አጠቃላይ ፖለቲካዊ ትግል የሁሉም መደብ ትግል ነው? በማለት ተቃውሞአትውን ሲሰነዝሩ ፤ ይህንን ትግል የማካሄዱ ቅድሚያ የቡርዧው ስለሆነ የሠራተኛው መደብ በዚህ ጉዳይ ላይ ጽኑ ትኩረት ሊኖረው አይገባም አሉ ። የሠራተኛው መደብ ዋነኛ ዓላማ ከአሠሪዎቹ ጋር ለኢኮኖሚ ጥያቄዎች ፣



ለደሞዝ ጭማሪ ፣ ለተሻሻለ የሥራ ሁኔታ ወዘተ . . . . የሚደረግ ትግል ነው ። ስለሆነም የሶሻል—ዲሞክራቶች ቀደምትና አስቸኳይ ዓላማ በዛሩ አገዛዝ ላይ ፖለቲካዊ የተቃውሞ ትግል ማካሄድ ሳይሆን ወይም የዛሩን አገዛዝ ማውደም ሳይሆን «ሠራተኞች አሰሪዎቻቸውንና አገዛዙን በመቃወም የሚደረግ የኢኮኖሚ ትግል» ማደራጀት ነው ። ከመንግሥቱ ጋር የሚደረግ የኢኮኖሚ ትግል በነርሱ አባባል ለተሻሻሉ የፋብሪካ ሕጐች መታገል ማለት ነው ። «ኢኮኖሚስቶች» በዚህ ዓይነት መንገድ ራሱ «የኢኮኖሚ ትግል ፖለቲካዊ ባሕርይ ሊያገኝ ይቻላ፡» ሲሉ ይለፍፉ ነበር ።

«ኢኰኖሚስቶች» የሠራተኛው መደብ ፖለቲካ ፓርቲን በግልጽ አይቃወሙት እንጂ የሰራተኛው መሪ ሀይል መሆን የለበትም ፤ እንዲያውም ብቻውን መምራት ይቅርና በሰራተኛው መደብ ግብታዊ እንቅስቃሴ ውስጥ እንኳ መሳተፍአይኖርበትም ፤ ነገርግን የሠራተኛውን ንቅናቄ ሂደት በመከተል ትምህርት ይቀስማል ከርሱም ይማራል እያሉ ሰበኩ ።

«ኢኮኖሚስቶች» ከዚህም በላይ በመቀጠል በሰራተኛው መደብ ንቅናቄ ውስጥ የነቁ ክፍሎች ሚና ፣ የሶሻል-ዲሞክራቶችን የመምራት ድርሻ ፣ እንዲሁም የሶሻሊስት ንድፈ-ሀሳብ የሚኖራቸው ጠቀሜታ እጅግ ያነሰ ወይም እንዳችም ጠቀሜታ አይኖራቸውም ። ሶሻል-ዲሞክራቶች የሠራተኛውን አስተሳሰብ ወደ ሶሻሊስት ንቃተ-ሕሊና ማሳደግ አይችሉም ። ይሁን እንጂ በተቃራኒው ራሳቸውን ዝቅ በማድረግ በአማካይ ደረጃ ወይም እጅግ ኋላ ከቀሩት የሠራተኛው መደብ ክፍሎች መስተካከል አለባቸው ። እንዲሁም ሶሻል - ዲሞክራቶች ሶሻሊስት ንቃተ-ሕሊናን ለሰራተኛው መደብ ለመስጠት ሳይሞክሩ የሰራተኛው መደብ ግብታዊ ንቅናቄ ራሱን ወደ ሶሻሊስት ንቃተ-ሕሊና እስኪያመጥቅ ድረስ መጠበቅ ይኖርባቸዋል በማለት ለፈፉ ።

የፓርቲውን ድርጅት ለማደራጀት ሌኒን የነደፈውን እቅድ በሚመለከት ረገድ ፣ «ኢኮኖሚስቶች» ግብታዊውን እንቅስቃሴ ለመቃወም የወጣ አድርገው ይመለከቱታል ።

በኢስክራ ዓምድና ፣ ምን መደረግ አለበት በሚለው ክቡር ሥራው ሌኒን ይህን አድርባይ «የኢኮኖሚስቶች» ፍልስፍና በመቃወም ጠንካራ ትግል በማካሄድ አጋልጦታል ።

1/ ሌኒን የሠራተኛው መደብ ዛሩን ለማውደም ከሚያደርገው አጠቃላይ ፖለቲካዊ ትግል አቅጣጫውን እንዲለውጥ ማድረግና ከአገዛዙ ጋር የኢኮኖሚ ትግል በማድረግ ብቻ ተወስኖ አሰሪዎችንና አገዛዙን እንዳይነኩ ፣ ማለት የሠራተኛውን መደብ ለዘላለም ባሪያ እንዲሆን መፍረድ ነው ሲል አጋልጧል ። በአሠሪዎችና በአገዛዙ ላይ ሠራተኞች የሚያደርጉት የኢኮኖሚ ትግል ሠራተኞች

የሥራ ሀይላቸውን ለካፒታሊስቶች በተሻሻለ ሁኔታ ለመሸጥ እን
ዲችሉ የሚያደርግ የሙያ ማኅበር ትግል ነበር ። ያም ሆነ ይህ
ሠራተኞች ለመዋጋት የሚፈልጉት የሥራ ጉልበታቸውን ለካፒ
ታሊስቶች እንዲሸጡና በብዝበዛ እንዲማቅቁ ያደረጋቸውን የካፒ
ታሊስት ሥርዓተ-ማኅበር ራሱን ለማስወገድም ጭምር ነው ። ይሁን
እንጂ የካፒታሊዝምን ሕልውና ጠባቂ የሆነው የዛሩ አገዛዝ የሠራ
ተኛውን መደብ የትግል ጐዳና በመዝጋት አብዮተኞችን ለመንከስ
ለሀጩን ሲያንጠባጥብና ጭራውን ሲቆላ ይታያል ። እንደዚህ ያሉ
የካፒታሊዝም ተናካሽ ውሾች (የዛሩ አገዛዝ) ከወዝአደሩ የትግል
ጐዳና ላይ እስካልተወገዱ ድረስ ሠራተኞች ከካፒታሊዝም ጋር
የሚያደርጉት ፍልሚያ ፣ ሶሻሊዝምን ለመገንባት እስከመጨረሻው
የሚያደርጉት መራራ ትግል ከቶም ሊሰምር አይችልም ። ስለሆነም
የፓርቲው አንገብጋቢና የመጀመሪያ ተግባር በጐዳናው ላይ የመሸ
ገውን የዛሩን አገዛዝ አስወግዶ ለሶሻሊዝም ግንባታ ጐዳናውን መጥ
ረግ ትልቁ ተግባሩ ነበር ።

2/ በሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ውስጥ ግብታዊውን ሂደት ማጋነንና
ማሞካሸት ፓርቲው የመሪነት ሚና ሊጫወት እንደማይችል
መካድ ፣ እንደ ድርጊቶች መዝጋቢ ሚናውን ዝቅ ማድረግ ፣ በሌላ
አባባል የድርጊቶች ጭራ ማለትም ኮቮቲዝምን መስበክ ሲሆን ፓር
ቲውን የግብታዊ ሂደቶች ጭራ ወይም ተሳትፎ አልባ ማድረግና
ነገሮች የራሳቸውን ሂደት ተከትለው እንዲሄዱ እንደመፍቀድ ይሆ
ናል በማለት ሌኒን አሳይቷል ። ይህንን መስበክ ማለት ሠራተኛውን
መደብ ያለ ፓርቲ ያለትጥቅ ማስቀረት ማለት ነው ። ይሁን እንጂ
እስከ ጥርሱ የታጠቀውን የዛሩን አገዛዝና በዘመናዊ መንገድ የተ
ደራጀውንና የሠራተኛውን መደብ ለመቃወም በሚያደርገው ትግል
የራሱ የሆነ ፓርቲ ባለው በቡርዧው ፊት የሠራተኛውን መደብ
ያለትጥቅ ማስቀረት ፣ ማለት ወዝአደሩን መክዳት ማለት ነው ።

3/ ለሰራተኛው መደብ ግብታዊ ንቅናቄን በማምለክ መስገድና የሶሻ
ሊስት ንቃተ-ሕሊና የሶሻሊስት ንድፈ-ሀሳብ አስፈላጊነትን ዝቅ
አድርጐ መገመት ማለት በመጀመሪያ ደረጃ በንቃተ-ሕሊናቸው
ዝቅተኛ የሆኑ ሠራተኞችን መስደብ ፣ በሁለተኛ ደረጃ ደግሞ በፓ
ርቲው አመለካከት የንድፈ-ሀሳብን ዋጋ ዝቅ ማድረግ ማለትም
ፓርቲው የወቅቱንና የወደፊቱን ተመልክቶ ለመረዳት የሚረዳ
ውን መሣሪያ ማንኳሰስና በሶስተኛ ደረጃም ፣ በአጠቃላይና በማይ
ለወጥ ሁኔታ በአድርባይነት ባሕር ውስጥ መስጠም እንደሆነ ሌኒን
አሳይቷል ።

«ያለአብዮታዊ ንድፈ-ሀሳብ» ይላል ሌኒን «አብዮታዊ ንቅናቄ
ሊኖር አይችልም . . . . . የግንባር ቀደም ተዋጊዎች ሚና ሊሟላ የሚ
ችለው እጅግ በመጠቀ ንድፈ-ሀሳብ በሚመራ ፓርቲ ብቻ ነው ።»



4/ «ኢኮኖሚስቶች» ሶሻሊስት ርዕዮተ-ዓለም ከሠራተኛው መደብ
ግብታዊ ንቅናቄ ይመነጫል ባሉበት ጊዜ ነበር ሠራተኛውን መደብ
ለማታለል የሞከሩት ። እንደ እውነቱ ከሆነ የሶሻሊስት ርዕዮተ-
ዓለም ከግብታዊ ንቅናቄ የሚገኝ ሳይሆን ከሳይንስ የሚመነጭ ነው ።
ለሠራተኛው መደብ የሶሻሊስት ንቃተ-ህሊና ለሠራተኛው መደብ
አስፈላጊነቱን በመካድ «ኢኮኖሚስቶች» ለቡርዧው ርዕዮተ-ዓለም
መንገድ በመጥረግ የመቻሉ መግቢያ መንገዱ ቀላል እንዲሆ
ንና በሠራተኛው መደብ መሀከልም እንዲሰራጭ ብሉም የሠራተ
ኛውን መደብ ንቅናቄ ሶሻሊዝምን የማዋሀዱ ሀሳብ እንዲቀበር
በማድረግ ቡርዧውን ያገለግላሉ ሲል ሌኒን አሳይቷል ።

«የሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ግብታዊ ነው ብለው የሚያምኑ
የሠራተኛውን የነቃ ክፍል ሚና ፣ የሶሻል ዲሞክራሲ ፓርቲ የሚጫ
ወተውን ሚና ዝቅ ማድረግ ወይም ማንኳሰስ ማለት ወደዱም ጠሉም
እነዚህ አንኳሳሾች የቡርዧው ርዕዮተ-ዓለም በሠራተኛው መደብ
መሀከልም ያለውን ተጽእኖ እያጠናከሩ ናቸው ።» በማለት ሌኒን
ገልጿል ።

በመቀጠልም «የቡርዧው አሊያም የሶሻሊስት ርዕዮተ-ዓለም ፣
አንድ ብቸኛ ምርጫ ነው ። ሌላ በመሀከል ያለ ሂደት የለም . . . . . .
ስለሆነም የሶሻሊስትን ርዕዮተ-ዓለም ማንኳሰስ በማንኛውም መን
ገድ ከሶሻሊስት ርዕዮተ-ዓለም ወደሌላ አቅጣጫ ማዘንበል ማለት
የቡርዧውን ርዕዮተ-ዓለም ማጠናከር ማለት ነው ።»

5/ እነዚህን «የኢኮኖሚስቶች» ስሕተት ሁሉ በማዳመር ሌኒን የሠራ
ተኛውን መደብ ከካፒታሊዝም ብዝበዛ ሥር ነጻ የሚያወጣ የሶሻል
አብዮት ፓርቲን አይፈልጉም ሲል ደመደመ ። ይሁን እንጂ
የካፒታሊስት አገዛዝን ለማዳን ሁኔታዎችን የሚፈጥር «የሶሻል
ጥገና» ፓርቲ ይፈልጋሉ ፤ ብሎም «ኢኮኖሚስቶች» የወዝአደሩን
መሰረታዊ ዓላማ የካዱ ጠጋኞች ናቸው ።

6/ በመጨረሻም ፣ ሌኒን አበጥሮ እንዳሳየው «ኢኮናሚዝም» በሩስያ
ውስጥ ድንገተኛ የመጣ ክስተት አልነበረም ። ነገር ግን «ኢኮኖ
ሚስቶች» ቡርዧው በሠራተኛው መደብ ላይ ተጽዕኖ ለማሳደር
የሚያገለግሉ መሣሪያዎች ሲሆኑ ፤ ከምዕራብ አውሮፓ ሪቪዥኒ
ስት ሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ጋር የጠበቀ ግንኙነት የነበራቸው
የአድርባዩ በርንስታይን ተከታዮች ነበሩ ። በምዕራብ አውሮፓ
የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ውስጥ አድርባይ አዝማሚያዎች ጥን
ካሬ እያገኙ ሲመጡ ማርክሲዝምን «የመውቀስ ነጻነት» ይሰጠን በሚ
ልሽፋን የማርክሲዝምን አስተምህሮ «ለመከለስ» ተነሱ (ከዚያም
በኋላ ነው ሪቪዥኒዝም የሚለውን ቃል መጠቀም የተጀመረው)
ይህም አብዮት ፣ ሶሻሊዝምና ፡ የወዝአደሩ አምባገነንነት ጭራሹኑ

እንዳይነሳ የማይፈልግ ነበር ። የሩስያ «ኢኮኖሚስቶች» አብዮታዊውን ትግል ፣ ሶሻሊዝምንና የወዝአደሩን አምባገነንነት በመካድ እንደዚሁ ዓይነት ፖሊሲ እንደሚያራምዱ ሌኒን አሳይቷል ።

ይህ ነበር «ምን መደረግ አለበት ?» በሚለው መጽሐፉ ሌኒን ንድፈ-ሀሳባዊ መመሪያውን ያብራራው ።

የሌኒን መጽሐፍ በሚገባ በመሠራጨቱና ሁለተኛው የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራሲ ፓርቲ ስብሰባ መጽሐፉ ከታተመ ከዓመት በኋላ በመደረጉ (በመጋቢት 1902 ዓ.ም. ታተመ) «የኢኮኖሚስቶች» ርዕዮተ-ዓለም የተጠላ ትዝታ ሆኖ ከመቅረቱ በቀርና «ኢኮኖሚስት» ተብሎ መጠራት በአብዛኛዎቹ የፓርቲ አባላት ዘንድ እንደ ስድብ የሚቆጠር ከመሆኑ በቀር ሌላ ምንም አልነበረም ።

ይህም «ለኢኮኖሚስቶች» ለኮበስቲስዝምና ለግብታዊነት ታላቅ ርዕዮተ-ዓለማዊ ሽንፈት ቢሆንም ምን መደረግ አለበት ? የሚለውን የሌኒን መጽሐፍ አስፈላጊነቱን አላስቀረውም ።

በዚሁ ታሪካዊ ጠቃሚነት ባለው ክቡር መጽሐፍ ውስጥ ሌኒን

1. በማርክሲስት የአስተሳሰብ ታሪክ ውስጥ ለመጀመሪያ ጊዜ የሰራተኛውን መደብ ንቅናቄ ግብታዊነት የሚያመልኩና በሰራተኛው መደብ ንቅናቄ ውስጥ ሶሻሊስት ንቃተ-ሕሊናን የሚያንኳስሱ መሆናቸውን በማሳየት የአድርባዮችን ርዕዮተ-ዓለም እርቃኑን አስቀርቷል ።

2. የንድፈ-ሀሳብ ፣ የንቃተ-ሕሊናና የፓርቲ ታላቅ ጠቀሜታ የሠራተኛውን መደብ ግብታዊ ንቅናቄ የሚመራና አብዮታዊ የሚያደርገውን ሀይል አስፈላጊነት አሳይቷል ።

3. ማርክሳዊ ፓርቲ የሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ከሶሻሊዝም ጋር መዋሀድ ነው የሚለውን መሰረታዊ የማርክሲስት በኩረ-ሀሳብ በአስደናቂ ሁኔታ አዳብሯል ።

4. የማርክሲስት ርዕዮተ-ዓለማዊ መሰረትን በሚገባ ገለጸ ።

ምን መደረግ አለበት? በተሰኘው መጽሐፍ ውስጥ ተበራርተው የነበሩት ንድፈ-ሀሳባዊ በኩረ-ሀሳቦች በኋላ ለቦልሼቪክ ፓርቲ ርዕዮተ-ዓለም መሰረት ሆኑ ።

እንደዚህ ያሉ የንድፈ-ሀሳብ ሀብቶች ለማበርከት ኢስክራ ትችል ነበርና ይህንንም በተገባር ለማዋል በቅታለች ። ፓርቲ ለመገንባት ሌኒን ለነደፈው ንድፍ ከፍተኛ ዘመቻ ማካሄዱን በማጠናከር የራስ ሀይሎችን ለማሰባሰብ ፣ ሁለተኛ የፓርቲ ኩንግረስ ፣ አብዮታዊ ሶሻል ዲሞክራቶችን በመጥራትና «በኢኮኖሚስቶች» ፣ በሪቪዥኒስቶችና በሁሉም ዓይነት አደርባዮች ላይ የአመጽ ችቦ ፣ አቀጣጥላለች ፣ የትግሉን አቅጣጫ በመጠቀም ከፍተኛ ጥረ አድርጋለች ።



ኢስክራ ከአከናወነቻቸው ሥራዎች ውስጥ እጅግ ጠቃሚው ክፍል ለፓርቲው መርሀ-ግብር መንደፍ ነበር ። የሠራተኛው መደብ ፓርቲ መርሀ-ግብር ፣ እስከምናውቀው ድረስ ፣ የሠራተኛው መደብ የሚታገልላቸውን ዓላማዎችና ግቦች በአጫጭሩና ሳይንሳዊ በሆነ መንገድ የተቀመረ እንደመሆኑ መጠን ፤ መርሀ-ግብሩ የወዝአደሩን ዘላቂ ግቦች አብራርቶ መንደፍ ብቻ ሳይሆን ይህን ዘላቂ ግብ በድል አድራጊነት ለመወጣት በሚያደርገው የትግል ጉዞው ውስጥ በቅደሚያ ሊያከናውናቸው ስለሚገቡ ጥያቄዎች ጭምር ያወሳልና ስለዚህም የመርሀ-ግብሩ ንደፍ ተቀዳሚ ጠቀሜታ ነበረው ።

ይህን መርሀ-ግብር በነደፉበት ወቅት በኢስክራ አዘጋጆች መሀል ጠንካራ ልዩነት ተፈጥሮ ነበር ። በአንድ ወገን ሌኒን ሲቆም በሌላው ወገን ደግሞ ፕሌክሀኖቭና ሌሎችም የጋዜጣው የመምሪያ አባሎች ሽንጣቸውን ገትረው ቆሙ ። ይህ ልዩነትና ግጭት በሌኒንና በፕሌክሀኖቭ መሀል መከፋፈልን ፈጠረ ። ይሁን እንጂ በዚያ ወቅት ነገሮች ከጊዜው ሁኔታ አልቀደሙም ነበር ። ሌኒን በተነደፈው መርሀ-ግብር ፣ በወዝአደሩ አምባገነንነት ጠቃሚ አንቀጽ ላይና በአብዮት ውስጥ የሰራተኛውን መደብ የመሪነት ሚና በሚገልጸው ጉልህ አረፍቱ ነገሮች ላይ ባዕዳን ሀሳቦች እንዳይታከሉበት ከፍተኛ ጥንቃቄ አድርጓል ።

በመርሐ-ግብሩ ላይ አጠቃላይ የገጠሩን ጥያቄ ነድፎ ያቀረበው ሌኒን ነበር ። በዚያን ወቅት ሌኒን መሬትን በቁጥጥር ሥር ማድረግ ቢፈልግም ቅሉ በመጀመሪያው የትግል ደረጃ አትሬዚኪ ማለትም በገበሬዎች «ነጻ መውጣት» ወቅት የመሬት ከበርቴዎች ከገበሬዎች መሬት ቆርሰው የወሰዱትን የማስመለሱን ጥያቄ ማራመድ ታላቅ ጠቀሜታ አለው ሲል ፕሌክሀኖቭ ግን መሬትን የመውረስ አስፈላጊነትን በይፋ ተቃወመ ።

በፓርቲው መርሀ-ግብር ላይ በሌኒንና በፕሌክሀኖቭ መሀል የተከሰተው ልዩነት ለወደፊቱ በቦልሼቪኮችና በሜንሼቪኮች መሀል ለሚፈጠረው ልዩነት እስከተወሰነ ደረጃ ወሳኝነት ነበረው ።

3. የሩስያ ሶሻል ዲሞክራቲክ የሠራተኞች ፓርቲ ሁለተኛ ኩንግረስ ። የአንድ ፓርቲ መርሐ-ግብር ፣ ደንቦችና አመሰራረት መውጣት ። በኩንግረሱ ላይ የነበሩ ልዩነቶችና በፓርቲ ውስጥ የተከሰቱ የሁለቱ የፖለቲካ መስመሮች - ቦልሼቪክና ሜንሼቪክ ።

ስለሆነም ሌኒን ለነደፈው የድርጅት ፕላን ኢስክራ ያካሄደችው ውጤታማ ትግልና የሌኒን መመሪያ አሸናፊነት ለፓርቲው መፈጠር አስፈላጊውን ሁኔታ ሁሉ አዘጋጀ ፣ ወይንም ፣ በወቅቱ እንደ ተባለው ሁሉ የእውነተኛውን ፓርቲ ለምለም መስክ አዘጋጀ ። ኢስክራ በሩስያ የሶሻል ዲሞክራቲክ ድርጅቶች ዘንድ ተቀባይነትን አተረፈች ። በመሆኑም ሁለተኛውን የፓርቲ ኩንግረስ ለመጥራት ሁኔታው ያመች ሆነ ።

ሁለተኛው የሩ.ሶ.ዲ.ሰ.ፓ ስብሰባ ሐምሌ 17 ቀን 1902 ዓ.ም. በሚስጢር ከሩሲያ ውጪ በመጀመሪያ በብራስልስ ስብሰባ ተከፈተ ። ይሁን እንጂ የቤልጂግ ፖሊሶች የስብሰባውን አባላት ሀገሪቷን በአስቸኳይ ለቀው እንዲወጡ በመጠየቃቸው ከዚያን ወቅት ጀምሮ ስብሰባው ወደሉንደን እንዲለወጥ ሆነ ።

በስብሰባው ላይ 43 ተወካዮች 26 ድርጅቶችን በመወከል ሲገኙ እያንዳንዱ ኮሚቴ ሁለት ተወካዮች እንዲልክ ተጠይቆ ነበር ። ነገር ግን አንዳንዶቹ የላኩት አንድ ተወካይ ብቻ ስለነበር ፤ አርባ ሶስቱ ተወካዮች 51 ድምጽ እንዲኖራቸው ሆነ ።

የኮንግሬሱ አበይት ዓላማ «ኢስክራ ባራመደችውና በአብራራችው መመሪያዎችና ድርጅታዊ መርሆች መሰረት ኮንግረሱን እውነተኛውን ፓርቲ መፍጠር ነበር ።»
(ሌኒን ምርጥ ስራዎች የእንግሊዝኛ እትም ሞስኮ 1947 ቅጽ 1 ገጽ 275)

ኮንግረሱን የተካፈሉት ተወካዮች ሁሉ እውነተኛ የመሥመር አራማጆች ባለመሆናቸው በርካታ የተለያዩና የማይመሳሰሉ ተወካዮችም ነበሩ ። እውቅ «ኢኮኖሚስቶች» በደረሰባቸው ከፍተኛ የርዕዮተ-ዓለም ሽንፈት የተነሳ በስብሰባው ባይወከሉም ቅሉ አመለካከታቸውን በረቀቀ ጥበብ በመሸፋፈን በርከት ያሉ የዚሁ መሥመር አማኒያንንና ተከታዮችን በኮንግሬሱ ውስጥ አስርገው አግብተው ነበር ። ከሁሉም በላይ የበንድ ተወካዮች «ኢኮኖሚስቶች» የመሆናቸውን እውነትነት ለመሸፈን ከመጣራቸው በቀር እንደ እውነቱ ከሆነ «ኢኮኖሚስቶች» በጽኑ የሚደግፉ ቡድኖች ነበሩ ።

ስለሆነም ኮንግረሱ የተካሄደው በኢስክራ ደጋፊዎች ብቻ ሳይሆን የኢስክራ ዓይነተኛ ጠላቶች በሆኑትም ጭምር ነበር ። ከኮንግረሱ አባላት 33ቱ ማለትም አብዛኞዎቹ የኢስክራ ደጋፊዎች ነበሩ ። ይህ ሲባል ግን ራሳቸውን ኢስክራዊያን በማለት የሚጠሩ ሁሉ ሌኒናዊ=ኢስክራውያን ናቸው ማለት አይደለም ። የኮንግረሱ ተካፋዮች በዛ ባሉ የተለያዩ ቡድኖች የተከፋፈሉ ነበሩ ። የሌኒን ደጋፊዎች ወይም ጽኑ ኢስክራውያን 24 ድምጽ ሲኖራቸው ፤ ዘጠኙ ኢስክራውያን ደግሞ የማርቶቭ ተከታዮች ሆኑ ። እነዚሁ ጽኑ ኢስክራዊያን አልነበሩም ። አንዳንድ የኮንግረሱ አባላት ደግሞ በኢስክራውያንና በተቃዋሚዎቹ መሀል ይዋዥቁ ነበር ። እነዚህ መሀል ሰፋሪዎች 10 ድምጽ ሲኖራቸው ፣ በማዕከሉም ውስጥ ከፍተኛ ቦታ ነበራቸው ። የኢስክራ ርቱእ ተቃዋሚዎች 8 ድምጽ ነበራቸው ። ይህም ሶስቱ «የኢኮኖሚስቶች» ሲሆኑ ፣ አምስቱ ደግሞ የባንዲስቶች ነበሩ—በኢስክራውያን መሀል የነበረው መከፋፈል ለኢስክራ ርቱዕ ጠላቶች ከፍተኛ ጥንካሬ ሊሰጥ በቅቷል ።

ስለሆነም በኮንግሬሱ ውስጥ የነበረው ሁኔታ ምን ያህል ውስብስብ እንደሚሆን በገሀድ ሊታይ የሚችል ነበር ። ሌኒን የኢስክራን አሸናፊነት ለማረጋገጥ ታላቅ ተጋድሎ አድርጓል ።



በኮንግረሱ አጀንዳ ላይ ከሰፈሩት ነጥቦች እጅግ ጠቃሚው ነጥብ የፓርቲውን መርሀ-ግብር ማጽደቅ ነበር ። በመርሀ-ግብሩ ላይ የከረረ ውይይት በተደረገበት ወቅት የኮንግረሱ አድርባይ ክፍሎች ያነሱት ዓበይት ነጥብ ስለ ወዝአደሩ አምባገነንነት ጥያቄ ነበር ። አድርባዮች ከኮንግረሱ አብዮታዊ ክፍል ጋር ያልተጣጣሙባቸው በፕሮግራሙ ውስጥ የተጠቀሱ በዛ ያሉ የተለያዩ ጥያቄዎች ነበሩ ። ምንም እንኳን በመርሀ-ግብሩ ላይ የተነሱ ሀሳቦች ለነዚህ ለኮንግረሱ አድርባዮች ሊዋጥላቸው ባይችልም ከመረሩአቸው ሀሳቦች ሁሉ እጅግ መራራው በሆነው ጥያቄ ፡— በወዝአደሩ አምባገነንነት ጥያቄ—ላይ ዓይነተኛ ተቃውሞ ለማድረግ ወሰኑ ። ከሀገር ውጪ የሚገኙ የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲዎች መርሀ-ግብር ላይ እንዳችም ስለወዝአደሩ አምባገነንነት የሚያነሳ አንቀጽ የለምና በሩሲያ የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ መርሀ-ግብር ላይ መጠቀስ አይኖርበትም ሲሉ ሽንጣቸውን ገትረው ተቃወሙ ።

መች ይህ ብቻ የገበሬውን ጥያቄ አስመልክቶ በመርሀ-ግብሩ ላይ እንዳችም ነገር መታከል የለበትም ሲሉ አይናቸው እስኪቀላ ፣ ደማቸው እስኪፈላ ጮሁ ። እነዚህ ሰዎች አብዮት የሚሹ አይደሉም ፣ የወዝአደሩንና የገበሬውን ኅብረት በመፍራት የሚያስከትለው ሁኔታ ስላስደነገጣቸው ብቻ ትግሉን ይደግፋሉ ።

ባንዲስቶችና የፖሊሽ ሶሻል ዲሞክራቶች የብሔሮችን የራስን እድል በራስ መወሰን መብት አጥብቀው ተቃወሙ ። የሰራተኛው መደብ የብሔር ጭቆናን መታገል እንዳለበት ሌኒን አዘውትሮ ያስተምር ነበር ። በመርሀ-ግብሩ ላይ ይህ ጥያቄ መታከሉን መቃወም ዓለም አቀፋዊ ወዛደራዊነትን እንደመክዳት የሚቆጠርና በብሔር ጭቆና ውስጥ ግብረአበር መሆን ነው ።

ለነዚህ ሁሉ ተቃውሞዎች ሌኒን አጠር ያሉ ጽሁፎችን አቅርቧል ።

በኢስክራ ላይ የተደገፈውን መርሀ-ግብር ኮንግረሱ አጽድቆ ተቀበለው ።

ይህ መርሀ-ግብር ሁለት ክፍሎች ማለትም መልእል መርሀ-ግብርና መንስእ መርሀ-ግብር ነበሩት ። መልዕሉ መርሀ-ግብር የሚያወሳው የሠራተኛውን መደብ ፓርቲ ዘላቂ ግብ (ዋናው ዓላማ) ማለትም የሶሻሊስት አብዮት ፣ የካፒታሊስቶችን ሀይል ማንኮታኮትና የወዝአደሩን አምባገነንነት መመስረት ሲሆን ፤ መንእሱ መርሀ-ግብር የሚያወሳው ደግሞ የፓርቲውን ጊዜያዊ ዓላማዎች ፣ የካፒታሊስት ስርዓት ከመገርሰሱና የወዝአደሩ አምባገነንነት ከመመስረቱ በፊት ሊሚሉ የሚችሉ ዓላማዎችን ማለትም የዛሩን ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ማስወገድ ፣ ዲሞክራሲያዊ ሪፐብሊክ መመስረትና የሥራ ጊዜ 8 ሰዓት እንዲሆን መወሰን ፣ በገጠር የገባርነትን ቅሬቶች ማስወገድና በመሬት ከበርቴዎች የሚበዘበዙትን ጉማድ መሬቶች (ኦትሬዝኪ) ለገበሬዎች ማስመለስ ነበሩ ።

በመቀጠልም ፣ ቦልሼቪኮች ጉማድ መሪዎችን (አትሬዝኪ.) የማስመለስ ጥያቄን መሬት በመውረስ ጥያቄ እንዲተካ አደረጉ ።

በሁለተኛው ኮንግረስ ላይ የጸደቀው መርሀ-ግብር የሰራተኛው መደብ ፓርቲ አብዮታዊ መርሀ-ግብር ነበር ።

ስምንተኛው የፓርቲ ስብሰባ እስኪተደረገበት ወቅት ድረስ የወዝአደሩ አብዮት ድል ካደረገ በኋላ ማለትም ስምንተኛው የፓርቲ ኮንግረስ እስኪተደረገበትና ፓርቲያችን አዲስ መርሀ-ግብር አጽድቆ እስከ አወጣበት ወቅት ድረስ ይህ መርሀ-ግብር ሀያል እንደሆነ ቆይቷል ።

መርሀ-ግብሩን በማጽደቅ ሁለተኛው የፓርቲ ኮንግረስ የፓርቲውን ሕግ ወደመንደፉ ተሸጋገረ ። እንግዲህ አሁን ኮንግሬሱ መርሀ-ግብሩን አጽድቋልና ለፓርቲው ርዕዮተ-ዓለማዊ አንድነት መሰረት ጥሏል ማለት ነው ። እንዲሁም የናቡድናቹን ጠባብ አመለካከትና ጮርቃነት ፣ ድርጅታዊ መንጣጠሎችንና በፓርቲው ሕልውና ውስጥ ያልሰፈነውን ጠንካራ ሥነ-ሥርዓት ለመስጠት የፓርቲውን ሕግጋት ማጽደቅ ይኖርበታል ።

መርሀ-ግብሩን ለማጽደቅ የነበረው ሁኔታ በእንጻራዊ ሲታይ የከረረ መንገድ አልተኬተለም ። ይሁን እንጂ የፓርቲውን ሕግጋት አስመልክቶ ኃይለኛ ግጭቶች (ክርክር) በኮንግረሱ ውስጥ ተፈጥረው ነበር ። በመጀመሪያ ስለፓርቲው አባልነት በሚያወሳው የሕግ አንቀጽ ላይ የሰላ ልዩነት ተከሰተ ። የፓርቲው አባል ሊሆን የሚችለው ማነው ? ፓርቲው ሊያቅፋቸው የሚገባው ምኖችን ነው ? የፓርቲው ድርጅታዊ ባሕርይ ምን መሆን ይገባዋል ? ሁሉን ያደራጀ ወይስ ምንም የተለየ መልክ የሌለው ? —እነዚህ ነበሩ በመጀመሪያው የሕጉ አንቀጽ ላይ ለተነሱት ጥያቄዎች ሁለት የተለያዩ ቅመራዎች ግጭት የፈጠሩት ። እነርሱም በፕሌክሀኖቭና በጽኑ ኢስክራይስቶች የተደገፈው የሌኒን ቅመራ ሲሆን በአክስልሮድ ፣ በዛሱሊች ፣ በጊዜያዊ ኢስክራይስት በነበረው በትሮትስኪና በመላው የኮንግረሱ እውቅ አድርባዮች የተደገፈው የማሮቶቭ ቅመራ ነበሩ ።

እንደ ሌኒን ቅመራ ከሆነ የፓርቲው ዓባል ሊሆን የሚችለው የፓርቲውን መርሀ-ግብር በሚገባ የተቀበለ ፣ የገንዘብ ድጋፍ የሚያደርግና ከፓርቲው ድርጅቶች በአንዱ የተሳተፈ መሆን ይኖርበታል ። የሚል ሲሆን የማርቶቭ ቅመራ ደግሞ የፓርቲውን መርሀ-ግብር አምኖ ከተቀበለና ለፓርቲው የገንዘብ ድጋፍ ካደረገ ለፓርቲው አባልነት ብቁ ይሆናል ። ከፓርቲው ድርጅቶች በአንዱ የግድ መሳተፍ አለበት ማለት የሚያስፈልግ አይደለም ሲል የፓርቲ አባል ለመሆን የግድ ከፓርቲ ድርጅቶች በአንዱ መሳተፍ አለበት የሚለውን አስፈላጊነት ተቃወመ ።

ፓርቲው ማንም መንገደኛ ራሱን የፓርቲ አባል ማድረግ የማይችልበት የተደራጀ መሪ አካል ነው ፤ ይሁን እንጂ የፓርቲ አባል ለመሆን ከፓርቲ ድርጅቶች በአንዱ ድርጅት የተፈቀደለትና ራሱን ለፓርቲው



ዲሲፕሊን ያስገዛ መሆን ይኖርበታል በማለት ሌኒን ሲናገር ፤ በሌላው ወገን ደግሞ ማርቶቭ ፓርቲን ድርጅታዊ ቅርጽ የሌለው ቅርጸ-አልባ ፣ አባሎቹ በፍላጎታቸው የፓርቲ አባል በመሆን የሚገቡበት ፤ ስለሆነም ለፓርቲው ሥነ-ሥርዓት ራሳቸውን እንዲያስገዙና ከፓርቲው ድርጅቶች ውስጥ በአንድ ድርጅት እንዲሳተፉ አይገደዱም በማለት በተቃራኒው ቆመ ።

ስለሆነም ፣ እንደ ሌኒን ቅመራ ሳይሆን የማርቶቭ ቅመራ የፓርቲውን በር ወዛደራዊነት ለሌላቸው ቋሚ ላልሆኑ ክፍሎች በረጋገደላቸው ። በቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት ዋዜማ ከቡርዧ ምሁራን መሀል ለጊዜው ፣ አብዮቱን የደገፉ ሰዎች ነበሩ ። ከጊዜ ወደጊዜ ጥቂት አስተዋጽኦ ለፓርቲው ማድረጋቸው የማይቀር ቢሆንም ቅሉ ፤ እንደዚህ ያሉ ሰዎች ድርጅቱን ሊቀላቀሉ ራሳቸውን ለፓርቲው ሥነ ሥርዓት ሊያስገዙ ፣ የፓርቲውን ሥራዎች ሊያከናውኑ ራሳቸውን ለፓርቲው ችግሮች አሳልፈው ሊሰጡ አይችሉም ።

ማርቶቭና ሌሎችም ሜንሼቪኮች እንደነዚህ ያሉትን ሰዎች እንደ ፓርቲ አባላት አድርገው ይመለከቷቸዋልና በፓርቲው ጉዳዮች ላይ ተጽእኖ እንዲያሳድሩ መብትና አጋጣሚ ይሰጡአቸዋል ። ምንም እንኳን ሶሻሊስት ያልሆኑ ፣ ሥርዓተ-አልበኞችና ሶሻሊስት አብዮተኞችም ጭምር በሥራ ማቆም አድማ ውስጥ ተሳትፎ ቢኖራቸውም ቅሉ ሜንሼቪኮች ማንኛውም በሥራ ማቆም አድማ ውስጥ የተሳተፈን ሰው በፓርቲው ውስጥ ራሱን «የማስመዝገብ» መብት እንዲኖረው ሃሳብ አቅርበዋል ። ስለሆነም እነዚህን ሁሉ ጸረ-አብዮተኞች ነበር የፓርቲው አባል እንዲሆኑ ጥያቄ ያቀረቡት ።

ስለዚህም ፣ ሌኒንና ሌኒኒስቶች በኮንግረሱ ላይ ለሚታገሉለት ብቸኛና ቅን ፓርቲ ከነ እውቅ ድርጅቶቹ ምትክ እነማርቶቭ አንድ ወጥ ያልሆነና ደካማ ቅርጸቢስ ፓርቲ-ማለትም በድብልቅ ባሕርያት ምክንያት በጸና ሥነ-ሥርዓት ላይ ያልተመሰረተ ፓርቲ-እንዲመሰረት ፈለጉ ።

የዋገቂ ኢስክራይስቶች ከጽኑ ኢስክራይስቶች መገንጠልና ከመአከላውያን ጋር ሕብረት በመፍጠር ከታወቁ አድርባዮች ጋር መገናኘት በዚህ ነጥብ ላይ የሀይል ሚዛኑን ለማርቶቭ እንዲያጋድል አደረገ ። አንድ ሰው ድምጽ ካለመስጠቱ በቀር 28 ለ 22 በሆነ የድምጽ ብልጫ ኮንግረሱ ማርቶቭ የቀመረውን የመጀመሪያውን የሕግ አንቀጽ አጽድቆ ተቀበለ ።

ኢስክራይስቶች በመጀመሪያው የሕግ አንቀጽ የተነሳ በአቋም ከተከፋፈሉ በኋላ በኮንግረሱ ውስጥ የነበረው ትግል እየከረረ መጣ ። በኮንግረሱ አጀንዳ ላይ በመጨረሻ የሰፈረው የፓርቲውን መሪ ተቋም የመምረጡ ማለትም የፓርቲውን ማዕከላዊ አካል የሥነ-ጽሁፍ ቦርድ (ኢስክራ)

ና የማዕከላዊ ኰሚቴን የመምረጡ ጉዳይ ነበር ። ይህም ቢሆን ቅሉ ምር
ጫው ከመደረጉ በፊት የሀይል አሰላለፉን ሊለውጥ የሚችል ድንገተኛ
ሁኔታ ተከሰተ ።

የፓርቲውን ሕጐች አስመልክቶ ኰንግረሱ በበንዶች ጥያቄ ላይ መነ
ጋገር ነበረበትና በንዶች በፓርቲው ውስጥ የተለየ ሥፍራ እንዲኖራቸው
ስለፈለጉ የሩሲያ አይሁዳዊ ሠራተኞች እውነተኛ ተወካዮች አድርጐ ፓር
ቲው እንዲቀበላቸው ጠየቁ ። ይህን ጥያቄ አንግቦ መቅረብ በፓርቲ ድርጅ
ቶች ውስጥ ያሉትን ሠራተኞች በብሔረሰብ መከፋፈልና የሠራተኞችን
ግዛታዊ የመደብ ድርጅቶች አለመቀበል ነው ። በንዶች ያቀረቡትን
በብሔራዊ መስመሮች ላይ የተመሠረተ አስተሳሰብ ኮንግረሱ ተቃወ
መው ። ሁለት « ኢኮኖሚስቶችም » በውጪ የሚገኘው የውጪ
ሊግ ድርጅታቸው የፓርቲው ተጠሪ የመሆኑን ኮንግሬሱ ባለመቀበሉ
ረግጠው ወጡ ።

የነዚህ ሰባት አድርባዮች ተለይቶ መውጣት በኮንግረሱ ውስጥ የሀ
ይል ሚዛኑን ለሌኒኒስቶች በሚያመች ሁኔታ ለወጠው ።

ከመጀመሪያው ሲጀምር ሌኒን በፓርቲው ማዕከላዊ ተቋም አመሰ
ራረት ላይ ነበርና ሀሳቡን ያተኰረው ፣ የማዕከላዊ ኰሚቴውም፤በጽኑና
ዘላቂ አብዮታውያን የመገንባቱ አስፈላጊነት ላይ ከፍተኛ እምነት ነበ
ረው ። ማርቶቭ ወላዋዮችና አድርባይ ክፍሎች በማእከላዊ ኰሚቴው
ውስጥ የበላይነት እንዲኖራቸው ይጥር ነበር ። በዚህ ጥያቄ ላይ የኮንግ
ረሱ አብዛኛው ክፍል ሌኒንን ደገፈ ። የተመረጡት የማዕከላዊ ኰሚቴው
አባሎች የሌኒን ደጋፊዎች ነበሩ ።

በሌኒን አስተሳሰብ ላይ በመመሥረት ሌኒን ፣ ፕሌክሀኖቭና ማርቶቭ
ለሥነ-ጽሁፍ ቦርድ ማለትም ኢስክራን ለማዘጋጀት ተመረጡ ። አብዛኛ
ዎቹ የማርቶቭ ተከታዮች የነበሩት ስድስት የቀድሞ የኢስክራ ቦርድ አባ
ሎች እንዲመረጡ ማርቶቭ ሃሳብ አቀረበ ። ሆኖም አብዛኛው የኮንግ
ረሱ አባላት የማርቶቭን ጥያቄ ተቃወሙት ። በሌኒን የቀረቡት ሶስቱ በኰ
ንግረሱ ተመረጡ ። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ማርቶቭ በማዕከላዊ አካል የሥነ-
ጽሁፍ ቦርድ ውስጥ እንደማይሳተፍ አስታወቀ ።

ስለሆነም ፣ በፓርቲው ማዕከላዊ ተቋም ውስጥ በነበረው ድምጽ
ኮንግረሱ የማርቶቭንና የተከታዮቹን ድል መምታትና የሌኒንን ተከታ
ዮች አሸናፊነት አረጋገጠ ።

ከዚያን ጊዜ ጀምሮ በኮንግረሱ ውስጥ አብዛኛውን ድምጽ በማግ
ኘት የተመረጡት የሌኒን ተከታዮች ቦልሼቪክ ተብለው ሲጠሩ (ቃሉ
ከቦልሼንስትቮ የመጣ ሲሆን ብዙሀን ማለት ነው) እንዲሁም አነስተኛ
ድምጽ ያገኙት የሌኒን ተቃዋሚዎች ሜንሼቪክ ተብለው ተጠሩ (ቃሉ
ከሜንሼንስቶቮ የመጣ ሲሆን ንዑሳን (ጥቂቶች) ማለት ነው ።



የሁለተኛው ኮንግረስ ተግባር ሲገመገም የሚከተሉት መደምደ
ሚያዎች ላይ መድረስ ይቻላል ።

1. ኮንግረሱ በ «ኢኮኖሚስቶች» ፣ በእውቅ አድርባዮች ላይ ማር
ክሲዝም ድል መቀዳጀቱን አረጋገጠ ።

2. ኮንግረሱ መርሀ-ግብሩንና ሕጐችን አጸደቀ ፣ የሶሻል ዲሞክ
ራቲክ ፓርቲን መሠረተ ፣ እንዲሁም ለብቸኛ ፓርቲ መሰረት ጣለ ።

3. ኮንግረሱ ፓርቲውን ቦልሼቪክና ሜንሼቪክ በሚል ሁለት
ክፍሎች በከፈለው የድርጅት ጥያቄ ላይ ያለውን ሰፊ ልዩነት አጋለጠ ።
የቦልሼቪኰች የአብዮታዊ ሶሻል ዲሞክራሲ ድርጅታዊ መመሪያ አሸ
ናፊ ሲሆን ሜንሼቪኮች ግን በድርጅታዊ ልልነትና የአድርባይነት ማጥ
ውስጥ ተዘፈቁ ።

4. ኮንግረሱ የጥንት አድርባዮች ማለትም በፓርቲው የተቶፉት
«ኢኮኖሚስቶች» በዘመናዊ አድርባዮች በሜንሼቪኮች እንደተተኩ
አሳየ ።

5. ድርጅቱን አስመልክቶ ኮንግረሱ ተመጣጣኝ አቋም ሳይወስድ
በመሀል ሲያወላውል ታይቷል ።
በአንዳንድ ሁኔታ ለሜንሼቪኰች የበላይነትን ሰጥቷል ። ምንም እንኳን
በመጨረሻው ገደማ ራሱን ማረም ቢችልም በድርጅት ተግባር ላይ የሜን
ሼቪኰችን አድርባይነት ለማጋለጥ አልቻለም ከፓርቲውም ለመነጠል
ወይንም እንደዚህ ያለውን ሥራ ለፓርቲው አላቀረበም ።

ይህ የመጨረሻው ሁኔታ በቦልሼቪክና በሜንሼቪክ መሀል የሚደ
ረገው ትግል ከኮንግረሱ በኋላ እየለዘበ ከመሄድ ርቆ ይበልጥ እየከረረና
እየሰላ ለምን እንደመጣ ከዋነኞቹ ምክንያት ውስጥ አንዱን አረጋገጠ ።

4/ <u>የሜንሼቪክ መሪዎች የመከፋፈል እንቅስቃሴና ከሁለተኛው
ኮንግሬስ በኋላ ውስጠ ፓርቲ ትግሉ እየሠላ መምጣቱ ፤ የሜንሼ
ቪኮች አድርባይነት ፤ «አንድ እርምጃ ወደፊት ሁለት እርምጃ
ወደኋላ» የተሰኘው የሌኒን መጽሐፍ ፤</u>

የማርክሳዊ ፓርቲ ድርጅታዊ መርሆች ፤

ከሁለተኛው ኮንግሬስ በኋላ ውስጠ ፓርቲ ትግሉ ከመቼውም ጊዜ
ይበልጥ እየናረና እየሰላ መጣ ። ሜንሼቪኮች ሁለተኛው ኮንግሬስ ያሳለ
ፈውን ውሳኔ ለማደናቀፍና የፓርቲውን ማእከላዊ ተቋም ለመያዝ የሚቻ
ላቸውን ሁሉ አደረጉ ። በኢስክራ ሥነ-ጽሁፍ ውስጥ የበላይነትን እንዲ
ይዙና በፓርቲው ማእከላዊ ኰሚቴም ውስጥ ከቦልሼቪኮች ቁጥር እኩል
የሚያደርጋቸውን አባሎች እንዲወከሉ ጠየቁ ። ይህ ጥያቄ የሁለተኛውን
ኮንግሬስ ውሳኔ ርቱዕ በሆነ መንገድ ይቃወመዋልና ቦልሼቪኰች ይህንን

ጥያቄ በሚገባ አወገዙ ። ከዚያን ወቅት አንስቶ ሜንሺቪኮች ሕቡዕ በሆነ መንገድ የራሳቸውን ጸረ-ፓርቲ የአንጃኞች ድርጅት መሠረቱ ። ይህ የአንጃኞች ድርጅት በማርቶቭ ፣ በትሮትስኪና በአክሲልሮድ የሚመራ ሲሆን ፤ ማርቶቭ እንዳለው «ሌኒኒዝምን በመቃወም»የተፈጠረ ነበር ። «ፓርቲውን ለመዋጋት የመረጡት ስልት ሌኒን እንደገለጸው» የፓርቲው አጠቃላይ ተግባርእንዳይቀናጅ ምንጩን ማፍረስ፡ «ሁሉንና ማናቸውንም ነገር መገደብ» ነበር ። እነዚህ ሰዎች ራሳቸውን በሩስያ ሶሻል-ዲሞክራቶች የውጪ ሊግ ውስጥ አጠናከረው ነበር ። ዘጠኝ አሥረኛ የሚሆኑት ከሩስያ አብዮታዊ ተግባር የተለዩ ስደተኛ ምሁራን ሲሆኑ ከዚህ ሥፍራ በፓርቲው ላይ ፣ በሌኒንና በሌኒን ተከታዮች ላይ እሳት ይጭራሉ ።

ሜንሺቪኮች ከፕሌክሀኖቭ በጣም ከፍተኛ ድጋፍ ያገኛሉ ። ምንም እንኳን ፕሌክሀኖቭ በሁለተኛው ኮንግረስ ወቅት አቋሙ ከሌኒን ጋር ቢሆንም ከኮንግረሱ በኋላ ሜንሺቪኮች ለመገንጠሉ ተግባራቸው እንዲሳተፍ ብዙ ጊዜ ስላማከሩትና ስላስፈራሩት ከሜንሺቪኮች ጋር «ሰላም ለማውረድ» ወሰነ ። ፕሌክሀኖቭ የጥንቱ አድርባይ ስህተቶቹ ወደ ሜንሺቪክ እንዲገባ ገፋፉትና ከሜንሺቪኮች ጋር እርቅ እንዲወርድ ከመስበኩ ጀምሮ በአጭር ጊዜ ውስጥ ራሱ የሜንሺቪክ አባል ሆነ ። ፕሌክሀኖቭ ኮንግረሱ ቀደም ሲል ያወገዛቸውን መሳውን የሜንሺቪክ ኢስክራ ቀደምት አዘጋጆች በስነ-ጽሁፍ ቦርድ ውስጥ እንዲገቡ ጠየቀ ። ይሁን እንጂ ሌኒን ይህንን የፕሌክሃኖቭን አስተሳሰብ አልተቀበለውም ። ይሁንና ሌኒን የፓርቲውን ማእከላዊ ኰሚቴ ለማጠናከርና ከዚህ ቦታ በመሆን አድርባዮችን በሚገባ ለመምታት አስቦ በፈቃዱ ከኢስክራ የሥነ-ጽሁፍ ቦርድ ለቀቀ ። የኮንግሬሱን ዓላማ ለመከላከል በራሱ ፍቃድ ፕሌክሀኖቭ የቀድሞዎቹን የሜንሺቪክ የኢስክራ አባሎች በኢስክራ ስነ-ጽሁፍ ቦርድ ውስጥ አስገባቸው ። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ማለትም የኢስክራ 52ኛ እትም መውጣት ከጀመረበት ጊዜ አንስቶ ሜንሺቪኰችም ኢስክራን ወደራሳቸው ልሳን በመለወጥ የራሳቸውን አድርባይ አስተሳሰብ በአምዶቻቸው ላይ ማሰራጨት ጀመሩ ።

ከዚያን ጊዜ ወዲህ የሌኒን ቦልሼቪክ ኢስክራ በፓርቲው ውስጥ ጥንታዊ ኢስክራ በመባል ሲጠራ የሜንሺቪኮች አድርባይ ኢስክራ ደግሞ አዲሱ ኢስክራ በመባል ታወቀ ።

ኢስክራ በሜንሺቪኮች መዳፍ ከተዳሰሰች ወዲህ ጸረ-ሌኒንና ጸረ-ቦልሼቪክ ትግል ማራመድ ጀመረች ። የአድርባይ ሜንሺቪኮችን ፕሮፓጋንዳ በተለይም የድርጅትን ጥያቄ አስመልክታ ጸረ-ሌኒንና ጸረ-ቦልሼቪክ አቋም የምታራምድ ልሳን ሆነች ። ከ «ኢኮኖሚስቶች» ና ከበንዲስቶች ጋር በማበር ሜንሺቪኮች ጸረ-ሌኒንዝም አቋም ሥር በመሰለፍ በኢስክራ አምዶች ላይ ዘመቻቸውን ከፈቱ ። ፕሌክሀኖቭም ቢሆን እርቅ መደረግ አለበት በሚለው አቋሙ ጸንቶ ሊቆይ ከቶ አልቻለም ። ወዲያውኑ



በተቀናበረው ዘመቻ ውስጥ ተሳተፈ ። ይህ ያለ ምክንያት የሆነ አይደለም ። ምንም ይሁን ምንም ከአድርባዮች ጋር የመታረቅ አዝማሚያ ማንጸባረቁ በራሱ በአድርባይነት ማጥ ውስጥ ማዝቀጥ ነውና ። ከዚያማ ምኑ ተነስቶ ምኑ ሊተው በጊጣጊጥ እንደተሸቆጠቆጠ የፈረስ ምስል ያሸበረቁ በድንቃላት ፓርቲው አንድ ወጥ መሆኑን በመቃወም ከኢስክራ አምዶች ይጕ ጉደጉድ ጀመረ ። ነጻ ቡድኖችና ግለሰቦች ፣ ራሳቸውን በፓርቲው ድርጅቶች ውስጥ እንዲያሳትፉ ሳይገደዱ ለፓርቲው ውሳኔ እንዲያስገዙ ሳይገደሉ እራሳቸውን የፓርቲ አባል ማድረግ መቻል አለባቸው ። ፓርቲውን እስከደገፈ ድረስ ማናቸውም ምሁር ፣ «ማናቸውም የስራ ማቆም አድማ ውስጥ የተሳተፈ» «በሠላማዊ ሠልፎች የተካፈለ» «ራሱን» የፓርቲ አባል ማድረግ ይችላል ። ለማናቸውም የፓርቲው ውሳኔ ራሳቸውን አስገዙ ማለት «ፎርማልና ቢሮክራሲያዊነት» ነው ። «ጥቂቱ በብዙሁኑ ፣ የበታች አካል በበላይ አካል ይመሩ ማለት » በፓርቲ አካሎች ፍላጐት ላይ የሚደረግ «ሜካኒካዊ ጭቆና» መላው መሪዎችና ከታች እስከላይ አካል የፓርቲውን ዲስፕሊን በእኩል መጠበቅ አለባቸው ማለት በፓርቲው ውስጥ «ገባርነትን» ማስፈን ሲሆን ፤ «እኛ» የምንፈልገው በፓርቲው ውስጥ ማዕከላዊነት ሳይሆን ግለሰቦችና የፓርቲ ድርጅቶች የፓርቲውን ውሳኔ እንዳይቀበሉ የሚፈቅድ ሥርዓት አልበኛ «የአካባቢ አገዝነትን» ነው በማለት ሜንሺቪኮች በኢስክራ አምዶቻቸው ላይ መስበክ ጀመሩ ።

ይህ የፓርቲን መመሪያና የፓርቲን ዲስፕሊን ዝቅ የሚያደርግ ፣ የምሁራንን ግለኝነት የሚያሞካሽና የስርዓት አልበኞችን የዲስፒሊን ጽንሰ-ሀሳብ የሚያጐላ ከቁጥጥር ውጪ የሆነ የተፈቀደ ድርጅታዊ የፕሮፓጋንዳ ፍቃድ ነው ።

ሜንሺቪኮች ፓርቲው ከሁለተኛው ኮንግሬስ እንዲወጣ ፤ የእድገት ደረጃውም ወደ ጥንታዊ የድርጅት መበታተን ፣ ወደ ጥንታዊ የክበቦች ጠባብ አመለካከት ፣ ወደጥንታዊ ጮርቃ የአሰራር ዘዴዎች ለመመለስ በግልጽ ሲጥሩ ታየ ።

ለሜንሺቪኮች መራርና ወቅታዊ ተቃውሞ ማድረግ የግድ አስፈለገ ። ይህም ተቃውሞ በግንቦት ወር 1904 ዓ.ም. አንድ እርምጃ ወደፊት ፣ ሁለት እርምጃ ወደኋላ በሚለው በሌኒን መጽሐፍ ተገለጸ ።

የሚከተሉት በመጽሐፉ ውስጥ ሌኒን የገለጻቸው መሰረታዊ የድርጅት መመሪያዎች ናቸው ። ለወደፊቱ የቦልሼቪክ ፓርቲ መሰረት የተጣለውምከእነዚሁ መመሪያዎች ነው ።

1/ ማርክሳዊ ፓርቲ የሠራተኛው መደብ አካልና ክፍል ነው ። ይሁን እንጂ የሠራተኛው መደብ ብዙ ክፍሎች አሉት ፤ ስለሆነም ማንኛው የሠራተኛው ክፍል የሠራተኛው መደብ ፓርቲው ተብሎ ሊጠራ አ

ችልም ። ፓርቲውን ከተቀሩት የሠራተኛው መደብ ክፍሎች የሚለየው ተቀዳሚ ደረጃ በሰራተኛው መደብ ውስጥ እንደ አንዱ ክፍል ብቻ ሳይሆን ግንባር ቀደም የንቃ አካል መሆኑ ፣ የሕብረተሰብን ኑሮ እድገት እና የመደብ ትግሉን ሕግጋት እውቀቶች ጠንቅቆ ማወቁ ፣ የሠራተኛው መደብ ማርከሳዊ አካል በመሆኑ የተነሳ የሠራተኛውን መደብ ለመምራትና ትግሉን ለመቀየስ መቻሉ ነው ። ስለሆነም እያንዳንዱ ነጠላ ክፍል (part) ከአጠቃላዩ (whole) ጋር መምታታት እንደሌለበት ሁሉ ፓርቲውም ከሰራተኛው መደብ ጋር መመታታት የለበትም ። ማንኛውም ከሠራተኛው መደብ ጋር በሥራ ማቆም አድማ ተሳታፊ የሆነ ሁሉ የፓርቲ አባል መሆን አለብኝ ብሎ መጮህ አይችልም ። ፓርቲውንና መደቡን ካምታታ የንቃተ-ህሊና ደረጃ ወደ «ሥራ ማቆም አድማ ተሳታፊዎች» ደረጃ ዝቅ ያደርገዋል ። የሠራተኛውን መደብ ግንባር ቀደም ፓርቲ ያወድማል ። ፓርቲ የራሱን ደረጃ ወደ «እያንዳንዱ የአድማው ተሳታፊ» ማድረግ ተግባሩ አይደለም ። የፓርቲው ዓይነተኛ ተግባር ሰፊውን ሠራተኛ ሕዝብ ፥ «እያንዳንዱ የአድማ ተሳታፊ» ወደ ፓርቲው ደረጃ ከፍ ማድረግ ነውና ።

«እኛ የመደብ ፓርቲነን» ይላል ሌኒን «ከሞላ ጐደል በአጠቃላይ መደቡ (በጦርነት ወቅት በተለይ ደግሞ በርስ በርስ የጦርነት ወቅት ፣ በአጠቃላይ መደቡ)—በፓርቲው መመራትና በተቻለም መጠን በቀረበ ሁኔታ ፓርቲውን መከተል ይኖርበታል ። ይሁን እንጂ በካፒታሊዝም ሥር መቼም ቢሆን መቼ የወዝአደሩ መደብ በሙሉ ከግንባር ቀደሙ ድርጅት-ከሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲው የንቃተ-ሕሊናና የትግል ደረጃ ላይ ይደርሳል ብሎ መገመት «ማኒሎቪዝም»ና «ኩቮስቲዝም» ነው ።... በካፒታሊዝም ሥር ሌላው ቀርቶ የሠራተኛ ማኅበራት እንኳን በአጠቃላይ የሠራተኛውን መደብ ሊያቅፉ እንደማይችሉ ማንም ሶሻል ዲሞክራት አይጠራጠርም ። በግንባር ቀደሙና በሰፊው ሕዝብ መሀል ያለውን ልዩነት መዘንጋት የግንባር ቀደሙ ድርጅት ተዘውታሪ ተግባር ሰፊውን የኅብረተሰብ ክፍል ወደ ራሱ ከፍተኛ የእድገት ደረጃ ከፍ ማድረግ መሆኑን መዘንጋት ነው ። ይህ ማለት ደግሞ ራስን ማታለል ፣ ከሚጠብቀን ታላቅ ተግባር መጋረድ ነው ። እንዲሁም እነዚህን ተግባሮች ማጥበብ ነው ።»
(የሌኒን ምርጥ ሥራዎች የእንግሊዝኛ ዕትም ሞስኮ ቅጽ 1 ፤ ገጽ 294)

2/ፓርቲው የሠራተኛው መደብ ግንባር ቀደም ፥ የመደቡ የንቃ አካል ብቻ ሳይሆን ፤ አባሎቹ የሚመሩበት የራሱ ዲሲፕሊን ያለው የሠራተኛው መደብ የተደራጀ አካል ነው ። በዚህም የፓርቲ አባላት በፓርቲው በአንደኛው ድርጅት ውስጥ የግድ አባል መሆን አለባቸው ። የድርጅት ሥርዓት ባይኖረውና በፓርቲው ድርጅቶች በአንዱ ድርጅት ውስጥ ያልተሳተፉ እንዲያው ራሳቸውን የፓርቲ አባል በማድረግ ያወጁ የማናቸውም ሰዎች



ጥርቅም ከሆኑና ካልተደራጁ ፣ ስለሆነም ለፓርቲ ውሳኔዎች ራሳቸውን ያላስገዙ አባላት ካሉት ፓርቲው በምንም ዓይነት የዓላማ አንድነት አይኖረውም ፤ በምንም ዓይነት የአባልቹን የተዋሀደ ተግባር ለማግኘትና ብሎም የወዛደሩን የመደብ ትግል ለመምራት አይችልም ። አንድ ፓርቲ የሠራተኛውን መደብ ተግባራዊ ትግል ሊመራና ወደ አንድ ግብ ማድረስ የሚችለው መላው አባላት በአንድ የጋራ አካል ሥር ሲደራጁና በዓላማ ፣ በተግባርና በዲስፕሊን አንድነት መሰረት ላይ በጽኑ ሲቀናጁ ብቻ ነው ።

ከሜንሼቪኮች በኩል በተሰነዘረው የበዛ ተቃውሞ የተነሳ በርካታ ምሁራን ለምሳሌ ፕሮፌሰሮች የዩኒቨርሲቲና የከፍተኛ ደረጃ ት/ቤት ተማሪዎች ወዘተ . . . . ከፓርቲው ውጪ ሊቆዩ በቅተዋል ። ይህም የሆነበት ምክንያት የፓርቲውን ማንኛቸውንም ድርጅቶች ለመቀላቀል ባለመፈለጋቸው ወይም ፕሌክሀኖቭ በሁለተኛው ኮንግረስ እንዳለው «የአካባቢ ድርጅቶች ውስጥ መሳተፍ ደረጃቸው ዝቅ የሚያደርጋቸው» አድርገው በመገመታቸው ምክንያት—በፓርቲው በአንዱ ድርጅት ውስጥ መሳተፍ ካልፈለጉ በፓርቲው ውስጥ ስፍራ ላያገኙ ነው ሲሉ ተቃወሙ ። የማይችሉትን ድንጋይ ማንሳት መልሶ በራስ ላይ መጣል ነው እንዲሉ ሜንሼቪኮች ያነሱት ተቃውሞ መልሶ ራሳቸውን በሚገባ መታቸው ። አንድ ፓርቲ የፓርቲውን ዲሲፕሊን የሚሸሽና በፓርቲው ድርጅት ውስጥ ለመሳተፍ የሚፈራ ማንኛውም ለአባልነት አይፈልገውም ። ሠራተኞች ዲስፕሊን አያስፈራቸውም ። የድርጅት ተሳትፎም አያስበረግጋቸውም ። አእምሮአቸውን ለፓርቲ አባልነት ብቁ አርገው ካዘጋጁ በፍላጐታቸው ድርጅት ውስጥ ይሳተፋሉ ። ግን ስብአዊ ምሁራን ብቻ ናቸው ዲሲፕሊንንና ድርጅትን የሚፈሩት ። በርግጥም እነዚህ ሰዎች ከፓርቲው ታላቅ ጠቀሜታ ውስጥ የተወገዱ ስፍራ የማይሰጣቸው ይሆናሉ ። ይሁን እንጂ ይህ ሁሉ ለፓርቲው ታላቅ ጠቀሜታ አለው ። በዚያን ወቅት ማለትም የቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት በተቀጣጠለበት ወቅት በሚገባ የታወቁ ያልተረጋጉ ክፍሎች ወደ ፓርቲው በመጉረፍ አደጋ ከማድረሳቸው በፊት ፓርቲው እንዲጠነቀቅ ያደርገዋል ።

ሌኒን ሲጽፍ «ፓርቲው የድርጅቶች አጠቃላይ ድምር—ሂሳባዊ ድምር ሳይሆን ውስብስብ—ነው ብዬ ስናገር . . . . . ለማለት የፈለኩትን በግልጽና በትክክል በማብራራት አስረድቼአለሁ ። የኔ ዓላማ ፓርቲው የመደቡ ግንባር ቀደም አካል እንደመሆኑ በተቻለ መጠን ሁሉ የተደራጀ መሆን አለበት ። ፓርቲው የአባልነት ሥፍራ የሚሰጠው ቢያንስ ራሱን ለፓርቲው የአስገዙትን ክፍሎች ብቻ መሆን ይገባዋል ። . . . .»

«የማርቶቭ አቀማመር የወዝአደሩን ሰፊ የሕብረተሰብ ክፍል ዓይነተኛ ፍላጐት የሚያስጠብቅ ይምስል እንጂ የወዝአደሩን ዲሲፕሊንና ድርጅት በመፍራት የሚዋጉትን የቡርዧ ምሁራን ጥቅም የሚያስጠብቅ ነው ። በዘመናዊ የካፒታሊዝም ሕብረተሰብ ውስጥ ምሁራንን የተለዩ ክፍል የሚያደርጋቸው ግለኝነታቸውና ለዲሲፕሊንና ለድርጅት ብቁ

አለመሆናቸው መሆኑን ማንም ሰው መካድ አይችልም ። »

(ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ፡ ገጽ 288 - 99)

በሌላም በኩል ፡—

«ወዝ አደሮች ድርጅትና ዲስፕሊን አይፈሩም ። . . . . ወዝአደሮች ድርጅት ውስጥ ሊገቡ የማይፈልጉትን ገና ለገና በድርጅቱ ቁጥጥር ስር ሆነው ይሰራሉ በማለት መልካም ግምት ያላቸውን ፕሮፌሰሮችና የከፍተኛ ትምህርት ቤት ተማሪዎች ማግኘት ለወዝአደሮች አንዳችም ጠቀሜታ አይኖረውም ። በፓርቲያችን ውስጥ ልምድ የሚያጥራቸው ወዝአደሮች ሳይሆኑ አንዳንድ ምሁራን ናቸው» (ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ፡ ገጽ 322)

3/ ፓርቲው የሠራተኛው መደብ የተደራጀ አካል ብቻ አይደለም ፤ ነገር ግን ከድርጅቶች ሁሉ ከፍተኛው የድርጅት መልክ ነው ። እንዲሁም በዙሪያው የተሰባሰቡትን የሠራተኛውን መደብ ድርጅቶች ሁሉ የመምራት ተልዕኮ አለበት ። ትልቁ የድርጅት መልክ እንደመሆኑ መጠን በመጠቀ ንድፈ-ሀሳባዊ ግንዛቤ የታጠቀ ፣ የመደብ ትግሉን ሕግጋት እውቀት ጠንቅቆ ያወቀ ፣ ከአብዮታዊ ንቅናቄ ከፍተኛ ልምድ ያካባቱ የመደቡን ምርጥ አባላት የሚያቅፍ መሆን አለበት ። ፓርቲው ሌሎች የሠራተኛው መደብ ድርጅቶችን የመምራት እድል ባጋጠመው ጊዜ የመምራት ግዴታ አለበት ። ሜንሼቪኮች የፓርቲውን የመምራት ሚና ዝቅ በማድረግና በማንኳሰስ በፓርቲው የሚመሩትን መላውን የወዝአደሩን መደብ ድርጅቶች ለማዳከምና ብሎም ወዝአደሩ «ለሥልጣን በሚያደርገው ትግል ካለድርጅት በቀር ሌላ አንዳችም መሣሪያ እንደሌለው ሁሉ» ይህንን ለማዳከምና ትጥቁን ለማስፈታት ይጥራሉ ።

4/ ፓርቲው በሚሊዮን ከሚቆጠረው የሠራተኛው መደብ ጋር የተሳሰረ ግንባር ቀደም አካል ነው ። ፓርቲው የቱንም ያህል ግንባር ቀደም ቢሆን ፣ የቱንም ያህል በሚገባ የተደራጀ ቢሆን የፓርቲ አባል ካልሆኑት ሰፊ ሕዝብ ጋር በሚገባ ካልተዋሀደ ፣ የጠበቀ ግንኙነት ከሌለው ግንኙነቱንም ከዕለት እለት ካላጠናከረና ካላዳበረ ሕልውናም ሆነ እድገት አይኖረውም ። በራሱ ክልል ውስጥ ራሱን የመሸገ ፣ ከሰፊው ሕዝብ ራሱን ያገለለና ደካማ ወይም የሚዝናና ፓርቲ ከመደቡ ጋር ያለው ግንኙነት እየላላና እየተዳከመ በመሄድ የሰፊውን ሕዝብ ድጋፍና እምነት ያጣል ። በመጨረሻም በርግጥ እንዲጠፉ ይገደዳል ። እስከመጨረሻው ግብ መዝለቅ እንዲችልና እድገት እንዲኖረው ከተፈለገ ፓርቲው በሰፊው ሕዝብ መሀል ያለውን የውህደት ደረጃ ከጊዜ ወደ ጊዜ በጣም ማሳደግና በሚሊዮን የሚቆጠረውን የመደቡን አባላት ማትረፍ አለበት ።

«የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ለመሆን ከተፈለገ» ይላል ሌኒን «የመደቡን ትክክለኛ ድጋፍ ማግኘት አለብን»

(ሌኒን ስብስብ ስራዎች የራሺያ ዕትም ቅጽ 6 ፡ ገጽ 208)

5/ የፓርቲውን ተግባር በትክክል ለማከናወንና ሰፊውን ሕዝብ ዘዴአዊ በሆነ መንገድ በትግሉ ውስጥ ለምመራት ፓርቲው በማዕከላዊ



ነትና ሰፊውን ሕዝብ ዘዴአዊ በሆነ መንገድ በማዕከላዊነት መመሪያ ፣ በአንድ የፓርቲ ሕጎች ፣ በአንድ ዓይነት የፓርቲ ዲሲፕሊን ፣ በአንድ መሪ አካል በፓርቲው ኮንግሬሶች መሀል ደግሞ በፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ ፤ ጥቂቶች ለብዙሀኑ ፣ የተለያዩ ድርጅቶች ለማእከሉ ፣ የበታች ድርጅቶች ራሳቸውን ማስገዛት አለባቸው ። ይህን ሁኔታ ካላሟላ የሠራተኛው መደብ ፓርቲ ለመሆንና መደቡንም የመምራት ተግባር ማካሄድ ይሳነዋል ።

በርግጥ በዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ሥር ፓርቲው ራሱን በሕቡዕ በማደራጀት ይሠራል ። እንደዚህ ባለ ሁኔታ ውስጥ በሚገኝበት ወቅት ከታች በሚደረግ የምርጫ መመሪያ መሰረት መገንባት አይቻልምና ፓርቲው እጅግ ጠንካራና ሚስጢራዊ መሆን ይኖርበታል የሚል መደምደሚያ መስጠት ይቻላል ። ይሁን እንጂ ሌኒን እንዳስገነዘበው ይህ በፓርቲያችን ሕይወት ውስጥ የተከሰተ ጊዜያዊ ገጽታ የዛሩ አገዛዝ እንደተወገደ ወዲያውኑ የሚቀየር ሁኔታ ነው ። ፓርቲው ግልጽና ሕጋዊ በሚሆንበት ወቅት የፓርቲ ድርጅቶች በዲሞክራሲያዊ ማእከላዊነት መመሪያ መሰረት ዲሞክራሲያዊ በሆነ ምርጫ ይገነባሉ ።

«ቀደም ሲል» ይላል ሌኒን ሲጽፍ «ፓርቲያችን የተለያዩ ቡድኖች ድምር እንጂ በአንድ መልክ የተደራጀ ባለመሆኑ በነዚህ ቡድኖች መሀከል ከርእዮተ-ዓለም ተጽእኖ ሌላ አንዳችም ግንኙነት ማድረግ አይቻልም ነበር ። አሁን የተደራጀ ፓርቲ ሊሆን በቅቷል ። ይህ ደግሞ የሥልጣን መመሥረትን ፣ የሀሳብ ሀይል ወደ ሥልጣን ሀይል መተላለፉን ፣ ዝቅተኛ የፓርቲ አካሎች ለበላይ የፓርቲ አካሎች መገዛታቸውን ያመለክታል»

(ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ ፡ 291)

የሜንሼቪኮችን ድርጅታዊ ጭፍን ያምላሾች የተለየ ድምሰሳ ፣ ለፓርቲው ሥልጣንና ዲሲፕሊን ራሳቸውን ስለአለማስገዛታቸው መሣፍንታዊ ሥርዓተ-አልበኝነት ሌኒን ሲጽፍ ፤

«ይህ መሣፍንታዊ ሥርዓተ-አልበኝነት የሩስያ ጭፍን ያምላሾች የተለየ ባሕርይ ነው ። የፓርቲውን ድርጅት እንደ አንድ አስፈሪ ግዙፍ ‘ፋብሪካ’ አድርገው ይቆጥሩታል ። አንዱ አካል ለአጠቃላዩ ፡ ጥቂቱ ለብዙሀኑ ራሱን የማስገዛትን ሥርዓት እንደ ‘ገባርነት’ ይቆጥሩታል ።... በተለያዩ ክፍሎች የሚደረጉትን የሥራ ክፍሎች በማየት ‘ሰዎች ወደ ተነጣጠለ ግዑዝ መኪና’ ተቀየሩ እያሉ አስገራሚ ጩኸት ያሰማሉ ። የፓርቲውን ድርጅታዊ ሕጎች እየጠቀሱ አቀራረባቸውን በመሸፈን አንድ ሰው ሕጎችን ሊያስወግድ ይችላል የሚል ወራዳ ገለጻ ያደርጋሉ »

(ሌኒን ምርጥ ስራዎች የእንግሊዝኛ እትም ሞስኮ 1047 ፡ ቅፅ1 ፡ ገፅ 324)

6/ በተግባራዊ ተሳትፎ ውስጥ የአባሎችን አንድነት ለማትረፍ ከተፈለገ ፓርቲው የጋራ የሆነ ወዝአደራዊ ዲሲፕሊን እንዲቀበሉ ማድረግና አባሎቹን በሙሉ ከታች እስከላይ አመራሩንም ጭምር በእኩልነት ማስተባበር ይኖርበታል ። በዚህም የተነሳ የፓርቲው ዲሲፕሊን የማይነካቸው «ጥቂት ምርጦች» ና የፓርቲው ዲሲፕሊን የሚጫንባቸው «ብዙ

ሆን» በማለት በፓርቲው ውስጥ መከፋፈል አይፈጠርም ። ይህ ሁኔታ ያልተሟላ እንደሆን የፓርቲው ውህደትና የአባላቱም አንድነት የተጠበቀ ሊሆን ከቶም አይችልም ።

«ኰንግሬሱ የመረጣቸውን የሥነ-ጽሁፍ ቦርድ አባሎች በመቃወም ማርቶቭና ተከታዮቹ የሚያደርጉት የተቃውሞ ክርክር» ይላል ሌኒን ሲጽፍ «እኛ ገባሮች አይደለንም በሚሉት ከሁሉም በላይ በራሳቸው አሸብራቂ ቃላቶች በሚገባ ተጋልጠዋል» ከሕዝባዊ ድርጅቶችና ከሰፊው ሕዝብ ዲሲፕሊን በላይ የቆሙ ጥቂቶቹ ምርጦች ማለትም የቡርዧ ምሁራን አስተሳሰብ እዚህ ላይ በሚገባ ተገልጿል ። ለእያንዳንዱ ምሁር መላው የወዝአደሩ ድርጅትና ዲሲፕሊን «ገባርነት» ነው ። . . . . . . . .
(ሌኒን ስብስብ ሥራዎች የራሺያ እትም ቅፅ 6 ገፅ 282)

«እውነተኛውን ፓርቲ ለመገንባት ወደፊት ስናመራ የመደቡ የንቃ ሠራተኛ አናርኪስት ሐረጐችን በድፍረት ከሚያራግቡት ከቡርዧው ምሁራን አስተሳሰብ የወዝአደሩን ሠራዊት አስተሳሰብ መለየትን መማር አለበት ። የፓርቲ አባላት ተግባር ሊሟላ የሚችለው ከታች ባሉት አካላት ብቻ ሳይሆን 'በእናት ላይ ባሉትም ሰዎች' ጭምር መሆኑንና ማሳሰብን መማር ይገባዋል» ።
(ሌኒን ምርጥ ሥራዎች የእንግሊዝኛ እትም ሞስኮ 1947 : ቅፅ 1 : ገፅ 326)

የዚህን ልዩነት ትንተና በማዳመርና የሜንሼቪኰችን «በድርጅት ሁኔታ የአድርባይነት አቋምን» በማብራራት ሌኒን ሜንሼቪዝምን አዘቅት ውስጥ የከተተው ወንጀል ወዝአደሩ ለራሱ ነጻ መውጣት በሚያደርገው ትግል ዓይነተኛ መሣሪያ የሆነውን የፓርቲ ድርጅት አስፈላጊነት ዝቅ ከማድረጋቸው ላይ የሚያርፍ ነው በማለት ተናግሯል ። ሜንሼቪኮች የወዝአደሩ የፓርቲ ድርጅት ለአብዮቱ ድል ማድረግ ይሄን ያህል ትልቅ ጠቀሜታ የለውም በማለት ሲያራምዱ ፣ ከሜንሼቪኮች በተቃራኒ ሌኒን የወዝአደሩ ርእዮተ-ዓለማዊ አንድነት ብቻውን ለድል በቂ አይደለም ፤ ድልን ለመቀዳጀት በወዝአደሩ «ቁሳዊ የድርጅት አንድነት» አማካይነት ርእዮተ ዓላማዊ ሕብረት «መጠናከር» ይኖርበታል ብሏል ። ይህ ሲሟላ ብቻ ነው ሌኒን እንዳለው ወዝአደሩ የማይበገር ሀይል ሊሆን የሚችለው ።

«ሌኒን ሲጽፍ» «ለሥልጣን በሚደረገው ትግል ወዝአደሩ ከድርጅቱ በቀር ሌላ ምንም መሣሪያ የለውም ። በሥርዓተ አልበኛ የቡርዧው የውድድር ዓለም እንዳይተባበሩ የተደረጉት ፣ በወረት ተገደው እንዲሰሩ የተጨፈለቁት ፣ በማያቋርጥ ሁኔታ ወደ አሰቃቂ የእርዛት ደረጃ አረማዊነትና ወራዳነት የተጣሉት ወዝአደሮች በማያጠራጥር ሁኔታ የማይበገር ሀይል መሆን የሚችሉት ርእዮተ-ዓለማዊ አንድነታቸው በማርክሲዝም መርሆ መሰረት ሲጠናከርና በሚሊዮን የሚቆጠሩ ምዝብሮችን ወደ ወዝአደሩ መደብ ሠራዊትነት ሊመለወጥ የሚያስችለው የቁሳዊ ድርጅት አንድነታቸው ሲጠናከር ብቻ ነው ።» ብሏል (ከላይ በተጠቀሰው መፅሐፍ፣ ገፅ 340)

በእነዚህ እርከ. ቃላት ነበረ ሌኒን መጽሐፉን ያጠቃለለው ።



በዚህም ነበር እንግዲህ አንድ እርምጃ ወደፊት ሁለት እርምጃ ወደኋላ በሚለው እውቅ መጽሐፉ ሌኒን የድርጅትን መሰረታዊ መመሪያዎች ያስቀመጠው ።

የዚህ መጽሐፍ አስፈላጊነት በተቀዳሚ የሚያርፈው አሸናፊ የሆነውን የፓርቲ መመሪያ በመንደፍ የጠባብ ቡድን መመሪያን በመቃወሙና ፤ የፓርቲ መመሪያ በማንሳት በታኞችን በሚጻረሩ ማለትም በድርጅት ጥያቄ ላይ የሜንሼቪኮችን አድርባይነት በመደርመሱና ለቦልሼቪክ ፓርቲ ድርጅታዊ መሠረት በመጣሉ እውነታ ላይ ነው ።

ይሁን እንጂ መጽሐፉ ተጠቃሚነቱን አላጣም ። የዚህ መጽሐፍ ታሪካዊ ጠቀሜታ የሚያሳየን ሌኒን በማርክሲዝም ታሪክ ውስጥ ለመጀመሪያ ጊዜ ፓርቲው የወዝአደሩ መሪ ድርጅት ፣ የወዝአደሩ ዓይነተኛ መሣሪያ መሆኑን፣ ያለዚህ መሣሪያ የወዝአደሩ አምባገነንነትን ለመመሥረት የሚደረገው ትግል በምንም ዓይነት ለድል እንደማይበቃ በማስረዳት የሚያስተምር የፓርቲ መመሪያ በማብራራቱ መሰረት ላይ የተገነባ ነው ።

አንድ እርምጃ ወደፊት ፣ ሁለት እርምጃ ወደኋላ የሚለው የሌኒን መጽሐፍ ለፓርቲው ሠራተኞች መዳረሱ የአካባቢ ድርጅቶች በሌኒን ዙሪያ እንዲሰባሰቡ አድርጓቸዋል ።

ነገር ግን ድርጅቶች ይበልጥ ቦልሼቪኰችን እየቀረቡ በዙሪያቸው እየተሰባሰቡ በሄዱ ቁጥር የሜንሼቪክ መሪዎች ባሕርያት ይበልጥ መሰሪ እየሆኑ መጡ ።

በ1904 ዓ.ም. የበጋ ወራት ፕሌክሀኖቭ ላደረገው ብርቱ ድጋፍና ለሁለት ሞራላቸው ለወደቀ የቦልሼቪክ አባላት ክራሲኒና ኖስኩቭ ክሕደት ምስጋና ይግባውና ሜንሼቪኰች የማዕከላዊ ኩሚቴውን አብዛኛውን ስፍራ ሊይዙ በቁ ። ሜንሼቪኮች እንደሆኑ ፓርቲውን ለመከፋፈል እየተሯሯጡ መሆናቸው ሳይታለም የተፈታ ነበር ። ማዕከላዊ ኩሚቴውንና ኢስክራን የመሰለ ቁልፍ አካል ማጣታቸው ቦልሼቪኰችን እጅግ አስቸጋሪ ሁኔታ ላይ ጣላቸው ። ቦልሼቪኰችም የራሳቸውን ጋዜጣ ማዘጋጀት ግድ ሆነባቸው ። ስለሆነም አዲስ ማዕከላዊ ኩሚቴ ለመፍጠርና ከሜንሼቪኰች ጋር ያለውን ልዩነት ፈርጅ ለማስያዝ አዲስ የፓርቲ ኮንግረስ—ሶስተኛውን ኮንግረስ ማዘጋጀቱ የማይዘሉት ግዴታ ሆኖ አገኙት ።

በሌኒን የሚመሩት ቦልሼቪኰች የወቅቱ አንገብጋቢ ተግባራቸው መሆኑን በሚገባ ተገንዘበው ሥራውን ጀመሩ ።

ሶስተኛው ኮንግረስ እንዲደረግ በመደገፍ ከያሉበት ዘመቻ በማካሄድ በነሐሴ 1904 ዓ.ም. 22 የቦልሼቪክ አባላት የተገኙበት ስብሰባ በስዊዘርላንድ ውስጥ ተደረገ ። ይህ ስብሰባ «ለፓርቲው» ጥሪ እንዲደረግ ወሰነ ። ጥሪው ለቦልሼቪኰች ሶስተኛውን ኮንግረስ ለመጥራት በሚያደርጉት ትግል ውስጥ እንደመርሀ-ግብር ጠቀማቸው ።

በሶስት አካባቢዎች የቦልሼቪክ ኰሚቴዎች ባደረጉት ስብሰባ (በደቡብ ፣ በካውካስያንና በሰሜን) ለሶስተኛው የፓርቲ ኮንግረስ ተግባራዊ ዝግጅት የሚያደርጉ የብዙሆን ኰሚቴዎች ተመረጡ ።

በሐምሌ 4 ቀን 1905 ዓ.ም. የመጀመሪያው የቦልሼቪክ ጋዜጣ ቪፒርዩድ (ወደፊት) ታትሞ ወጣ ። ስለሆነም በፓርቲው ውስጥ እያንዳንዳቸው የራሳቸውን ማዕከላዊ አካልና የራሳቸውን ልሳን የሚያወጡ ሁለት የተለያዩ ክፍሎች ተፈጠሩ ። እነርሱም ሜንሼቪኰችና ቦልሼቪኰች ነበሩ ።

## አ ጭ ር ድ ር ሞ ፤

ከ1901—04 ዓ.ም. የሰራተኛው መደብ ንቅናቄ ከማደጉ ጋር የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቲክ ድርጅቶች ጥንካሬ እየጨመረ ሄደ ። «በኢኮኖሚስቶች» ላይ የሚደረገው አድካሚ የመስመር ትግል የሌኒንስት ኢስክራ አብዮታዊ መስመር ድልን ተጐናጸፈ ፣እንዲሁም ርዕዮተ-ዓለማዊ ውኸርንብርና «ጮርቃ የአሰራር ዘዴዎችን» መቋቋም ተቻለ ።

ኢስክራ የተበታተኑትን የሶሻል ዲሞክራቲክ ክበቦች ፣ ቡድኖች በማግኘት ለሁለተኛው የፓርቲ ኮንግረስ መጠራት ጥርጊያ ጐዳና ከፈተ ። ሁለተኛው ኮንግረስ በ1903 ተደርጐ የሩሲያ የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ተመሰረተ ፣ የፓርቲው መርሀ-ግብርና ሕጐች ጸደቁ ፣ የፓርቲው መሪ አካል ተመረጠ ።

በሁለተኛው ኰንግረስ ውስጥ የኢስክራን አሸናፊነት ለማረጋገጥ በተደረገው ትግል በሩ.ሶ.ዴ.ሠ.ፓ ውስጥ ሁለት ቡድኖች ተከሰቱ ። ቦልሼቪኰችና ሜንሼቪኮች ።

ከሁለተኛው ኩንግረስ በኋላ በሜንሼቪኮችና በቦልሼቪኰች መሀከል የነበረው ዓይነተኛ ልዩነት በድርጅት ጥያቄ ላይ ያተኰረ ነበር ።

ሜንሼቪኰች ወደ «ኢኮኖሚስቶች» እየተገፉ መጥተው በፓርቲው ውስጥ የነርሱን ቦታ ወሰዱ ። ለጊዜው የሜንሼቪኰች አድርባይነት በድርጅት ጥያቄ ራሱን አጐላ ። ሜንሼቪኮች ሌኒን የሚለውን ዓይነት ጠንካራና አስተማማኝ ፓርቲ በጽኑ ተቃወሙ ። እነርሱ የሚፈልጉት ደካማ (የላላ) ያልተያራጀና ኩቮቲስት የሆነ ፓርቲ ነበር ። የፓርቲውን አመራር ለመከፋፈል ከፍተኛ ጥረት አድርገዋል ። በፕሌክሀኖቭ ከፍተኛ ድጋፍ ኢስክራንና ማዕከላዊ ኰሚቴውን በመዳፋቸው ካስገቡ በኋላ ለራሳቸው ዓላማ ፡— ፓርቲውን ለመከፋፈል በሚገባ ተጠቀሙበት ።

ሜንሼቪኰች ለመከፋፈል እንደሚቅበዘበዙ በማየት ቦልሼቪኰች ከፋፋዮችን ለመቋቋም እርምጃ መውሰድ ተገደዱ ። የአካባቢ ድርጅቶችን ለሶስተኛው ኮንግረስ ለመጥራት የራሳቸውን ጋዜጣ ቪፔርዩድ ማዘጋጀት ጀመሩ ።

ስለሆነም በመጀመሪያው የሩሲያ አብዮት ዋዜማ የሩስያና የጃፓን ጦርነት እንደተጀመረ ሜንሼቪኰችና ቦልሼቪኰች እንደሁለት የተለያዩ የፖለቲካ ቡድኖች ሆነው ይታዩ ነበር ።



ምዕራፍ ሶስት

# ሜንሸቪኮችና ቦልሼቪኰች በሩሲያና በጃፓን ጦርነት ወቅት የመጀመሪያው የሩሲያ አብዮት

(1904—1907)

## 1. የሩስያና የጃፓን ጦርነት ፣ በሩስያ ውስጥ አብዮታዊ ንቅናቄ ይበልጥ እያደገ መምጣቱ ፤ በቅዱስ ፒተርስበርግ የሥራ ማቆም አድማ፣ጥር 9፣ 1905 ዓ.ም. በክረምቱ ቤተመንግስት ፊት ለፊት የተደረገው የሠራተኞች ሰላማዊ ሰልፍ እየተጋጋለ መሄዱ ፤ የአብዮቱ ፍንዳታ

በአሥራ ዘጠነኛው ምዕተ-ዓመት መጨረሻ ኢምፔሪያሊስት አገሮች የፓስፊክ ሙሉ ተቆጣጣሪነት ለማረጋገጥና ቻይናን እንደ ቅርጫ ሥጋ ለመቀራመት መራራ ትግል ማድረግ ጀመሩ ። ዛሪስት ሩሲያም ብትሆን ከዚህ ቅርጫ ለመሳተፍ የዱለታው ተባባሪ ነበረች ። ከ1900 ዓ.ም. የዛሩ ሠራዊት ከጃፓን ፣ ከጀርመን ከፈረንሳይና ከእንግሊዝ ሠራዊቶች ጋር በመደመር የቻይና ምዝብር ሕዝብ ለጸረ-ኢምፔሪያሊስት ትግላቸው ያደረጉትን ከፍተኛ መነሳሳት በማይመጣጠን አረመኔያዊ ጭፍጨፋ አዳፈኑት ። ይህ ሁኔታ ከመሆኑ ቀደም ብሎ እንኳ የዛሩ አገዛዝ ቻይና የሊያኦቱንግን ልሳነ-ምድር ከአርተር ወደብ ምሽጐች ጋር ለሩሲያ እንድትሰጥ ጠይቃ ነበር ። ሩሲያ በቻይና ግዛት ክልል ውስጥ የባቡር ሀዲድ ለመዘርጋት በመቻሏ ፣ ይኸው ሀዲድ በሰሜናዊ ማንቹሪያ ፡— የቻይና ምሥራቃዊ የባቡር ሀዲድ ተዘረጋ ። የሩሲያ ወታደሮችም የሀዲዱን ደህንነት ለመጠበቅ በአካባቢው ሰፈሩ ። ሰሜናዊ ማንቹሪያ በዛሩ ወታደሮች ይዞታ ወደቀች ። የዛሩ አገዛዝ መች በዚህ ብቻ ረክቶ ወደ ኰሪያም ገሰገሰ ። የሩሲያ ቡርዧ በማንቹሪያ ውስጥ «ብጫ ሩስያ» ለመመሥረት ንድፍ ያወጣ ነበር ።

የዛሩ አገዛዝ በሩቅ ምስራቅ ውስጥ ግዛት ለማስፋፋትና ለዝርፊያ ከምትቅበዘበዘው ፤ በአጭር ጊዜ ውስጥ ኢምፔሪያሊስት አገር ለመሆን ከበቃችውና በኤስያ አሕጉር ፣ በመጀመሪያ ደረጃ የቻይናን ግዛት ለመ

ውረር ከምትፈልገው ጃፓን ጋር ግጭት ፈጠረ ። እንደ ዛራዊት ሩሲያ ሁሉ ጃፓንም እጆቿን በኰሪያና በማንቹሪያ ላይ ለማሳረፍ ከፍተኛ ፍላጐት ነበራት ። በዚያን ወቅት ጃፓን ሻክህሊንና የሩሲያን ሩቅ ምስራቅ ፣ ለመያዝ አለመች ። በሩቅ ምስራቅ ውስጥ እያደገ የመጣው የዛሪስት ሩስያን መጠናከር የፈራችው ታላቋ ብሪታኒያ በሚስጢር ከጃፓን ጐን ተሰለፈች ። በሩስያና በጃፓን ጦርነት ለመፈንዳት ሁኔታዎች እየተከማቹ ሄዱ ። አዲስ የገበያ ጥማት ባደረበት ትልቁ ቡርዧና ይበልጥ አድሀሪ በሆኑት የመሬት ከበርቴ መደብ ክፍሎች የዛሩ አገዛዝ ጦርነትን እንዲያካሄድ ተገፋፋ ።

የዛሩ አገዛዝ ጦርነት ማወጁን ሳትጠብቅ ጃፓን እራሷ ጦርነቱን ከፈተች ። ጃፓን በሩሲያ ውስጥ ቀልጣፋ የሥለላ አገልግሎት አላትና ጠላቶቿ (የዛሩ አገዛዝ) ለጦርነት እንዳልተዘጋጁ በቅድሚያ መረጃ ማግኘት ቻለች ። በጥር ወር 1904 ዓ.ም. አንዳችም ለጦርነቱ መነሳቷን ሳታስታውቅ በድንገት የሩስያ ምሽግ የሆነችውን የአርተርግ ወደብ በመውረር በወደቡ ላይ በሰፈረው በሩስያ የባሕር ሃይል (Fleet) ላይ ከባድ አደጋ አደረሰችበት ።

የሩስያና የጃፓን ጦርነት የተጀመረው እንዲህ ባለ ሁኔታ ነበር ።

የዛሩ አገዛዝ ጦርነቱን የራሱን ፖለቲካዊ ሥፍራ የሚያጠናክርና አብዮቱን የሚፈትን ነው ሲል አስቦ ነበር ። ነገር ግን አገማመቱ እርሱ እንዳሰበው አልነበረም ። ከመቼውም ጊዜ ይልቅ የዛሩ አገዛዝ በጦርነቱ ተናወጠ ።

ዝቅተኛ ትጥቅና ልምድ ያለው የሩስያ የጦር ሠራዊት ብቃት በሌላቸውና መንፈሳቸው በላሸቀ ጀኔራሎች እየተመራ ባደረገው ጦርነት በሽንፈት ላይ ሽንፈትን ተከናነበ ።

ካፒታሊስቶች ፣ የመንግስት ባለሥልጣኖችና ጀኔራሎች በጦርነቱ ይበልጥ በለጸጉ ። የግል ሀብትም እየተስፋፋ ሄደ ። ለሠራዊቱ የሚላከው ስንቅና ትጥቅ በጣም ዝቅተኛ ነበር ። ሠራዊቱ የመሳሪያ እጥረት በነበረበት ወቅት በመኪና የተጫኑ የማምለኪያ ምስሎች እንዲቀበል በመደረጉ ፣ ወታደሮቹ ምርር ባለሁኔታ «ጃፓኖች ያነዱናል እኛ ግን ሁሉን ለታቦት ሰጥተናል»እያሉ ይናገሩ ነበር ። ልዩ ባቡሮች የቆሰሉ ወታደሮችን ከጦርነት ሥፍራ በማንሳት ማጋጋዝ ሲገባቸው በዛሩ ጀኔራሎች የተዘረፉ ንብረቶችን እየጫኑ ይሄዳሉ ።

ጃፓኖች የአርተርን ወደብ በመከበብ ሊይዙት በቁ ። የጃፓን ወታደሮች ፡— በመደጋገም በዛሩ ሠራዊት ላይ ከፍተኛ ጉዳት ካደረሱ በኋላ በመጨረሻ በሙክደን አካባቢ የዛሩን ሰራዊት ደመሰሱት ። በዚህ ጦርነት ከ300,000 ያህል ሠራዊት ውስጥ 120,000 ያህሉ ተገደሉ ፣ ቆሰሉ ፣ ተማረኩ ። ይህም ሁኔታ አጠቃላይ ሽንፈትን አስከተለ ። ከባልቲክ የአ



ርተርን ወደብ ለማስለቀቅ የተላከው የዛሩ የባሕር ኃይል በቱሺማ የባሕር ሰላጤ ድል ተመታ ። የቱሺማ ሽንፈት በጣም አሰቃቂ ነበር ። ከተላኩት 20 የጦር መርከቦች ውስጥ አሥራ ሶስቱ ፣ ሰመጡ ወይም ተደመሰሱ አራቱ ተማረኩ ። ዛሪስት ሩስያ በማያጠራጥር ሁኔታ ተሸነፈች ።

የዛሩ አገዛዝ ከጃፓን ጋር አሳፋሪ እርቅ ለማድረግ ተገደደ ። ጃፓን ኰሪያን ስትይዝ እንዲሁም የአርተርን ወደብና የሳክሃሊንን ደሴት በከፊል ከሩስያ ነጠቀች ።

ሕዝቡ ጦርነቱን አልፈለገምና ጦርነቱ ለሀገሪቷ ምን ያህል አስከፊ መሆኑን ተገነዘበ ። ለዛሪስት ሩሲያም ኋላቀርነት ታላቅ አስተዋጽኦ አድርጓል ።

ቦልሼቪኰችና ሜንሼቪኰች ጦርነቱን አስመልክተው የተለያየ አቋም ይዘው ነበር ።

ሜንሼቪኰች ትሮትስኪም ጭምር የዛሩን የመሬት ከበርቴዎችና የካፒታሊስቶችን «አባት አገር» መከላከል በማለት በተከላካይነት አቋም ውስጥ ተዘፈቁ ።

በሌኒን የሚመሩት ቦልሼቪኰች በሌላ በኩል ደግሞ በዚህ የዝርፊያ ጦርነት ላይ የዛሩ አገዛዝ መሸነፍ የዛሩን አገዛዝ እስካዳከመና የአብዮታችንን ሰፈር እስካጠናከረ ድረስ ታላቅ ጠቀሜታ አለው የሚል አቋም ነበራቸው።

የዛሩ ሠራዊት መሸነፍ ሰፊውን ሕዝብ የዛሩ አገዛዝ መበስበሱን በሚገባ እንዲረዳው ዓይኑን ከፍቶለታል ። በዛሩ ላይ ያላቸው ጥላቻ ከዕለት ወደ እለት እየጨመረ ሄደ ። የአርተር ወደብ መነጠቅ ማለት የፈላጭ ቆራጩ አገዛዝ መውደቅ መጀመር ማለት ነበር ። ሌኒን ሲጽፍ የዛሩ አገዛዝ አብዮቱን ለማፈን ጦርነቱን መጠቀም ፈልጐ ነበር ። ነገሩ ግን ከአሰበው በተቃራኒ ሆኖ አገኘው ። በሩሲያና በጃፓን መሀል የተደረገው ጦርነት የአብዮቱን ፍንዳታ አፋጠነው ብሏል ።

በዛሪስት ሩስያ የካፒታሊስት ኢ-ሰብአዊ ቀንበር በዛሩ አገዛዝ ቀንበር ይበልጡን እየጠበቀና ይበልጡን እየከፋ ሄደ ። ሠራተኞች በካፒታሊስት ኢ-ሰብአዊ የሆነ አድካሚ ሥራና ብዝበዛ ብቻ የሚማቅቁ ሳይሆኑ ፡ ከመላው ሕዝብ ጋር እንዲሁም ሰብአዊ ልዕልናቸው ተረግጦ ፣ መብታቸው ተገፎ ይገኝ ነበር ። ስለሆነም በፖለቲካ የነቁ ሠራተኞች በከተማና በመላው ሀገሪቷ ያሉትን ዲሞክራሲያዊ ሀይሎች ለማሰባሰብ ጸረ-ዛር የሆነ አብዮታዊ ንቅናቄ ማካሄድ ይፈልጋሉ ። እርሶ አደሮች መሬት በማጣትና ብዙ የገባርነት ቅሪቶች በመኖራቸው የተነሳና ከመሬት ከበርቴዎችና ሀብታም ገበሬዎች ጋር ተሳስረው በመኖራቸው የተነሳ በአስከፊ ችግሮች ላይ ነበሩ ። በዛሪስት ሩስያ ውስጥ የሚገኙ ብሔሮች በጣምራ ቀንበር ሥር የራሳቸው የመሬት ከበርቴዎች ፣ ካፒታሊስቶችና እንዲሁም

በሩሲያ የመሬት ከበርቴዎችና ካፒታሊስቶች ተጣምደው የሲቃ ጩኸት ያሰማሉ ፡ በ1900—03 ዓ.ም. የኢኮኖሚ ቀውስ የሠርቶ አደሩን ሕዝብ ችግር ይበልጥ እንዲባባስ አደረገው ። ጦርነቱ ደግሞ ይበልጥ ሁኔታውን አጉላው ። የጦርነቱ ሽንፈት ደግሞ ይበልጥ ሰፊው ሕዝብ በዛሩ አገዛዝ ላይ ጥላቻ እንዲያድርበት አደረገ ። የሕዝቡ ትእግሥት ተሟጦ አከተመ ።

እንደምናየው ለአብዮቱ ፍንዳታ በቂ የለማ መስክ ነበር ማለት ይቻላል ።

በታህሣሥ ወር 1904 ዓ.ም. ትልቅና በሚገባ የተደራጀ የሥራ ማቆም አድማ በባኩ የቦልሼቪክ ኮሚቴ እየተመራ በባኩ ውስጥ ተካሄደ ፡ በዘይት አውጭ ሠራተኞችና በአሠሪዎቹ መሀል የጋራ ስምምነትን ያስገኘ በሩሲያ ሠራተኞች የንቅናቄ ታሪክ ውስጥ የመጀመሪያውን ምዕራፍ የያዘው ይህ ታላቅ የሥራ ማቆም አድማ በድል አድራጊነት ተፈጸመ ።

የባኩ ሥራ ማቆም አድማ በትራንስካውካሲያንና በተለያዩ የሩሲያ ክፍሎች ውስጥ የአብዮታዊ መነሳሳት የመጀመሪያው ምልክት ነበር ማለት ይቻላል ።

«የባኩ የሥራ ማቆም አድማ በጥርና በየካቲት ወር ለመላው ሩሲያ አሸብራቂ እርምጃዎች ምልክት ነበር» (ስታሊን)

ይህ የሥራ ማቆም አድማ ታላቁን አብዮታዊ ማዕበል ለማብሰር የተደረገ ነጐድጓዳዊ ጥሪ ነበር ።

በጥር 9/1905 በቅዱስ ፒተርስበርግ አብዮታዊ ማዕበል ፈነዳ ።

በጥር 3/1905 በትልቁ የቅዱስ ፔተርስበርግ የፑትሌቭ (አሁን ኪሮቭ) ፋብሪካ የሥራ ማቆም አድማ ፈነዳ ።

የሥራ ማቆም አድማው መነሾ አራት ሠራተኞች ከሥራው በመባረራቸው ምክንያት ነበር ። ወዲያውኑ በመስፋፋትም የቅዱስ ፔተርስበርግን የወፍጮና የፋብሪካ ሠራተኞች አዳምሮ ተነሳና የሥራ ማቆም አድማው አጠቃላይ ሊሆን በቃ ። ይበልጥም እስጊና አስደንጋጭ እየሆነ በመምጣቱ «እባብን በእንጭጩ ነው» በማለት የዛሩ አገዛዝ አድማውን ለመምታት ወሰነ ።

በ1904 ዓ.ም. ከፑቲሎቭ አመጽ ቀደም ብሎ ፖሊሶች ጋፖን የሚባለውን ቄስ በሰላይነት በመጠቀም የሩስያ የፋብሪካ ሠራተኞች ስብሰባ ተብሎ የሚታወቀውን ድርጅት እንዲመሠረት አድርገው ነበር ። ይህ ድርጅት በመላው የቅዱስ ፔተርስበርግ ቀበሌዎች የራሱ ቅርንጫፎች ነበሩት ። የሥራ ማቆም አድማው ሲፈነዳ ቄስ ጋፖን በድርጅቱ ስብሰባ ላይ ከሀዲ ፕላኑ ተቀባይነት እንዲያገኝ ሰበከ ። ጥር 9 ቀን መላውን ሰራተኞች በመሰብሰብ የቤተክርስቲያን ግርማና የዛሩን ምስል በመያዝ በሰላማዊ ሰልፍ ወደ ክረምቱ ቤተመንግስት አመሩ ። ጉዞአቸውም የተሰ



ማሙባቸው (የተፈራረሙባቸውን) ጥያቄዎች በመደርደር ለዛሩ ለማቅረብ ነበር ። ዛሩም ከሕዝቡ በፊት በመገኘት ሕዝቡ የሚለውን ሁሉ አዳመጠና ጥያቄአቸውን መለሰላቸው።ቄስ ጋፖን የዛሩ አከሀራና (ሚስጠራዊ ፖሊሲ) ያለምክንያት በሠራተኞቹ ላይ የጥይት ናዳ እንዲያወርድና የሰራተኛው መደብ ንቅናቄ በደም እንዲዋጅ ታላቅ ድጋፍ አደረገ ። ይሁን እንጂ ይህ የፖሊሲ ድርጊት በዛሩ እናት ላይ ተጠመጠመ ።

ይህ የድጋፍ ፊርማ በሰራተኞች ስብሰባ ላይ ተጨማሪ ሀሳብ ታክሎበት ተወያዩበት ። ራሳቸውን በጉልህ ሳያሳውቁ ቦልሼቪኮች በዚህ ስብሰባ ላይ ንግግሮችን አደረጉ ። እነርሱ ባደረጉት ግፊት በጥያቄው ላይ የጽሁፍ ነጻነት ፡ የንግግር ነጻነት ፡ የድርጅት ነጻነት ፡ የሩሲያን የፖለቲካዊ ስርዓት ለመለወጥ የሚያስችል ሥልጣን ያለው ስብሰባ የማዘጋጀቱ ፡ ከሕግ በፊት የሁሉም እኩልነት ፡ የቤተ ክርስቲያን ከመንግስት መገንጠል ፡ የጦርነቱ ማብቃት ፡ በቀን 8 የሥራ ሰዓት የመሆንና የተያዙ መሬቶች ለገበሬዎች የመስጠታቸው ጥያቄዎች ሊታከሉ በቅተዋል ።

ቦልሼቪኮች በዚሁ ስብሰባ ላይ እርግጥ በየሠራተኞች ፊርማ የጸደቁ ጥያቄዎችን በወረቀት ላይ ጽፎ ለዛሩ በማቅረብ የሚገኝ ሳይሆን በትጥቃዊ ድል በመምታት የሚገኝ ነው ሲሉ በስብሰባው ላይ ለሰራተኞች ገለጹ ። የጥያቄውን ወረቀት ለዛሩ በምታቀርቡበት ወቅት የምታገኙት ምላሽ ቢኖር የጥይት ውርጅብኝ ብቻ ነው በማለት ሠራተኛውን አስጠነቀቁ ። ታዲያ ምን ያደርጋል የሠራተኛው አብዛኛው ክፍል አሁንም ቢሆን የዛሩ አገዛዝ ሊረዳን ይችላል ፡ ብሎ ያምን ነበር ። ንቅናቄውም ከፍተኛ ድጋፍ በሰፊው ሕዝብ ዘንድ አገኘ ።

የቅዱስ ፔተርስበርግ ሠራተኞች በጽሁፍ ያቀረቡት ጥያቄ የሚከተለው ነበር ፡—

«እኛ የቅዱስ ፔተርስበርግ ሠራተኞች ሚስቶቻችንን ፡ ልጆቻችንና ረዳት ያጡ ደካማ ወላጆቻችንን ፡ በአንድነት እዚህ ስንመጣ የኛ ንጉስ እውነተኛነትን የሚሹና መድኃኒታችን ነዎት በማለት ነው ። እኛ ድህነት ያላሸቀን ጉስቋሎች ነን ። እኛ የተመዘበርን ፡ በአድካሚና በአስልቺ ሥራ ተጠምደን የምንማቅቅ ጭቁኖች ነን ። እኛ ኢ-ሰብአዊ በሆነ የግፍ ማጥ ውስጥ የተጣልንና የተዋረድን ምስኪኖች ነን . . . እኛ በትልቅ ችግር አዘቅት ውስጥ የተነከርን ይበልጥ በድሕነት ማጥ ውስጥ እየጠለቅን እየራቅን የምንሄድ ፡ መብቶቻችንን የተገፈፍንና እንድንደነቁር የተደረግን ነን ። እኛ በአልተለመደና ተቀናቃኝ በሌለው ጨካኝና ፍትህ በማያውቅ አገዛዝ ስር ወድቀን እንገኛለን ። . . . አሁን ግን ትእግስታችን ተሟጦ አልቋል ። እጅግ አስፈሪና አስቸጋሪው ወቅት ከፊታችን ተጋርጦ የምናየው ነው ። ይህን ድቅድቅ ጨለማ ፡ ይህን ፍጹም ልንወጣው የማንችለውን ችግር ከመጋፈጥ መሞት እንመርጣለን ። . . . . .»

ጥር 9 ቀን 1905 ዓ.ም. ማለዳ የክረምቱ ቤተ መንግስት በሴቶች ፥ በልጆች በአዛውንቶችና በባልቴቶች በአንድ ቃል በሰራተኛ መላው ቤተሰቦች ተጥለቀለቀ ። ብሶታቸውን ለዛሩ ለማሰማት በሰላማዊ ሰልፍ ወደ ክረምቱ ቤተመንግስት አመሩ ። እነዚህ ሠላማዊ ሰልፈኞች ድምጻቸውን ከፍ በማድረግ መንፈሳዊ መዝሙር ከመዘመራቸውም ሌላ የዛሩን ምሥልና የቤተክህነት አርማዎችን ከፍ በማድረግ ይዘው ነበር ። ያ አውራ ጐዳና ከ140,000 በላይ በሚገመቱ ሰዎች ተጥለቅልቆ ቢታይም ከመሀከላቸው ትጥቅ አንዳችም ሰው አልነበረውም ።

ዳግማዊ ዛር ኒኮላስ ሰላማዊ ሠልፈኞችን በጠላትነት አስተናገዳቸው። ወታደሮቹም በሕዝቡ ደም ይዋጁ ዘንድ ትእዛዝ ሰጠ ። ዛሩ ወይም የዛሩ ባለሟሎች እንደታሰበው ሠራተኛውን ሊረዱ የሚችሉ አልነበሩምና ለረሀባቸው ፥ ለርዛታቸውና ለአቀረቡት ብሶታቸው የአገኙት መልስ ቢኖር የጥይት ውርጅብኝና አረመኔያዊ ጭፍጨፋ ብቻ ነበር ። ያልታጠቀው ሕዝብ አንዳችም ምላሽ ማድረግ አይችልምና ኢ-ሰብአዊ በሆነ መንገድ በየመንገዱ ወደቀ ። ከሺህ በላይ የሚሆኑ ሰዎች የሞት ጽዋ ተጐነጩ ። ከሁለት ሺህ በላይ የሚሆኑት ቆሰሉ ። የቅዱስ ፔተርስበርግ አውራ ጐዳናዎችም በደም ጐርፍ ቀለሙ ።

ቦልሼቪኮች ትግሉን ከዳር ቆመው አልተመለከቱም ። ከሠራተኛው ጐን በመቆም ሠላማዊ ሰልፉን ተካፍለዋል ። ከሠላማዊ ሠልፈኞቹ ጋር የሞት ጽዋ ጨልጠዋል ። አብረው ታስረዋል ። በየጐዳናው ላይ በወደቁት ባልቴቶች ወጣቶችና ልጆች እሬሳ ላይ ከሠራተኞች ጋር እየተሯሯጡ ይህን አስከፊ ወንጀል እንዲፈጸም ያደረገው ማንው እንዴትስ ነው የምንታገለው ? በማለት በጓዶቻቸው ደም ላይ ሰራተኞችን አስተምረዋል ቀስቅሰዋል ።

ያ አውራጐዳና በሠራተኞች ደም የተጥለቀለቀበት ጥር 9 ቀን 1905 ዓ.ም. «የደም ሰንበት» በመባል ይታወቃል ። በዚህ እለት የሠራተኞች የደም ዋጋ ታላቅ ትምህርት ቀስመዋል ፥ አዎ በዛሩ ላይ የነበራቸው እምነት ነበር የዚያን እለት መልስ ጥይት እንዲሆን ያደረገው ። አሁን ግን የሠራተኛው መብት ያለትግል ፍጹም እንደማይገኝ አበክረው ተረድተዋል ። በዚያን ማለዳ የሠራተኛውን ቀበሌዎች ከጠላት ለመከላከል መሰናክሎች (Barricade) በየመንገዶቹ ተደርገው ነበር ። «ዛሩ ለኛ በሚገባ አድርጐልናል አሁን ደግሞ እኛ እናደርግለታለን» የሚሉ ዛቻዎች ከሰራተኛው ይሰሙ ነበር ።

ይህ የሚሰቀጥጥ የዛሩ አረመኔያዊ የወንጀል ድርጊት በሰፊው ተወራ። የሰራተኛውን መደብና መላው ሀገር ሁኔታውን ማሰብና ማሰላሰል ጀመረ ። ይህን ኢ-ሰብአዊ ድርጊት በመቃወም አንዳችም የሥራ ማቆም አድማ ያልተደረገበት ከተማ አይገኝም ። ሁኔታው ሁሉ ተለውጧል ። ሠራተኞች በየጐዳናው «ፈላጭ ቆራጩ አገዛዝ ይውደም !» የሚሉ መፈክሮችን



ይዘው መውጣት ጀመሩ ። በጥር ወር ላይ የሥራ ማቆም አድማው ተሳታፊዎች ቁጥር ሲሰላ 440,000 የሚገመት ከፍተኛ እርከን ደረሰ ። ከአለፉት አሥር ዓመታት ጋር ሲነጻጸር ከበፊቱ ይልቅ በአሁኑ አንድ ወር ውስጥ የተሳታፊዎቹ ቁጥር እጅግ ጨመረ ። የሠራተኛው መደብ ንቅናቄ በአልተጠበቀ ቁጥር እየጨመረ ሄደ ።

አብዮት በሩስያ ተቀጣጠለ ።

2/ <u>የሠራተኞች ፖለቲካዊ የሥራ ማቆም አድማና ሠላማዊ ሠልፎች ፥ በአርሶ አደሮች መሀል አብዮታዊ ንቅናቄ ማደጉ ፥ በ «ፖተምኪን» የጦር መርከብ ላይ አመጽ ስለ መነሳሳቱ ። —</u>

ከጥር 9 ቀን 1905 በኋላ የሠራተኛው አብዮታዊ ትግል እያደገ ፥ ይበልጥ እየከረረና ፖለቲካዊ ባሕርይ እያገኘ መጣ ። ሠራተኞች ከኢኮኖሚ ትግል እየተላቀቁ ለፖለቲካዊ ጥያቄዎች ሥራ በማቆም ወደ መታገሉ በማምራት ሠላማዊ ሠልፎች አካሄዱ ። የታጠቀን የዛር ሠራዊት በታጠቀ ሕዝባዊ ሀይል ወደመመከቱ ተሸጋገሩ ። በተለይም አብዛኛው የሰራተኛው ክፍል የተከማቸባቸው በነቅዱስ ፔተርስበርግ ፥ ሞስኰ ፥ ዋርሶው ፥ ሪጋ ፥ ባኩ በመሰሉ ታላላቅ የኢንዱስትሪ ከተሞች በሚገባ የተደራጁና የተጠናከሩ የሥራ ማቆም አድማዎች ተደርገዋል ። በዚህም ወቅት የብረታ ብረት ሠራተኞች በመዋጋት ላይ የነበሩትን ወዝአደሮች በቀደምትነት ይመሩ ነበር ። በዚህ የነቁ ወዝአደሮች ግንባር ቀደምነት የሚደረጉት እንቅስቃሴዎች የመደብ ንቃታቸው ዝቅተኛ የሆኑትን ክፍሎች አነሳሱአቸው ። ብሎም መላውን የሠራተኛ መደብ ለትግሉ አዘጋጁት ። የሶሻል ዲሞክራቶች ተሳትፎ በተፋጠነ ሁኔታ አደገ ።

የሜይ ዴይ ሰላማዊ ሠልፎች በብዙ ከተሞች ከፖሊሶችና ከዛሩ ሠራዊት ጋር ትንቅንቅ በማድረግ ይታወሳሉ ። በዋርሶው በተደረገው የሰራተኞች ሠላማዊ ሠልፍ ላይ የጥይት ተኩስ ተከፍቶ በብዙ መቶ የሚቆጠሩ ሰዎች ተገለዋል ወይንም ቆስለዋል ። የፖሊስ ሶሻል ዲሞክራቶች በአደረጉት ጥሪ መሰረት በዋርሶው ላይ ለአደረጉት ፍጅት ምላሽ አጠቃላይ የሥራ ማቆም አድማ ተመታ ፥ የሚደረጉት የሥራ ማቆም አድማዎችና ሠላማዊ ሠልፎች በዚያን ወር (ግንቦት) ውስጥ ብቻ አልተጠቃለሉም ። ይሁን እንጂ በዚሁ ግንቦት ወር ውስጥ ብቻ በመላው ሩስያ 200,000 ሠራተኞች በሥራ ማቆም አድማው ተሳትፈው ነበር ። በካኩ ፥ በሎድዝና በኢቫኖቮ-ቮዝኔሲስክ አጠቃላይ የሥራ ማቆም አድማዎች ተደረጉ ። የሥራ ማቆም አድማዎችና ሠላማዊ ሰልፎች ከዛሩ ሠራዊት ጋር ግጭት ማድረጉ ተዘወተረ ። እንደነዚሁ ዓይነት ትንቅንቆች በኦዴሳ ፥ በዋርሶው በሪጋ ፥ በሎዶዝና በሌሎችም ከተሞች ተደርገዋል ።

በተለይ እጅግ ግለት የነበረው ፍልሚያ የፖሊሽ ታላቅ ኢንዱስትሪያዊ ማእከል በሆነችው በሎድዝ የተደረገው ትግል ነበር ። የሎድዝ ሠራተኞች በየአውራጐዳናው ላይ መሰናክሎችን በማድረግ ለሶስት ቀናት

በየጉዳናው ከዛሩ ወታደሮች ጋር መራራ ፍልሚያ አደረጉ ። ከአጠቃላይ አድማው ጋር እነዚህ ትጥቃዊ እርምጃዎች ተዋህደው (ተቀናጅተው) ሲታዩ የሰራተኛውን የትግል እድገት ደረጃ አጉልተው ያሳዩናል ። ሌኒን ይህንን እርምጃ የሩሲያ ሠራተኞች ለሚያካሂዱት ትጥቃዊ አመጽ የመጀመሪያው አድርጎ ይመለከተዋል ።

በዚያን በጋ ወራት የተደረገ ታላቅ የሥራ ማቆም አድማ ቢኖር የአቫኖቮ-ቮዝኔሲንስኪ ሠራተኞች ያደረጉት ነበር ። ይህ አድማ ሁለት ወር ተኩል—ከግንቦት መጀመሪያ እስከ ነሐሴ መጀመሪያ 1905 ዓም—የፈጀ ነበር ። በቦልሼቪክ ስሜናዊ ኰሚቴ እየተመራ 70,000 —(አብዛኛው ሴቶች ናቸው) ።— ያህል ሠራተኞች ተሳታፊ የሆኑበት ትልቅ አድማ— ነበር ። በየእለቱ በሺህ የሚቆጠሩ ሠራተኞች ከከተማው ወጣ ብሎ በሚገኘው የታልካ የባሕር ዳርቻ በመሄድ እየተሰበሰቡ የቦልሼቪኮችን ንግግር ማዳመጡ የተለመደ ሲሆን ፣ ጥያቄዎች እየተነሱ ሀሳብ ለሀሳብ ይለዋወጣሉ ፣ ይመካከራሉም ። የሠራተኛውን እንቅስቃሴ ለመምታት የዛሩ ባለሥልጣኖች ሠራዊቶቻቸውን በመላክ እንቅስቃሴውን ለመከተል ተኩስ እንዲከፍቱ ትእዛዝ ሰጡ ። በርከት ያሉ ምርጥ ታጋዮች ተገደሉ ። በብዙ ሺህ የሚቆጠሩም ቆሰሉ ። በከተማው የአስቸኳይ ጊዜ አዋጅ ታወጀ ፣ ይሁን እንጂ ይህ አረመኔያዊ ፍጅትም ሆነ አዋጁ ሠራተኞቹን ከአላማቸው ፍንክች አላደረጋቸውም ። ወደ መደበኛ ሥራቸው አልተመለሱም ። ሠራተኞቹም ሆኑ ቤተሰቦቻቸው በአስከፊ የረሀብ ሰቆቃ ይገረፉ እንጂ በከፍተኛ የኑሮ ችግር ውስጥ ይዘፈቁ እንጂ ለዛሩ ኢ-ሰብአዊ ጭፍጨፋ እጃቸውን አልሰጡም ። በጉልበታቸው ተንበርክከው ማረን ፣ ይቅርታ አድርግልን አላሉትም፣ አሁን ሠራተኞች የመደብ ጠላታቸውን በቅጡ ተገንዝበውታልና ። ወደ መደበኛ ሥራቸው የመለሳቸው አጠቃላይ ሀይል በማጣታቸው ብቻ ነበር ። ያም ሆነ ይህ እንቅስቃሴው ሠራተኞችን ከብረት ይልቅ እንዲጠነክሩ አድርጓቸዋል ። በሠራተኛው መደብ ውስጥ መተማመን ፣ ጀግንነት ፣ ያለመበገርና የአንድነት መልካም ምሳሌ ተፈጠረ ፤ ለኢቫኖቮ ቮዝኔሴንስክ ሠራተኞች እውነተኛ ፖለቲካዊ ትምህርት ነበር ።

የኢቫኖቮ—ቮዝኔሴንስክ ሠራተኞች አድማውን በመቱበት ወቅት በሩስያ የመጀመሪያው የሶቭየቶች የሠራተኞች እንደራሴ አንዱ የሆነውን የተወካዮች የመማክርት ሸንጎ መሠረቱ ።

የሠራተኞች አድማ መላውን አገር ከዳር እስከዳር አናወጠው ። ስለሆነም የከተማውን የእንቅስቃሴ ፈለግ በመከተል ገጠሩም አድማውን በሌላ እንቅስቃሴ በማጀብ አሸበረቁ ። በጸደይ ወራት የአርሶ አደሮች እንቅስቃሴ ፈንድቶ እጅግ በርካታ አርሶ አደሮች የመሬት ከበርቴዎችን በመቃወም ሁዳዶችን ፣ የስኳር ማጣሪያና ማንጠሪያዎችን በመውረር መኖሪያ ቤታቸውንና ቤተ ክርስቲያኖቻቸውን በእሳት አጋዩት።በርከት ባሉ



አካባቢዎች የመሬት ከበርቴዎችን መሬት በመያዝ ለሕዝቡ ተመልሰው ይሰጡ በማለት በላዩ ላይ ያለውን እየቆረጡ ለመሸጥ ይተጋገዙ ነበር ። እህል የተከማቸባቸውን የመሬት ከበርቴዎችን መሬት በመያዝ እህል ለተራቡ ወገኖቻቸው አከፋፈሉ ። በዚሁ ሁኔታ የተደነገገው የመሬት ከበርቴዎች የገጠሩን የአርሶ አደር አመጽን በመሸሽ ወደ ከተሞች ሸሹ ። የዛሩ አገዛዝ የመደብ ጓዶቹን መጠበቅ ታሪካዊ ግዴታው ነውና የተለመዱትን ሰው በላ ወታደሮቹንና ኮዛኮችን አመጸውን «እንዲያጠፉ» ላካቸው ። ተልእኮአቸው ነውና የጥይት ናዳ በአርሶ አደሮች ላይ አወረዱባቸው «የአመጸውን መሪዎች» በማሰርና በመግረፍ በጽኑ አሰቃዩአቸው ። ይሁን እንጂ አርሶ አደሮች ትግል ከማድረግ አልተቆጠቡም ።

በቮልጋ አካባቢና በትራንስካውካሲያን ውስጥ በተለይ ደግሞ በጆርጅያ ውስጥ ማለትም በሩስያ ማዕከላዊ ክፍል የአርሶ አደሮች አመጽ እየተቀጣጠለና እየሠፋ መጣ ።

ሶሻል ዲሞክራቶች በገጠር አካባቢዎች በሚገባ ሁኔታ ሰርገው ገቡ ። «አርሶ አደሮች መልእክቶቻችን ይድረሳችሁ !» በሚል ርእስ የፓርቲው ማዕከላዊ ኰሚቴ ለአርሶ አደሮች ጥሪ አደረገ ። የሶሻል ዲሞክራቲክ ኰሚቴዎች በቲቬር ፣ በፓልታቫ ፣ በቼርኒኮቭ ፣ በስራቶቭ ፣ በኤካቴርኖስላቭ ፣ በቲፍሊስና በሌሎች ጠቅላይ ግዛቶች አርሶ አደሮች ጥሪ አደረጉ ። በየመንደሮቹ ስብሰባዎች በማዘጋጀት በአርሶ-አደሮች መሀል ክበቦች አደራጁ ፣ ከዚህም በቀር የአርሶ አደር ኰሚቴዎችን በየአካባቢው መሰረቱ ። በ1905 ዓ.ም. የበጋ ወራት በሶሻል-ዲሞክራቶች የተደራጁ የእርሻ ሠራተኞች በየአካባቢው ይታዩ ነበር ።

ይሁን እንጂ ይህ ወቅት የአርሶ አደሮች የመጀመሪያ ትግል ነበር ። የአርሶ አደሮቹ እንቅስቃሴ በ85 አካባቢዎች (አዩዝድስ) ወይም የመላው አካባቢ አንድ ሰባተኛ—ያውም በአውሮፓ በኩል ባለው ዛሪስት ሩስያ ብቻ ነበር የተዳረሰው ።

የሠራተኞችና የአርሶ አደሮች እንቅስቃሴ እንዲሁም በሩስያና በጃፓን መሀከል የተደረገው ጦርነት በዛሩ ወታደሮች ላይ ያስከተለው ጠንካራ ችግር በጦር ሀይሎች ላይ ተጽእኖ አሳደረ ። የዛሩ አገዛዝ ከሚደርስበት ጥቃት ራሱን ለመከላከል ያለው ሀይል እየተዳከመ በራሱ ጸንቶ ለመቆም እንኳን እየተሳነው መንገዳገድ ጀመረ ።

አጠቃላይ የሠራተኛው የሥራ ማቆም አድማ በመደረግ ላይ በነበረበት በኦዴሳ አካባቢ ሠፍሮ በነበረው የጥቁር ባሕር የጦር መርከበኞች የተቀጣጠለው የፖተምኪን አመጽ በሰኔ 1905 ፈነዳ ። የአመጹት ወታደሮች በአድሀሪ መኰንኖች ላይ የበቀል እርምጃ ለመውሰድ የጦር መርከቦቻቸውን ወደ ኦዴሳ አመጡ ። የፖተምኪን የጦር መርከበኞች ከአብዮቱ ጎን ያለአንዳች ማወላዳት ተሰለፉ ።

ሌኒን ለፖተምኪን አመጽ የማይዘነጋ አስተዋጽኦ አበርክቷል ። የንቅናቄውን አመራር ከሠራተኞች ፣ ከአርሶ አደሮችና ከአካባቢ ወታደሮች ንቅናቄ ጋር በማያያዝ መመልከቱ ለበልሼቪኮች እጅግ ጠቃሚ ነው ሲል አጥብቆ አስገንዝቧል ።

የዛሩ አገዛዝ በርካታ የጦር መርከቦችን ወደ ፖትምኪን አዘመተ ። ይሁን እንጂ እነዚህ የጦር መርከበኞች በአመጹት ጓዶቻቸው ላይ ተኩስ ላለመክፈት ተስማሙ ። ለበርካታ ቀናት የፖተምኪን መርከብ ምሰሶዎች አብዮታዊ ሰንደቅ ሲያውለበልቡ ሰነበቱ ። ይሁን እንጂ በዚያን ወቅት ማለትም—ከ1905 ዓ/ም በኋላ በ1917 እንደሆነው እንቅስቃሴውን ይመራ የነበረው የቦልሼቪክ ፓርቲ ብቻ አልነበረም ። ጥቂት የሜንሼቪክ ፣ የሶሻሊስት አብዮተኞችና ሥርዓተ-አልበኞች በፖትምኪን የጦር መርከበኞች ውስጥ ነበሩ ። እንዲሁም የሶሻል ግለሰቦች በአመጻው ውስጥ ተካፍለዋል ። ይሁን እንጂ እንቅስቃሴው የሚያመረቃና ልምድ ያለው የአመራር እጥረት ነበረበት ። በወሳኙ ወቅት ጥቂቶቹ መርከበኞች ማንገራገር ጀምረው ነበር ። ሌላው የጥቁር ባሕር መርከበኞች ጓድ የፖተምኪን አመጻ አልተካፈለም ። አብዮታዊ መርከበኞች በሩማኒያ የባሕር ዳርቻ ላይ መርከቦቻቸውን ለማሸሽ የከሰል እጥረት በመኖሩና አስፈላጊውን ዝግጅት ባለሟሟላታቸው እጆቻቸውን ለባለሥልጣኖች ሰጡ ።

ስለሆነም በፖትምኪን መርከበኞች የተደረገው አመጻ በሽንፈት አከተመ ። በዛሩ አገዛዝ ሥር የወደቁት መርከበኞች በከባድ መከራ ውስጥ ወደቁ ። ጥቂቶቹም ተገደሉ ፣ ሌሎቹም ወደ እስር ተጋዙ ። በሚያሰቃዩ ቅጣቶችም ተቀጡ ። ይሁን እንጂ አመጻው ታላቅ ጠቀሜታ የነበረው ነው ። የፖትምኪን አመጽ በጦር ሠራዊቱና በባሕር ሀይሉ ውስጥ የተደረገ የሰፊው ሕዝብ አብዮታዊ ተግባር ዓይነተኛ ምሳሌ ነው ። የዛሩ በርካታ የታጠቁ ሀይሎች ከአብዮቱ ጎን የቆሙበት የመጀመሪያ ወቅት ነው ። አመጻው የሰራዊቱንና የባሕር ሀይሉን አስተሳሰብ ከሠራተኛው መደብ ጋር እንዲገናኝ አድርጓል ። ሠራተኛውንና አርሶ አደሩን በተለይም በራሳቸው ወታደሮችና በመርከበኞች ዘንድ የቅርብ ልብ ለልብ መግባባትና መረዳዳትን አትርፏል ።

የሠራተኞች ሰፊ ፖለቲካዊ እንቅስቃሴና ሰላማዊ ሠልፎች ፣ እያደገ የመጣው የአርሶ አደሮች ንቅናቄ ፤ በሕዝቡና በፖሊሶች መሀከል የሚደረገው የተዘወተረ ግጭት ፣ በመጨረሻም በጥቁር ባሕር የመርከበኞች ጓድ የፈነዳው አመጽ በአጠቃላይ ሲገመገም ለታጠቀ ሕዝባዊ አመጽ መነሳሳት ሁኔታው አመቺ መሆኑን የሚያሳይ ሆነ ። ይህ ሁኔታ ለዘብተኛ ቡርዧው በእንቅስቃሴው ውስጥ እንዲገባ ጐተተው ። አብዮቱን እንደጦር በመፍራትና በዛሩ አገዛዝ ላይ አብዮቱ ወደፊት የሚያስከትለውን በጭንቀት በማሰላሰል አብዮቱን በጽኑ ተቃወመ ። ከዛሩ ጎን ተሰልፎ «ለሕ



ዝቡ» ትንሽ ጥገናዊ ለውጥ እንዲያደርግና ሕዝቡን «ተሳትፎ አልባ» ማድረግ እንዲቻል የአብዮቱን ሀይል ለመከፋፈልና እንዲሁም «አብዮቱ ያስከተለውን ድንጋጤ» ለማስወገድ ለዘብተኛ ቡርዧዎች ተነሱ ። «መሪዎቻችንን ከምናጣ መሬታችንን ብናጣ ይሻለናል» በማለት ለዘብተኛ የመሬት ከበርቴዎች ይናገሩ ጀመር ። ለዘብተኛ ቡርዧው ከዛሩ ጋር ሥልጣን ለመቀራመት ራሱን አዘጋጀ ። ሌኒን የሠራተኛውን መደብ ታክቲክና የለዘብተኛ ቡርዧውን ታክቲክ አስመልክቶ በወቅቱ ሲጽፍ «ወዝአደሩ እየተፋለመ ሳለ ቡርዧው ሥልጣን ለመንጠቅ ይዋትታል» ሲል ተናገረ ።

የዛሩ አገዛዝ ሠራተኛውንና አርሶ አደሩን በአረመኔያዊ ጭካኔ ረግጦ መግዛቱን ይበልጥ ገፋበት ። ይሁን እንጂ እንደዚያ ያለ ኢ-ሰብአዊ እርምጃ በመውሰድ አብዮቱን መግታት ቀርቶ መቋቋም አለመቻሉን ተገነዘበና ግልጽ አሰሳዎችን እርምጃዎችን ከመውሰድ ሳይቆጠብ የጦርነት እንቅስቃሴ እቅድ መመሪያ በማውጣት ተግባሩን ማራመድ መረጠ ። በአንድ ወገን በሠላዮቹ እየተረዳ የሩስያ ሕዝቦች እርስ በርሳቸው እንዲናከሱ ያደርጋል ። በሌላ ጎን ደግሞ የዚሚሽኪ ሰበር ወይም በመንግስቱ ዱማ መልክ የተቀረጸ «የተወካዮች ተቋም» ጉባኤ ለማዘጋጀት ቃል ገብቶአል ። እንደዚህ ላለው ዱማ ፕሮጀክት ሚኒስተር ቡልጅንን በማሰልጠን አዘጋጅቷል ። ያም ሆነ ይህ የሚወራለት ይህ ዱማ ሕግ የማውጣት ሥልጣን የለውም ። ይህ ሁሉ ርምጃ የአብዮቱን ኃይላት ለመከፋፈልና መሀከለኛውን ሕዝብ ከአብዮቱ ተሳትፎ ለማገድ የተሸረበ ዘዴ ነበር ።

ቦልሼቪኮች ሕዝባዊ ተወካዮች በገለጸው ለማስፈራራት የታቀደበትን የቡልጂን ዱማን ጥለው ለመውጣት ወሰኑ ።

በሌላ ወገን ደግሞ ሜንሼቪኮች ዱማውን ማደናቀፍ አያስፈልግም በውስጡ መሳተፍ አስፈላጊነት አለው ሲሉ ወሰኑ ።

### 3/በቦልሼቪኮችና በሜንሼቪኮች መሀከል የነበሩ የታክቲክ ልዩነቶች፣ ሶስተኛው የፓርቲ ኰንግሬስ ፣ «በዲሞክራሲያዊ አብዮት ውስጥ የሶሻል ዲሞክራሲ ሁለት ታክቲኮች» የተሰኘው የሌኒን መጽሐፍ የማርክሲስት ፓርቲ ታክቲካዊ መሰረቶች ።

አብዮቱ መላውን የህብረተሰብ መደቦች በንቅናቄው ውስጥ አሳተፋቸው ። አብዮቱ የፈጠራቸው የሩስያ የፖለቲካ ሕይወት የጥንት መደቦች ከነበሩበት አስፈላጊ ሥፍራ ለቀው ራሳቸውን ከአዲሱ ሁኔታ ጋር እንዲያስተካክሉ አስገደዳቸው ። እያንዳንዱ መደብና እያንዳንዱ ፓርቲ የራሱ ታክቲኮች ፣ የፖለቲካ መስመር አመራር በሌሎች መደቦችና በመንግሥቱ ያለውን አቋም በተግባር እንዲያውል ጥረት ያደርጋል ። ሌላው ይቅርና የዛሩ አገዛዝ እንኳን ቢሆን የራሱ አዲስና ያልተለመደ ታክቲኮች

እንዲነድፍ ተገዷል ። «የተወካዮች ተቋም» ለመሰብሰብ ቃል ለመግባቱ የቡልጂን ዱማ ዓይነተኛ ምሳሌ ነው ።

የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ እንዲሁ የራሱን ታክቲክ መጠቀም አለበት ። የአብዮቱ ግፊት ይህንን እንዲያደርጉ ያስገድዳቸዋል ። ወዝአደሩን ፊት ለፊት በገጠሙት ተግባራዊ ጥያቄዎችና ሊያዘገዩት በማይችሉት የትጥቃዊ አመጽ ድርጅት ፣ የዛሩን አገዛዝ ገርስሶ መጣል ፣ የጊዜያዊ አብዮታዊ መንግስት መፈጠር በዚህ አስተዳደር ውስጥ የሶሻል—ዲሞክራቶች መሳተፍ ፣ በአርሶ አደሩና በለዘበተኛ ቡርዧው ላይ ያለው አዝማሚያ ወዘተ . . . እነዚህ ሁኔታዎች ታክቲካቸውን እንዲቀይሱ አስገደዱአቸው ። ሶሻል ዲሞክራቶች ለራሳቸው በጥንቃቄ መርምረው አንድ ዓይነት ማርክሳዊ ታክቲኮችን መጠቀም አለባቸው ።

ይሁን እንጂ የሜንሼቪኮች አድርባይነት ከነርሱ የመገንጠል እንቅስቃሴ ጋር ሲገናዘብ የሩስያ ሶሻል—ዲሞክራቲክ ፓርቲ በወቅቱ በሁለት ቡድን ተከፍሎ ነበር ። በርግጥ የነበረው መነጣጠል ሙሉ በሙሉ አልተጠናቀቀም ፤ እነዚህም ሁለት ቡድኖች ገና ሁለት የተነጣጠሉ የፓርቲዎች መልክ በመሆን ራሳቸውን አልከሰቱም ። ነገር ግን በእውነቱ እያንዳንዳቸው የራሳቸው መሪ አካልና የግላቸው እትም የነበራቸው ሁለት የተነጣጠሉ የፓርቲ መልክ ይመስሉ ነበር እንጂ ።

የነበረውን መነጣጠል ይበልጥ ያሰፋው ጥንት በድርጅት ጥያቄ ከፓርቲው ብዙኃን ክፍል ጋር በነበራቸው ልዩነት ላይ እንደገና ሜንሼቪኮች አዲስ ልዩነት በታክቲክ ጥያቄ ላይ — ፈጥረው በፊት ከነበሩት ልዩነቶች ላይ ስለአከሉበት ነው ።

የተዋሀደ ፓርቲ አለመኖር አንድ ዓይነት የፓርቲ ታክቲክ እንዳይኖር አደረገ ።

ቦልሼቪኮች የጋራ ታክቲክ ለመንደፍና ጥቂቶቹ የኰንግሬሱን ውሳኔ (የብዙኃኑን ውሳኔ) በሚገባ አምነው በመቀበል ራሳቸውን ለውሳኔው እንዳያስገዙ የሚያስችል ሶስተኛ የፓርቲ ኰንግሬስ መጥራት ከዚህ ሁኔታ ውስጥ ሊያወጣን ይችል ይሆናል ሲሉ ለሜንሼቪኮች አሳሰቡ ። ይሁን እንጂ ሜንሼቪኮች ለሶስተኛው ኰንግሬስ ጥሪ ጆሮ ዳባ ልበስ አሉ ። ፓርቲው ያጸደቀውን ታክቲክ በመቃወም ፓርቲውን ያለታክቲክ ማስቀረትና መላው የፓርቲ አባላት እንዳይተሳሰሩ ማድረግ እንደወንጀል በመቁጠር ቦልሼቪኮች የሶስተኛውን ኰንግሬስ በራሳቸው እጅ ለማስገባት ስብሰባ እንዲደረግ ወሰኑ ።

ሁሉም የፓርቲ ድርጅቶች ፣ መላው ቦልሼቪኮችና ሜንሼቪኮች በኮንግረሱ ላይ እንዲገኙ ተጋብዘው ነበር ። ነገር ግን ሜንሼቪኮች በሶስተኛው ኰንግረስ ውስጥ አንሳተፍም አሻፈረን በማለት የራሳቸው የሆነ ዝግጅት ለማድረግ ወሰኑ ። በኮንግረሳቸው ላይ የነበሩት የተወ



ካዮች ቁጥር በማነሱ ምክንያት ጉባኤ (ኰንፈረንስ) ብለው ጠሩት ። በርግጥ እንደዚያ ብለው ይጥሩት እንጂ ነገሩ ኮንግሬስ ነበር ። ውሳኔው መላውን የሜንሼቪክ አባሎች የሚያስተሳስር የሜንሼቪክ ፓርቲ ኰንግሬስ ነበር ።

የሩስያ ሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ሶስተኛ ኰንግረስ በሚያዝያ ወር 1905 ዓ.ም. በሎንደን ተሰበሰበ ። በኰንግሬሱ 24 ተወካዮች 20 የቦልሼቪክ ኰሚቴዎችን በመወከል ተካፍለዋል ። የፓርቲው ትላልቅ ድርጅቶችም ሊካፈሉ በቅተዋል ።

«ከፓርቲው እንደተገነጠሉ ክፍሎች» በማድረግ ኰንግሬሱ ሜንሼቪኮችን አውግዞ የፓርቲውን ታክቲኮች ወደ መንደፉ ተግባር ተሸጋገረ።

ልክ ቦልሼቪኮች ይህን ኮንግሬስ በሎንደን ሲያካሄዱ ሜንሼቪኮችም የራሳቸውን ጉባኤ በጄኔቭ ያካሂዱ ነበር ።

«ሁለት ኮንግሬሶች — ሁለት ፓርቲዎች» በማለት ነበር ሌኒን ሁኔታውን የገመገመው ።

የቦልሼቪኮች ኰንግሬስና የሜንሼቪኮች ጉባኤ የተወያየው ተመሳሳይ በሆነ በታክቲክ ጥያቄዎች ላይ ነበር ።

ይሁን እንጂ የአሳለፉት ውሳኔ (አቋም) ፍጹሙኑ የተለያየ ነበር ። በኰንግረሱና በጉባኤው የጸደቀው ውሳኔ በሶስተኛው የፓርቲ ኰንግሬስ እና በሜንሼቪክ ጉባኤ ፣ በቦልሼቪኮችና በሜንሼቪኮች መሀከል የነበረውን ጠሊቅ የታክቲክ ልዩነቶች ገልጿል ።

የነዚህ ልዩነቶች ዓይነተኛ ነጥቦች የሚከተሉት ናቸው ፡—

<u>የሶስተኛው ፓርቲ ኰንግሬስ ታክቲካዊ መሥመር</u> ፡— ምንም እንኳ እያደገ የመጣው አብዮት የቡርዧ ዲሞክራሲያዊ አብዮት ባህርይ ቢኖረውም ፣ ምንም እንኳ በካፒታሊዝም መሰረቶች ውስጥ በተወሰነ ወቅት ሊደረግ ይችል ከነበረው ገደብ አልፎ ለመሄድ ያለመቻሉ እውነትነት ቢኖረው የአብዮቱ ድል ማድረግ ፤ ወዝአደሩ ራሱን እንዲያደራጅ ፣ በፖለቲካ እንዲጐለምስ ፣ በሰፊው ሠራተኛ ሕዝብ ፖለቲካዊ አመራር ውስጥ እንዲሳተፍ ፣ ከቡርዧ አብዮት ወደ ሶሻሊስት አብዮት እንዲሸጋገርና ጠቃሚ ልምድ እንዲያገኝ ያስችለዋልና ለአብዮቱ ሙሉ በሙሉ ድል ማድረግ በቅድሚያ ፍላጐት የሚኖረው ወዝአደሩ ነው በማለት ኮንግረሱ የጸና አቋም ወሰደ ።

የወዝ አደሩ ታክቲኮች የቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት ግቡን እንዲመታ የተነደፉ ሲሆኑ ፣ እነዚህም ታክቲኮች በአርሶ አደሩ የሚደገፉ ናቸው ። የቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት ግቡን ካልመታ መሬት ሊከፋፈልና ገበሬዎች የራሳቸውን መሬት ሊያገኙ አይችሉም ። ስለሆነም ገበሬዎች የግድ የወዝአደሩ አጋሮች ይሆናሉ ።

ለዘብተኛ ቡርዧው ግን ለአብዮቱ ግብ መምታት ደንታ የለውም ። እንደ ጦር የሚፈራቸውን ሠራተኞችና አርሶ አደሮች አፍኖ እንዲይዝለት

የዛሩ አገዛዝ ይፈልገዋልና ግፉ ቢል የሚኖረውን ሥልጣን ከመወሰን በቀር ሌላ ምንም የማያደርገውን የዛሩን አገዛዝ ከመጣበት መዓት ለመዳን የማይበጥሰው ቅጠል አይኖረውም ። ስለሆነም ለዘብተኛ ቡርዧው ነገሮች ሁሉ በፓርላሜንታዊ ዘውደኝነት እንዲያከትም ታላቅ ጥረት ያደርጋል ።

አብዮቱ በአሸናፊነት ሊወጣ የሚችለው በወዝአደሩ የተመራ እንደ ሆነ ብቻ ነው ። አብዮቱ በወዝአደሩ ቢመራና ከአርሶ አደሩ ጋር ኅብረት ቢፈጥር ለዘብተኛ ቡርዧው ቢገለል የዛሩን አገዛዝ በመቃወም ሕዝቡ በሚያደርገው መንሣሣት የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ አመጹን በማደራጀቱ ረገድ ከፍተኛ ሚና ቢጫወት ፣ በአመጹ መሣካት ሳቢያ ጊዜያዊ አብዮታዊ መንግስት ቢመሰረት ፣ የጸረ-አብዮተኞችን መሰረትና ቅርንጫፎች በማውደም መላውን ሕዝብ የሚወክለውን ስብሰባ ለመምራት መሰናዳት ይቻላል ። እንዲሁም የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ የተቀበለው እንዲሆን አብዮቱን ለማጠናቀቅ በጊዜያዊ አብዮታዊው መንግሥት ውስጥ ለመሳተፍ ሁኔታው አመቺ ይሆናል ።

<u>የሜንሼቪክ ጉባኤ (ኰንፈረንስ) ታክቲካዊ መስመር</u> ፣— አብዮቱ የቡርዧው አብዮት እስከሆነ ድረስ ለዘብተኛው ቡርዧው ብቻ ነው የአብዮቱ መሪ ሊሆን የሚችለው ። ወዝአደሩ ከገበሬው ጋር ሳይሆን ከለዘብተኛ ቡርዧው ጋር ነው የጠበቀ ሕብረት መመሥረት ያለበት ። ለዘብተኛው ቡርዧው የሚያሳየውን አብዮታዊ መንፈስ በመፍራትና ትክክል ያልሆነ ምክንያት በማቅረብ ከአብዮቱ ማሽቀንጠር አይደለም ፣ ለዘብተኛው ቡርዧው ከአብዮቱ የወጣ እንደሆን አብዮቱ ይዳከማል ።

አመጹ ድልን ሊያረጋግጥ ይችል ይሆናል ፣ ነገር ግን አመጸው ድል ካደረገ በኋላ የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ለዘብተኛ ቡርዧው እንዳይበረግግ ከጐኑ መቆም ይኖርበታል ። በአመጹ ሳቢያ ጊዜያዊ አብዮታዊ መንግስት ሊመሰረት ይቻላል ። ይሁን እንጂ የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ በምንም ዓይነት ሁኔታ በጊዜያዊ አብዮታዊ መንግስት ውስጥ መሳተፍ አይኖርበትም ። ምክንያቱም ይህ የሚመሰረተው መንግስት ሶሻሊስት ባሕርይ ሊኖረው አይችልም ። እንዲሁም በመንግስቱ በመሳተፍና በሚኖረው አብዮታዊ መንፈስ ፡— ይህ ነው ትልቁ ነገር — የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ለዘብተኛ ቡርዧውን በመፍራት አብዮቱን ዝቅ ያደርገዋል ።

ሠራተኛው መደብ ይህንን ወደ ሕገ መንግሥታዊ ስብሰባ ለማሸጋገር ወይም ለሕገ መንግሥታዊ ስብሰባ ጥሪ እንዲያደርግ ግፊት ሊያደርግበት የሚችል የዚሚሽኪ ሶበር ወይም መንግሥታዊ ዱማ ዓይነት የተወካዮች ተቋም መጥራት ለአብዮቱ ጥሩ ተስፋ ይሆናል ።

ወዝ አደሩ የተለየ የራሱ ንጹህ የደሞዝ ሠራተኝነት ስሜት አለውና ለዚህ ስሜት ብቻ የሚያገለግል በመሆኑ የአጠቃላዩ ፖለቲካዊ አብዮት የሆነውና ወዝ አደሩን ብቻ ሳይሆን ሁሉንም የኅብረተሰብ መደቦች የሚመለከተውን የቡርዧ አብዮት መሪ ለመሆን አይሞክርም ።



እንግዲህ በአጭሩ የሩሲያ ሶሻል ዲሞክራቲክ የሠራተኞች ፓርቲ ሁለቱ ቡድኖች የነደፉት ታክቲኰች እነዚህ ነበሩ ።

<u>በዲሞክራሲያዊ አብዮት ውስጥ የሶሻል—ዲሞክራቲክ ሁለት ታክቲኮች</u> በተሰኘው ታሪካዊ መጽሐፉ ውስጥ ሌኒን በሜንሼቪኮች ታክቲክ ላይ መሠረታዊ ሂስ በማቅረብ የቦልሼቪኰችን ብልህነት የተሞላባቸውን ታክቲኰች በመደገፍ አውስቶታል ።

ይህ መጽሐፍ ሶስተኛው ኰንግረስ ከተጠናቀቀ ከሁለት ወር በኋላ ማለትም በሐምሌ 1905 ዓ ም ታትሞ ወጣ ። አንድ ሰው የመጽሐፉን ርእስ በማየት ሌኒን ከቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት ወቅት ጋር ስለሚዛመዱ ታክቲካዊ ጥያቄዎች ፣ የሚያወሳና የሩሲያን ሜንሼቪኰች በአእምሮው ውስጥ እንዲቀረፁ አድርጐ ያስባል ። ይሁን እንጂ እንደእውነቱ ከሆነ የሌኒን ሥራ በዚህ አድማስ ውስጥ ብቻ ሳይሆን ከአድማሱም ውጪ ወጥቶ ዓቢይ ተግባር አከናውኗል ። የሜንሼቪኰችን ታክቲኰች በሄሰበት ወቅት ከዚሁ ጋር የዓለም አቀፍ አድርባይነት ታክቲኰችን አጋልጧል ። ብሎም በቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት ወቅት መኖር ስለሚገባቸው ማርክሳዊ ታክቲኰች አስገንዝቧል ። እንዲሁም በቡርዧው አብዮትና በወዝ አደሩ አብዮት መካከል ያለውን ልዩነት ከማሳየቱም በላይ ከቡርዧው አብዮት ወደ ሶሻሊስት አብዮት ሽግግር በሚደረግበት ወቅት መወሰድ ስለሚገባቸው ማርክሳዊ ታክቲኮች መሠረታዊ መመሪያዎችን ቀምሯል ። <u>በዲሞክራሲያዊ አብዮት ውስጥ የሶሻል—ዲሞክራሲ ሁለት ታክቲኮች በተሰኘው</u> ጽሑፉ ሌኒን መሠረታዊ የታክቲክ መመሪያዎችን እንደሚከተለው ያብራራል ።

1/ በሌኒን መጽሐፍ ውስጥ የሚገኘው ዋነኛው ታክቲካዊ መመሪያ ወዝ አደሩ የቡርዧውን ዲሞክራሲያዊ አብዮት ሊመራ የሚችልና መሆንም ያለበት ፤ በሩሲያም የቡርዧ ዲሞክራሲያዊ አብዮት ውስጥ መሪ ኃይል ነው ።

ሌኒን የዚህን አብዮት የቡርዧ ባሕርይ በመቀበል እንዲህ ይላል ። «የዲሞክራሲያዊ አብዮትን ወሰን ርትዕ በሆነ መንገድ መዝለል አይችልም ።» ያም ሆነ ይህ የሚካሄደው አብዮት የሕብረተሰቡ የበላይ ክፍሎች አብዮት አይደለም ። ነገር ግን መላውን ሠራተኛ መደብ ፣ መላውን አርሶ አደር ፣ መላውን ሕዝብ በንቅናቄው ውስጥ የሚጨምር ሕዝባዊ አብዮት ነው ። ስለሆነም ሜንሼቪኮች የቡርዧው አብዮት ለወዝ አደሩ የሚሰጠውን ጠቀሜታ ዝቅ የማድረግ አዝማሚያ ፣ ወዝ አደሮች በአብዮቱ (የቡርዧው) ውስጥ የሚኖራቸውን ሚና ማንኳሰስና ከተሳትፎው እንዲርቅ ማድረግ በሌኒን አስተሳሰብ የወዝ አደሩን ዓላማ ከመካድ ሌላ ምንም ሊሆን አይችልም ።

«ማርክሲዝም» ይላል ሌኒን «ወዝአደሮች ከቡርዧው አብዮት ተነጥለው እንዳይቀመጡ ፣ ከአብዮቱ ገለልተኛ መሆን እንደማያስፈል ጋቸው ፣ ቡርዧው የአብዮቱን አመራር እንዲጨብጥ በር በመክፈት መፍቀድ እንደሌለባቸው ፣ ነገር ግን በተቃራኒው አብዮቱን ለማጠናቀቅ ከፍተኛ ተጋድሎ ማድረግ ፤ ለወዝ አደራዊ ዲሞክራሲ በታላቅ ቆራጥ ነት መፋለም እንደሚኖርባቸው ያስተምራል ።»
(የሌኒን ምርጥ ሥራዎች ፣ እንግሊዘኛ እትም ፣ ሞስኮ 1946 ቅጽ 1 ገጽ 369)

ሌኒን ንግግሩን በማራዘም ፦ «ከተጠናቀቀ ፖለቲካዊ አርነት ይልቅ ከዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ይልቅ በአሁኑ ወቅት ሶሻሊዝምን ለማቃረብ የሚያስችል ሌላ ዓይነት መንገድ አልነበረም ። አሁንም አለመኖሩን መዘ ንጋት አይኖርብንም» (ከዚህ በላይ በጠቀስነው መጽሐፍ ገጽ 144)

ሌኒን የአብዮቱን ሁለት ውጤቶች በቅድሚያ ተገንዝቦ ነበር ።

ሀ/አብዮቱ በዛሩ አገዛዝ ላይ ወሳኝ ድል በመቀዳጀት ያከትማል ። ያ ማለት የዛሩን አገዛዝ ገርስሶ ዲሞክራሲያዊ ሪፖብሊክ ይመሠረታል ፣

ለ/አሊያም የአብዮቱ ኃይላት በቂ ካልሆኑ ቡርዧው ከዛሩ አገዛዝ ጋር በአንዳንድ በተሸፈነ ወይም በተመሳጠረ ሕገ መንግሥታዊ ድርድር የሕዝቡን ዓላማ አሳልፎ ይሰጣል ።

ከአብዮቱ ሁለት ውጤቶች ውስጥ ወዝ አደሩ በዛሩ አገዛዝ ላይ ወሳኝ ድል መቀዳጀትን ይፈልጋል ። ይሁን እንጂ ይህ ዓላማ ሊሰምር የሚችለው ወዝ አደሩ የመሪነቱን ሥፍራ ለመያዝ አሸናፊ ሲሆንና አብ ዮቱን መምራት ሲችል ብቻ ነው ።

«የአብዮቱ ውጤት» ይላል ሌኒን «የአብዮቱ ውጤት የሚወሰነው ሠራተኛው መደብ የቡርዧው አጋር በመሆን የፈላጭ ቆራጩን አገዛዝ ለመገልበጥ ኃይለኛ ፤ ነገር ግን በፖለቲካው አቅመ ቢስ ሚና በመጫ ወቱ ፣ አሊያም የሕዝቡን አብዮት በመምራት በሚጫወተው ድርሻ ላይ ነው ። (ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 344)

ሌኒን እንዳስገነዘበው ወዝ አደሩ ለቡርዧው አጋር ከመሆን ግፊት በማምለጥ የቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት መሪ ለመሆን ማናቸውም ችሎታ አለው ። ይህ ችሎታ እንደሌኒን አስተሳሰብ ከሚከተሉት የመነጨ ነው ።

መጀመሪያ ፦ «ወዝ አደሩ በሚኖረው ኅብረተሰብአዊ ሥፍራ በምግባሩ እጅግ የተራመደና ሁልጊዜም አንድ ብቸኛ አብዮታዊ መደብ ነው ። በዚህ ዓይነተኛ ምክንያት በሩሲያው አጠቃላይ ዲሞክራሲያዊ አብዮት የመሪ ነት ሚና መጫወት አለበት »
(ከላይ በጠቀስነው መጽሐፍ ገጽ 386)



ሁለተኛ ፦ ወዝ አደሩ ከቡርዧው ላይ ነጻ የሆነና «ወደ ተባበረና ነጻ የፖለቲካዊ ኃይል » ራሱን እንዲገነባ የሚያስች ለው የራሱ የፖለቲካ ፓርቲ አለው ።
(ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 368)

ሶስተኛ ፦ «በአንዳንድ ሁኔታ የቡርዧው አብዮት ከቡርዧው ይልቅ ለወዝ አደሩ ይበልጥ ይጠቅማል» በሚለው አመለካከት ወዝ አደሩ ከቡርዧው ይበልጥ ለአብዮቱ ወሳኝ ድል አድራጊነት ታላቅ ፍላጎት አለው ። (ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 368)

«ቡርዧው» ይላል ሌኒን በጽሁፉ «ከወዝአደሩ ጋር በሚያደር ገው ትግል በአለፉት ሥርዓት ርዝራዦች ላይ ማለትም በመደበኛው ወታደር ፣ በፈላጭ ቆራጩ አገዛዝ ወዘተ . . . ላይ እምነት መጣል ለቡ ርዧው ጥቅም ነው ። የቡርዧው አብዮት በቆራጥነት መላውን የአለፈ ውን ሥርዓት ርዝራዦች ሳያስወግድ ጥቂቶቹን ካስቀረ ማለትም የሚ ካሄደው አብዮት በሚገባ ካልተጠናቀቀና ወሳኝነት ከሌለው የሚሰጠው ጠቀሜታ ዝቅተኛ ከሆነ ለቡርዧው እጅግ ጠቃሚ ነው ። . . . በቡርዧ አብዮት አቅጣጫ ውስጥ ቀስ በቀስ ፣ ደረጃ በደረጃ ፣ እጅግ ጥንቃቄ በተሞላበት ሁኔታ ፣ ብዙ ቆራጥነትን ባይጠይቅ ፣ በአብዮት ሳይሆን በጥገ ናዊ መንገድ አስፈላጊው ለውጥ ከተደረገ ለቡርዧው ታላቅ ጠቀሜታ ይሰጠዋል ። . . . እነዚህ ለውጦች የሕዝቡን ነጻ አብዮታዊ ተግባር ፣ አነ ሳሽነቱንና መላውን ኃይሉን በተቻለ መጠን በጥቂቱ እንዲያድግ ማድ ረግ ሲገባው ይህንን ካላደረገ ፦ ያም ማለት የገበሬውን በተለይ ደግሞ የወዝ አደሩን—ግን እንደፈረንሣዮች አባባል ለሠራተኛው ቀላል ይሆ ንለታል ። ፈረንሣዮች «ጠመንጃን ከአንደኛው ትከሻ ወደ ሌላው መቀ የር ነው» ይላሉ ። ይህ ማለት ፤ የቡርዧው አብዮት ያስታጠቀውን ጠመ ንጃ ለቡርዧው መልሶ መስጠት ነው ። አብዮቱ የሚያስገኘውን አርነት ፣ በገባርነት ክርሰ መቃብር ላይ የሚፈልገውን ዲሞክራሲያዊ ተቋሞች ለቡርዧው መመለስ ነው ። በሌላ በኩል ደግሞ በቡርዧው ዲሞክራ ሲያዊ አብዮት አቅጣጫ ውስጥ አስፈላጊው ለውጦች ጥገናዊ ሳይሆኑ አብዮታዊ በሆነ መንገድ ቢከናወኑ ለወዝ አደሩ ታላቅ ጠቃሚ ነት አለው ። የጥገናው መንገድ የማዘግያ መንገድ ነው ። በቀጠሮ የማስተላለፍ ፣ በብሔራዊ ክፍሎች ውስጥ ተቀባይነት የሌላቸውን ቀስ በቀስ እየበሰበሱ እንዲሔዱ ማድረግ ነው ። ከእነርሱ ሥልጣን መባለግ በአንደኛውና በከፍተኛው ደረጃ የተሰቃየው ወዝአደሩና አርሶ አደሩ ነበር ። አብዮታዊው መንገድ ወዝአደሩን ጥቂት እንኳ የማይጎዳና ፣ የሚበሰብሱ ክፍሎችን በቀጥታ የማስወገድ መንገድ ፣ ለወዝአደሩና ከርሱም ጋር ለሚሄዱ ለሚያንገሸግሹ ፣ አስከፊ ፣ የበሰበሱና ፣ ለተበከሉ ተቋሞች በጣም ጥቃቅን ጥገናዎችንና ትናንሽ ግምት የሚሰጣቸው አፋጣኝ መቋረጫ መንገድ ነው ።
(ከዚህ በላይ በጠቀስነው መጽሐፍ ገጽ 368—69)

ሌኒን በመቀጠል «ለዚያ ነው ወዝ አደሩ በግንባር ቀደምትነት ለሪፓብሊክ የሚታገለውና ቡርዧውን መንከባከብ እንጂ መታገል እንደማይገባው የቂለና ዋጋ ቢስ ምክራቸውን የሚቃወመው» (ላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 405)

ወዝ አደሩ የአብዮቱ መሪ ሊሆን መቻሉን ወደ እውነትነት ለመለወጥና ወዝአደሩ በወቅቱ የቡርዧው አብዮት መሪ ኃይል ሊሆን እንዲችል ለማድረግ ቢያንስ ቢያንስ ሁለት ሁኔታዎች መሟላት አለባቸው ይላል ሌኒን ። (ላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ)

መጀመሪያ ፦ በዛሩ እገዛዝ ላይ ወሳኝ ድል መገኘቱን በሙሉ ልባቸው ከሚደግፉትና የወዝአደሩን አመራር ለመቀበል ከሚፈልጉ ጋር ሕብረት መፍጠር በጣም አስፈላጊ ነው ። ይህ ደግሞ ከአመራር ቀደምት አስተሳሰብ እንደሚነገረው የሚመራ ከሌለ መሪ መሪነቱ ያከትማል ፣ አቅጣጫ የሚቀይስ ከሌለ አቅጣጫ ቀያሹ አቅጣጫ ቀያሽነቱ ያበቃል ። ሌኒን የአርሶ አደሩን አጋርነት እንደዚህ ያለ አድርጐ ይቆጥረዋል ።

ሁለተኛ ፦ የአብዮቱ መሪ ለመሆን ወዝአደሩን የሚፋለመው መደብና የወዝ አደሩ መልካም መሪ ለመሆን የሚጥረውን ከአመራሩ መሀከል ተመንጥቆ በመውጣት ማግለሉ እጅግ አስፈላጊ ነው ። ይህም ቢሆን ከአመራር ቀደምት አስተሳሰብ እንደሚነገረው ለአብዮቱ ሁለት መሪዎች ማስፈለጋቸውን የሚሽር ነው ። ሌኒን ለዘብተኛ ቡርዧውን እንደዚህ ዓይነት መደብ ነው ይለዋል ።

«ወዝአደሮች ብቻ ናቸው ለዲሞክራሲ የማያወላዱ ቆራጥ ታጋዮች ሊሆኑ የሚችሉት» ሌኒን ሲናገር «ወዝአደሩ ድል አድራጊው የዲሞክራሲ ታጋይ ሊሆን የሚችለው ሰፊው ገበሬ በአብዮታዊው ትግል ውስጥ ሲሳተፍ ብቻ ነው» (ከዚህ በላይ በጠቀስነው መጽሐፍ ገጽ 376)

በመቀጠል ፦

«ገበሬው ከፊል—ወዝአደሮችንና የንዑስ ከበርቴ ክፍሎችን በርካታ ቁጥር አጠቃሎ የያዘ ነው ። በዚህ ምክንያት የተነሳ ወላዋይ ባሕርይ አለው ፣ በመሆኑም ወዝአደሩ በጥብቅ መደባዊ ፓርቲ በመሆን እንዲደራጅ ይገደዳል ። ይሁን እንጂ የገበሬው አለመረጋጋት የግል ንብረት ዓይነተኛ መልክ የሆነው ባለርስትነት ከቀረና መሬት ከተወረሰ ወዲህ ገበሬው የግል ንብረትን ሙሉ ለሙሉ ለመንከባከብ ያለው ፍላጐት በጣም ጥቂት ነው ። ይህ ሲባል ደግሞ ገበሬውን ለአንድ አፍታም ሶሻሊስት እንዲሆን አያደርገውም ። ወይም ንዑስ ከበርቴ ከመሆን አያግደውም ።



ገበሬው የዲሞክራሲያዊ አብዮት ሥር ነቀል ደጋፊና በሙሉ ልቡ ለአብዮቱ የቆመ ሊሆን ይችላል ። ገበሬው እንደምንለው ዓይነት ሥርነቀል የአብዮቱ ደጋፊ መሆኑ የግድ የማይቀረው ፦ የአብዮቱ ድርጊቶች ዕድገት በገበሬው ላይ ብሩህ ተስፋ ሊያሳድሩበት የቻሉ እንደሆን ብቻ ነው ፣ ወዲያውኑ በቡርዧው ተደልሎ ያልተቋረጠና ወዝ አደሩ ድል ያልተመታ እንደሆነ ብቻ ነው ።

ይህ ሁኔታ ከተሟላ ገበሬው በማያጠያ ይቅ ሁኔታ የአብዮቱና የሪፓብሊኩ መከታ ይሆናል ። እንዲሁም በተጠና ቀቀ ድል አድራጊ አብዮት ብቻ ነው የገጠሩ የለውጥ አድማስ ለአርሶ አደሩ ሁሉንም ነገር መስጠት የሚችለው ማንኛውንም ነገር የሚፈልጉትን ፣ የሚያልሙትንና በትክክልም የቆሙለትን ሁሉ ።
(ከዚህ በላይ በጠቀስነው መጽሐፍ ገጽ 405)

የሜንሼቪኮችን ተቃውሞ በመተንተን እነዚህ የቦልሼቪክ ታክቲኮች «የቡርዧው መደብ በአብዮቱ እንዳይሳተፍ ምክንያት ይሆናል ። በዚህ የተነሣ ሊገኙ የሚችሉት ድሎች ይቀንሳሉ» ና ይህተቃውሞ «አብዮቱን የመክዳት ታክቲኮች » ፣ «ወዝአደሩን ወደ ችግረኛ የቡርዧው መደብ ተጠዋሪ (ተጐታች) የሚያደርጉ ታክቲኮች » በማድረግ ባሕሪውን ይገልጻል ።

ሌኒን ሲጽፍ «በድል አድራጊው የቡርዧ አብዮት ውስጥ የገበሬውን ሚና ጠንቅቀው የተረዱ ቡርዧው በአብዮቱ ያልተሳተፈ እንዲሆን አብዮቱ የሚያስገኘው ድሎች ይቀንሳሉ ወደሚል ሕልም ውስጥ በጭራሽ አይሰጥሙም ። እንደእውነቱ ከሆነ የሩሲያው አብዮት እውነተኛ ድሉን ማሰቡን ጀምሮአል ። ቡርዧው በአብዮቱ ያልተሳተፈ እንደሆን ሰፊው ገበሬ እንደንቁ አብዮተኛ ከወዝ አደሩ ጋር ጐን ለጐን የቆመ እንደሆነ ብቻ ፣ በቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት ዘመን ውስጥ በርግጥ ሊገኝ ስለሚችለው ሰፊ አብዮታዊ ድል ያስባል ። በቆራጥነት እስከመጨረሻው ግብ ለማድረስ በዲሞክራሲያዊ አብዮታችን የማይቀረውን የቡርዧ አለመረጋጋት ለማሽመድመድ የሚችሉ እነደዚህ ባሉ ኃይላት ላይ—ማለትም ትክክለኛ በሆነ መንገድ «በአብዮቱ እንዳይሳተፍ ለማድረግ» ይቻላል ። (ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 406)

የወዝአደሩን የቡርዧ ዲሞክራሲያዊ አብዮት መሪነት በሚመለከት ረገድ ይህ ነበር ዓይነተኛው መርሆ ። የወዝአደሩን የበላይነት አስመልክቶ በቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት ውስጥ የወዝአደሩን መሠረታዊ የታክቲክ መመሪያ ፦ በዲሞክራሲያዊ አብዮት ውስጥ የሶሻል ዲሞክራሲ ሁለት ታክቲኮች በተሰኘው መጽሐፉ ሌኒን አብራርቷል ።

በቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት ውስጥ በታክቲክ ጥያቄ ላይ ይህ የማርክሳዊ ፓርቲ አዲስ የፖለቲካ መስመር ነበር ። እስከዛሬ ድረስ በማርክ

ሲዝም የታክቲክ ክምችቶች ውስጥ ከሚገኙት ታክቲካዊ መስመሮች መሠረታዊ በሆነ መንገድ የተለየ መሥመር ሲሆን በቡርዧው አብዮት ውስጥ ቢፊትየነበረው ሁኔታ—ስምሳሌ በምዕራብ አውሮፓ—የግንባር ቀደም መሪነቱን ሚና ይጫወት የነበረው ቡርዧው ነበር ። ወዝአደሩ ወደደም ጠላም የቡርዧው ደጋፊ የሆነ ሚና ሲጫወት ገበሬው ደግሞ የቡርዧው ተጠባባቂ ነበር ። ማርክሲስቶች እንዲህ ዓይነቱን ውሕደት በዛም አነሰም መሆን ያለበት ነው ይሉታል ። ከዚሁ ጋር ወዝአደሩ ለራሱ መደብ ወቅታዊ ዓላማ ለመታገል እንዲችል የራሱን ፖለቲካዊ ፓርቲ የግድ ማስፈለጉን ያወሳሉ ። አሁን በአዲስ ታሪካዊ ሁኔታ እንደሌኒን አስተሳሰብ ወዝአደሩ የቡርዧው አብዮት መሪ ሀይል በሚሆንበት መንገድ ሁኔታው ተለውጧል ። ቡርዧው ከአብዮቱ አመራር ጠርዝ ሲወጣ ገበሬው ደግሞ የወዝአደሩ ተጠባባቂ ኃይል ይሆናል ።

ለወዛደሩ የበላይነት ተቃውሞ ፕሌክሀኖቭ «ጭምር የቆመለት» ነገሩን ጠንቅቆ ካለመገንዘብ የመነጨ ነው ። የወዝአደሩን የበላይነት አስተሳሰብ ፕሌክሀኖቭ አስተሳሰቡ ቢዋጥለትም ቃሉን እንዳለ መቀበሉን ይቃወማል ። —ያ ደግሞ ትክክል ነው ። ይሁን እንጂ ፕሌክሀኖቭ እንደ እውነቱ ከሆነ ያልተዋጠለት ቃሉ ብቻ ሳይሆን ይዘቱንም ጭምር ይቃወማል ። የወዝ አደሩ የበላይነት የሚለው አስተሳሰብ የሚያሳየው በቡርዧው አብዮት ውስጥ ወዝአደሩ የሚኖረው የመሪነት ሚናና በወዝአደሩና በገበሬው መሀከል አጋርነት በመፍጠር መመሪያና ለዘብተኛ ቡርዧውን በማግለል መመሪያ መታጀቡን ነው ። ፕሌክሀኖቭ እስከምናውቀው ድረስ ለዘብተኛ ቡርዧውን የማግለል መመሪያ በመቃወም በተቃራኒው ከለዘብተኛ ቡርዧው ጋር ስምምነት የማድረግ መመሪያን የሚደግፍና በወዝአደሩና በገበሬው መሀከል ሕብረት የመፍጠርን መመሪያ በጥብቅ የሚቃወመው ነው ። እንደ እውነቱ ከሆነ የፕሌክሀኖቭ ታክቲካዊ መስመር የወዛደሩን የበላይነት ከሚያወግዙት ከሜንሼቪኮች መስመር የሚጣጣም እንጂ አንዳችም ልዩነት የለውም ።

2/ ሌኒን ሲያስገነዝብ የዛሩን አገዛዝ ገርስሶ ዲሞክራሲያዊ ሪፓብሊክ ለመመሥረት እጅግ ፍሬአማ የሆነው መንገድ ድል አድራጊው ሕዝባዊ ትጥቃዊ አመጽ ነው ብሏል ። ከሜንሼቪኮች በአንጻራዊ ቆሞ ሌኒን ሲናገር ፦«የአጠቃላይ ዲሞክራሲያዊ አብዮት ንቅናቄ የትጥቃዊ አመጽን አስፈላጊነት በሚገባ አሳይቶናል» ፣«ማለትም የወዝአደሩ የአመጽ ድርጅቶች እንደ አንዱ አስፈላጊ ፣ ዋነኛና ፣ የማይዘሉት የፓርቲው ተግባር በመሆን ወቅቱ በሚያዘው መሠረት ቦታቸውን ይዘዋል» «ወዝአደሩን ማስታጠቅና የአመጸው ቀጥተኛ የመሪነቱን ችሎታ ለማረጋገጥ እጅግ ኃይለኛ የሆነውን እርምጃ መውሰድ» አስፈላጊ ነበር ።
(ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 386)

ሰፊውን ሕዝብ ወደ አመጻው ለመምራትና ወደ የመላው ሕዝብ (አጠቃላይ) አመጽ ለመለወጥ አብዮታዊ መነሳሳት እንዲደረግ ሰፊውን ሕዝብ የማጥራት ተግባር ፣ አመጻው መደራጀት ፣ ብሎም የዛሩን ጠንካራ መኪና ማፈራረስ ፣ እንደነዚህ ያሉትን መፈክሮች ማንሳት እጅግ አስፈላጊ መሆኑን ሌኒን አበክሮ ይናገራል ። በዲሞክራሲያዊ አብዮት ውስጥ የሶሻል—ዲሞክራሲ ሁለት ታክቲኮች በተሰኘው መጽሐፉ ለመከላከል የተሰዋለት የሶስተኛው የፓርቲ ኰንግሬስ ታክቲካዊ ውሳኔ እንደ ነዚህ ያሉ መፈክሮችን ሰንዝሮ እንደነበረ አስገንዝቦአል ።

የሚያወሳቸውም መፈክሮች የሚከተሉት ናቸው ።

ሀ/ «በመጀመሪያና በአመጽ ቀደምት ሂደቶች ውስጥ ታላቅ ጠቃሚ ነት የሚኖራቸው የሰፊው ሕዝብ ፖለቲካዊ አድማዎች»
(ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 386)

ለ/ «ሥምንት የሥራ ሰዓትና ሌሎችም የሠራተኛው መደብ ወቅታዊ ጥያቄዎችን አብዮታዊ በሆነ መንገድ በአስቸኳይ ማረጋገጥ»
(ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 358)

ሐ/ «መላውን ዲሞክራሲያዊ» ለውጦች የመሬትን መውረስ ጨምሮ አብዮታዊ የገበሬ ኮሚቴዎች በአስቸኳይ ማደራጀት»
(ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 398)

መ/ ሠራተኞችን ማስታጠቅ ።
በተለይ ሁለቱ ነጥቦች የተለየ ስሜት አላቸው ።

የመጀመሪያው ፦ ሥምንት የሥራ ሰዓትን በከተሞችና ዲሞክራሲያዊ ለውጥ በገጠሮች አብዮታዊ በሆነ መንገድ ማረጋገጥ ማለት ከባለሥልጣኖች ውጪ ከሕግ ውጪ ባለሥልጣኖችንና ሕጉን ቸል በማለት ሕጉን በመጣስ ገናና በሆነ እርምጃ ድል በማድረግ አዲስ ስርዓት መመስረት ነው ። ይህ ነበር የዛሩን መንግሥታዊ መኪና ኃያልነት በማሽመድመድና የሰፊውን ሕዝብ እንቅስቃሴና ፈጠራዊ አነሳሽነት ነጻ ሊያወጣ የሚችለው አዲሱ ታክቲካዊ መንገድ ። እነዚህም ታክቲኮች ነበሩ በከተማዎች ለአብዮታዊ የአድማ ኮሚቴዎች እንዲሁም በገጠሩ ለአብዮታዊ የገበሬ ኮሚቴዎች አነሳሽ የሆኑት ። የመጀመሪያው ዘግየት ብሎ ወደ የሠራተኛ ሶቭየቶች መማከርት ሲያድግ ሁለተኛው ደግሞ ወደየገበሬዎች ሶቭየቶች መማክርት አደገ ። ሁለተኛ ፦ በሰፊው ሕዝብ ፖለቲካዊ አድማ መጠቀም ፣ በአጠቃላይ ፖለቲካዊ አድማ መጠቀም ፣ በተለይም በኋለኛው የአብዮት ሂደት ውስጥ ለሰፊው ሕዝብ አብዮታዊ እንቅስቃሴ የመጀመሪያው ጠቃሚነት አለው ። ይህ ነበር በወዝአደሩ እጅ ላይ የሚገኘው አዲስና እጅግ ጠቃሚው መሣሪያ ። በማርክሳዊ ፓርቲ ተግባር ውስጥ እስካሁን ያልታወቀ ተቀባይነት ያተረፈ መሣሪያም ነበር ።

ሌኒን የሕዝቡን ድል አድራጊ አመጽ በመከተል የዛሩ አገዛዝ በጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥት መተካት አለበት ሲል ተናገረ ። የአብ ዮቱን ድሎች ማጠናከር ፣ የፀረ-አብዮት ኃይላትን የመከላከል አቅም ቅስ ሙን ለመስበርና የሩሲያ—ሶሻል ዲሞክራቲክ የሠራተኞች ፓርቲ መለ ስተኛ መርሀ ግብር ፍሬአማ ማድረግ የጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥት ተግባር መሆን አለበት ። እነዚህ ተግባሮች ካልተጠናቀቁ በዛሩ አገዛዝ ላይ ወሳኝ ድል ለመቀዳጀት የማይቻል መሆኑን ሌኒን አስገነዘበ ። ብሎም ይህንን ተግባር ለማጠናቀቅና በዛሩ አገዛዝ ላይ ወሳኝ ድል ለመቀዳጀት ከተፈለገ የሚመሠረተው ጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥት የበፊቱ ዓይ ነት (የተለመደ ዓይነት) መሆን የለበትም ። ነገር ግን ጊዜያዊ መንግሥት የድል አድራጊው መደብ መንግሥት ፣ የሠራተኛውና የገበሬው መንግ ሥት ፣ የወዝአደሩና የገበሬው አብዮታዊ አምባገነን መሆን አለበት ። የማ ርክስን እውቅ በኩረ-ሃሣብ ስንጠቅስ «ከአብዮት በኋላ ማናቸውም የመ ንግስቱ ጊዜያዊ ድርጅቶች አምባገነንነትን ይሻሉና ሀይል የተሞላበት አምባገነንነት ያስፈልገዋል» ይለናል ። ሌኒን ጊዜያዊ አብዮታዊ መን ግሥት በዛሩ ላይ ወሳኝ ድል የተቀዳጀ እንደሆን የወዝአደሩና የገበሬው አምባገነንነት እንጂ ሌላ ምንም ሊሆን አይችልም ወደሚለው መደ ምደሚያ ደረሰ ።

«የአብዮቱ በዛሩ አገዛዝ ላይ ወሳኝ ድል መቀዳጀት የወዝ አደሩና የገ በሬው አብዮታዊ ዲሞክራሲያዊ አምባገነንነት ነው» ይላል ሌኒን «. . . እናም እንዲህ ያለ ድል በትክክል አምባገነንነት ይሆናል ። ያ ማለት በማያ ጠያይቅ ሁኔታ በወታደራዊ ኃይል ላይ ፣ ሰፊውን ሕዝብ በማስታጠቅ ላይ ፣ በአመጽ የሚያርፍ እንጂ 'በሕጋዊ' ወይም 'በሰላማዊ' መንገድ በተመሠረቱ አንድ ወይም ሌላ ዓይነት ተቋሞች ላይ የሚያርፍ አይደለም ። አምባገነን ሊሆን የሚችለው አፋጣኝና ፍጹም ሊዘለሉ የማይችሉትን ለውጦች ለማስ ከበርና ፣ የመሬት ከበርቴዎች ፣ ታላቁ ቡርዧና ዛሩ ለመከላከል ለሚያ ደርጉት ቀቢፀ ተስፋ ለማረጋገጥ ብቻ ነው ። ያ አምባገነንነት ይህን የአ ድኃሪያንን መቋቋም ለመደርመስና የፀረ አብዮተኞችን ጥረት ለማንበ ርከክ አይቻልም ። ይሁን እንጂ በርግጥ የሚመሠረተው አምባገነንነት ዲሞክራሲያዊ እንጂ ሶሻሊስታዊ አምባገነንነት አይደለም ። የካፒታ ሊዝምን መሠረቶች ለማናጋት (ያለ ተከታታይ የአብዮቱ የሽግግር ደረጃ ዕድገት) የሚቻል አይደለም ። ምርጥነቱ ለገበሬዎች መሬትን ያከፋፍ ላል ። ጠንካራና ሙሉ ዲሞክራሲን ፣ የሪፓብሊክን መቋቋም አዳምሮ ይመሠርታል ። በመንደር ብቻ ሳይሆን ፤ ነገር ግን በፋብሪካ ኑሮ ውስጥ ፣ መላውን እስያዊ የጭቆና ሀረግ በማስወገድ ፣ ሠራተኞችን ከሚገኙበት ሥፍራ ለማሻሻልና የኑሮ ደረጃቸውን ለማሳደግ መሠ ረት ይጥላል እንዲሁም የአብዮቱን ቋያ ወደ አውሮፓ ያዛምታል ። እንዲህ ዓይነቱ ድል በምንም ዓይነት መንገድ የቡርዧ አብዮታችንን ወደ ሶሻሊስት አብዮት እንዲሸጋገር ያደርጋል ። ዲሞክራሲያዊ አብ

ዮት የቡርዧውን የሶሻልና የምጣኔ-ሀብታዊ ግንኙነትን ገደብ በቀጥታ አይዘልም ። ይሁን እንጂ እንደዚህ ያለ ድል ለሩሲያ የወደፊት ዕድገት ጠቃሚ ከመሆኑም በላይ ለመላው ዓለም ታላቅ አስተዋጽኦ ይኖረዋል ። በሩሲያ ውስጥ አሁን ከሚካሄደው ወሳኝ የአብዮት ድል ሌላ የዓለምን ወዝአደሮች ጥንካሬ ይህን ያህል የሚያሳድግ ምንም ነገር የለም ። ለአጠቃላዩ ወሳኝ ድል የሚወስደውን መንገድ እንደዚህ የሚያሳጥረው አንዳችም ነገር የለም» ። (ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 373)

ጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥትን አስመልክቶ የሶሻል ዲሞክራቶች አዝማሚያና በዚሁ መንግሥት ውስጥ መሳተፉ የሚፈቀድ እንደሆነ፥ ሌኒን የሶስተኛ ፓርቲ ኰንግሬስ በዚሁ ርዕስ ያሳለፈውን ውሳኔ ይደግፋል ።

«በሐይሎች ግንኙነት ርእስና በድርጊት ከመዋላቸው በፊት በቀጥታ ሊወሰኑ የማይገባቸው ሁኔታዎች ሁሉንም የፀረ-አብዮት ጥረቶች ለመቃወም የሠራተኛውን መደብ ፍላጐት ለመንከባከብ ቆራጥ ትግል ማካሄድ እንዲቻል የፓርቲያችን ተወካዮች በሚመሠረተው ጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥት ውስጥ መሳተፍ አለባቸው ። እንደዚህ ላለው ተሳትፎ እጅግ አስፈላጊ ሁኔታ ፓርቲውን ወክለው በጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥት ውስጥ በሚገቡት አባሎች ላይ ፓርቲው ጠንካራ ቁጥጥር ማድረግ ይኖርበታል ። ለተጠናቀቀ ሶሻሊስት አብዮት የሚጥረውና ከመላው ጠላት ቡርዧ ፓርቲዎች ጋር ከቶም የማይታረቀውን የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ነጻነት በሚገባ መጠበቅ አለበት ። ምንም እንኳ ሶሻል ዲሞክራቶች በጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥት ውስጥ ለመሳተፍ መቻሉን ወይም አለመቻሉን ቢያረጋግጡም በጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥት ውስጥ በመሳተፍ በሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ እየተመራ ለመከላከልና የአብዮቱን ድሎች ለማቆየት በታጠቁ ወዝአደሮች የማያቋርጥ ግፊት ማድረግ እንደሚገባን በሰፊው ወዝአደር መሀከል ማስፋፋት አለብን» (ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 348—49)

እንደሜንሼቪኮች ተቃውሞ ከሆነ ጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥት አሁንም ቢሆን የቡርዧው መንግሥት ነው የሚሆነው፥ ሶሻሊስት ሚሊራንችዶ በፈረንሣይ የቡርዧው መንግሥት ውስጥ እንደተሳተፉ ሁሉ ደግሞ ይህንን ስህተት ለመፈጸም ካልሆነ በቀር እንደዚህ ባለው መንግሥት ውስጥ ሶሻል ዲሞክራቶች ለመሳተፍ ሊፈቀድላቸው ጨርሶም አይገባም ። እዚህ ላይ ሜንሼቪኮች ሁለት ጨርሶ የተለያዩ ነገሮችን ከማቀላቀላቸውም በላይ ጥያቄውን እንደማርክሲስቶች ለማስተናገድ ያላቸውችሎታ መክዳታቸውን ሌኒን በመግለጽ ተቃውሞአቸውን አገለለው ። በፈረንሣይ አብዮታዊ ሁኔታ ባልነበረበት ወቅት በአድኃሪው የቡርዧ መንግሥት ውስጥ መሳተፍ የሶሻሊስቶች ጥያቄ ነበር ። እንዲህ

ባለው መንግሥት ውስጥ አለመሳተፍ በሶሻሊስቶች ጫንቃ ላይ እንዲያርፍ
ሆኖ ነበር ። በሌላ በኩል በሩሲያ ውስጥ አብዮቱ ሙሉ ለሙሉ በሚ
ዋልልበት ወቅት ለአብዮቱ ድሎች ለመታገል በአብዮታዊ የቡርዧ
መንግሥት ውስጥ መሳተፍ የሶሻሊስቶች ጥያቄ ሆነ ። ይህንን ለማድረግ
ሁኔታው የሚፈቅድለትና በአመቺ ሁኔታ ውስጥ እንደዚህ ባለው መንግ
ሥት በመሳተፍ «ከታች» ብቻ ፣ ከውጪ ሳይሆን «ከላይ» በመንግሥቱ
ውስጥ በመሆን ፀረ-አብዮትን በሚገባ ለመምታት መቻል በሶሻል
ዲሞክራቶች ትክሻ ላይ ወድቋል ።

3/ የቡርዧውን አብዮት ድልና የዲሞክራሲያዊ ሪፓብሊክን መመ
ሥረት በሚያወሳበት ወቅት ሌኒን ፣ በዲሞክራሲያዊ ደረጃው ለመግታ
ትና የአብዮታዊ ንቅናቄውን አውድ በቡርዧው ዲሞክራሲያዊ ተግባር
አልደመደመውም ። በተቃራኒው ሌኒን የተጠናቀቀውን ዲሞክራሲያዊ
ተግባር በመከተል ወዝአደሩና የተቀረው መላው ምዝብር ሕዝብ ትግ
ላቸውን መጀመር አለባቸው ። በአሁኑ ወቅት የሚያደርጉት ትግል ለሶሻ
ሊስት አብዮት የሚደረግ ትግል ነው ሲል አስገነዘበ ። ይህንን ጠንቅቆ የሚ
ያውቅና የቡርዧውን ዲሞክራሲያዊ አብዮት ወደ ሶሻሊስት አብዮት
ለማሸጋገር ማንኛውንም ነገር ማከናወኑ የሶሻል ዲሞክራቶች ተግባር
በማድረግ ሌኒን ይመለከተዋል ። ሌኒን ይህንኑ በመደገፍ ሲናገር የወዝ
አደሩና የገበሬው አምባገነንነት ያስፈለገው አብዮቱ በዛሩ አገዛዝ ላይ ያገ
ኘውን ድል ፍሬ በመጠቀም ደረጃ እንዲያከትም አይደለም ። ነገር ግን
የአብዮቱን ሁኔታ ማራዘም እንዲቻል የጸረ-አብዮትን የመጨረሻ
ምሽግ ድባቅ ለመምታት ፣ የአብዮቱ ቋያ በአውሮፓ እንዲቀጣጠል ለማ
ድረግና በሚኖረው ጊዜ ውስጥ ወዝአደሩ በፖለቲካ ራሱን እንዲያስተ
ምርና ራሱን በታላቅ ሠራዊት እንዲያደራጅ እድል ለመስጠትና ወደ
ሶሻሊስት አብዮት ቀጥተኛ የሆነ ሽግግር ለመጀመር ነው ።

የቡርዧውን አብዮት አውድና ማርክሲስት ፓርቲ ስለሚኖረው
ባሕርይ አስመልክቶ ሌኒን ሲጽፍ ፣

«የፈላጭ ቆራጩን አገዛዝ የመቋቋም አቅም ለመስበርና የቡርዧ
ውን መዋዠቅ ለመግታት ወዝአደሩ ከሰፊው ገበሬ ጋር ህብረት በመ
ፍጠር ዲሞክራሲያዊ አብዮቱን ማጠናቀቅ አለበት ። የቡርዧውን
የመቋቋም አቅም ለማዳሸቅና የገበሬውን እንዲሁም የንዑስ ከበርቴውን
መዋለል ለማስቀረት እንዲቻል ከፊል ወዝአደር የሆነውን ሕዝብ ክፍል
ከራሱ ጋር በማስተባበር ወዝአደሩ ሶሻሊስት አብዮቱን ማጠናቀቅ
አለበት ። እንግዲህ እነዚህ ናቸው ማለትም አዲሱ ኢስክራይስቶች (ሜንሼ
ቪኮች) ስለአብዮቱ አውድ ሁልጊዜ እጅግ ጠባብ የሆነ ክርክራቸውንና
ውሳኔያቸውን የሚያቀርቡት »። (ከዚህ በላይ በጠቀስነው መጽሐፍ ገጽ 406)
እናም በመቀጠል ፣—

«በመላው ሕዝብ መሪነትና በተለይም በገበሬው ለተረጋገጠ ነጻነት
ለፍጹም ዲሞክራሲያዊ አብዮት፣ ለሪፑብሊክ ፣ በመላው ሠራተኞችና በተበ



ዘበዙ ሕዝቦች መሪነት ለሶሻሊዝም ፣ ይህ አብዮታዊ ወዝአደር በተግባር
ማዋል ያለበት መመሪያ ነው ። ይህ እያንዳንዱን ታክቲካዊ ችግሮች መፍ
ትሄ የሚሰጥና የሚወስን መደባዊ መፈክር ነው ።»
ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 415)

እንዳችም ነገር ተድበስብሶ እንዳይቀር ሁለቱ ታክቲኮች የተሰኘው
መጽሐፍ ታትሞ ከወጣ ከሁለት ወራት በኋላ ሌኒን «ለአርሶ አደሩ እንቅ
ስቃሴ የሶሻል ዲሞክራቶች አዝማሚያ» በሚል ርእስ በጻፈው ጽሁፉ
እንደገለጸው ፤

«ልክ እንደ ጥንካሬአችን መጠን በንቃው መደብ ጥንካሬነትና
በወዝአደሩ መደራጀት በአንድ ጊዜ ከዲሞክራሲያዊ አብዮት ወደ
ሶሻሊስት አብዮት ለመሸጋገር እንችላለን ። እኛ የቆምነው ለማያቋርጥ
አብዮት ነው ። እኛ በግማሽ መንገድ ላይ የምንቆም አይደለንም ።»
(ከዚህ በላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 442)

በቡርዧው አብዮትና በሶሻሊስት አብዮት መሀከል ባለው የግንኙ
ነት ጥያቄ ውስጥ የቡርዧውን አብዮት መደምደሚያ አስመልክቶ ወደ
ሶሻሊዝም ለሚደረገው ቀጥተኛ ሽግግር—የቡርዧውን ዲሞክራሲያዊ
አብዮት ንድፈ-ሀሳብ ወደ ሶሻሊስት አብዮት ውስጥ ማስተላለፍ ፣
እንግዲህ ይህ ነበር ። አዲሱ መስመር ።

ይህንን አዲስ መስመር ተግባራዊ ለማድረግ ሌኒን በመጀመሪያ
ራሱን መሰረት ያደረገው ካርል ማርክስ በ1840 ዎቹ መጨረሻ ስለ የማ
ያቋርጥ አብዮት ታዋቂ በኩረ ሀሳቡ ለኮሚኒስት ሊግ ባደረገው ንግግር
ላይ ነው ። ሁለተኛ ደግሞ ፡— በ1856 ዓ.ም. ካርል ማርክስ ለፍሬድሪክ
ኤንግልስ የገበሬውን ንቅናቄ ከወዝአደሩ አብዮት ጋር ማዋሀድ እንደሚ
ያስፈልግ እውቅ ሀሳቡን በደብዳቤ ሲገልጽ ፡— «በጀርመን ውስጥ ሁሉም
ነገር አንዳንድ የገበሬዎች ጦርነትን በመድገም የወዛደሩን አብዮት በመ
ደገፍ ችሎታ ላይ የሚወሰን ነው» ብሏል ። ቢሆንም ቅሉ የሁለተኛው
ዓለም አቀፍ ንድፈ-ሀሳባውያን እነዚህ ሀሳቦች እንዲታፈኑና ጨርሰው
እንዲዘነጉ የተቻላቸውን ሁሉ በሚጥሩበት ወቅት እነዚህ በሳል የማ
ርክስ አስተሳሰቦች በማርክስና በኤንግልስ ስራዎች ውስጥ በመቀጠል
አላደጉም ። እነዚህን የተዘነጉ የማርክስ ሀሳቦች ብሩህ የማድረጉ ሙሉ
መብታቸውን የማጐናጸፉ ተግባር በሌኒን ትከሻ ላይ ወደቀ ። ይሁን
እንጂ እነዚህ ማርክሳዊ ሀሳቦች እንዲያንሰራሩ በሚጥሩበት ወቅት ሌኒን
እነርሱኑ በመደጋገም ላይ አልተወሰነም ሊወስንም አይችልም ።
በእንጻሩ ይበልጥ እንዲዳብሩ በማድረግና አዳዲስ እውነቶችን በማቅረብ
ወደ አሸብራቂ የሶሻሊስት ንድፈ-ሀሳብ ቀረጻቸው ። እንዲሁም ወዝአደሩ
በሀገሪቷ ከሚገኙ ከፊል ወዝአደሮች ጋር ሕብረት መፍጠር ለወዝአ
ደሩ አብዮት ድል አድራጊነት አመቺ ሁኔታ መሆኑን ለሶሻሊስት
አብዮት እጅግ አስፈላጊ መሠረቶች መሆናቸውን አስገነዘበ ።

ከቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት በኋላ ገበሬው ፣ ደሀ ገበሬዎችንም
አዳምሮ አብዮቱን ይከዳሉ ። በዚህም የተነሳ ከሀምሳና ከመቶ ዓመታት

ያላነሰ የተራዘመ ጣልቃ ስለሚያስከትል ረዘም ላለ ጊዜ « ጸጥታ » ይሰ
ፍናል ። በዚህም ወቅት ወዝአደሩ « ሰላማዊ በሆነ መንገድ » የሚበዘበ
ዝበትና ቡርዧው ደግሞ « ሕጋዊ በሆነ መንገድ » ሌላ ዙር አዲስ ሶሻ
ሊስት አብዮት እስከሚመጣ ድረስ ራሱን ያበለጽጋል በሚለው እምነ
ታቸው የምእራብ አውሮፓ ሶሻል ዲሞክራቶች ታሪካዊ አቋም በዚህ
መስመር ተጋረደ ።

የሶሻሊስት አብዮት የሚጠናቀቀው ገለልተኛው ወዝአደር በመ
ላው ቡርዧ ላይ በሚያደርገው ተቃውሞ ሳይሆን ፣ ነገር ግን የህዝቡ
ክልል ከሆነው ከከፊል ወዝአደር ፣ « ከሠርቶ አደሩ ሚሊዮን ምዝብር
ሕዝቦች » ጋር ሕብረት በመፍጠርና የወዝአደሩ መሪ መደብ በመሆን
እንደሆነ የሚያበስር አዲስ ንድፈ-ሀሳብ ነው ።

እንደዚህ ንድፈ-ሀሳብ ከሆነ በቡርዧው አብዮት ውስጥ የወዝ
አደሩ የበላይነት ከገበሬው ጋር ሕብረት በመፍጠር የሶሻሊስት
አብዮት ወደ ወዝአደሩ የበላይነት ያድጋል ። ወዝ አደሩ በአሁኑ ጊዜ
ከሌሎች ሰራተኞችና ምዝብር ሕዝቦች ጋር ህብረት ሲፈጥር የወዝአደ
ሩና የገበሬው ዲሞክራሲያዊ አምባገነንነት እንደዚሁ ለወዝአደሩ ሶሻ
ሊስት አምባገነንነት አመቺ መሠረት ያዘጋጃል ።

የሀገሪቷን አብዮታዊ ወዝአደሮች የሆኑትን ከፊል ወዝአደሮች የካ
ዱትና « ከቡርዧውና ከወዝአደሩ በቀር በሀገራችን ተቃዋሚ አሊያም
አብዮታዊ ውህደት በማድረግ ድጋፍ ሊያስገኙ የሚችሉ አሉ ብለን የም
ንቀበላቸው ሌላ አንዳችም የሕብረተሰብ ሀይሎች የሉም » በሚሉት
የምእራብ አውሮፓ ሶሻል ዲሞክራቶች አካባቢ የሚነፍሰውን ንድፈ-
ሀሳብ ይቃወማል ።(እነዚህን የፕሌክሀኖቭ ቃላት ነበሩ የምዕራብ አው
ሮፓ ሶሻል ዲሞክራቶች የሚያስተጋቡት) የምእራብ አውሮፓ ሶሻል
ዲሞክራቶች በሶሻሊስት አብዮት ውስጥ ወዝአደሩ ከመላው ቡርዧ ፣
ወዝአደር ካልሆኑት መደቦችና የህብረተሰብ ክፍሎች ጋር በሚያደ
ርገው ትግል ሕብረት ሳይፈጥር ብቻውን መቋቋም እንዳለበት ያወሳሉ ።

በካፒታሊዝም አስከፊ ጥፍሮች የተጧጠጠው ማነው ? ፣ ሕብረተሰ
ቡን ከካፒታሊዝም የብዝበዛ ቀንበር ነጻ ለማውጣት የወዝአደሩ አጋር
ሊሆን የሚችለው ማነው ? ፣ ካፒታል ወዝአደሩን ብቻ ሳይሆን በሚሊ
ዮን የሚቆጠረውን የሀገሪቷን ከፊል ወዝአደሮች ጭምር የመበዝበዙን
ሀቅ ከቁም ነገር አይቆጥሩትምና የምእራብ አውሮፓ ሶሻል ዲሞክ
ራቶች በአውሮፓ ውስጥ ሶሻሊስት አብዮት ለማካሄድ ሁኔታው ገና
ጥሬ ነው (አመቺ ሁኔታ አልተፈጠረም) በማለት ይናገራሉ ። ለነርሱ
ሁኔታው የለማ የሚሆነው ህብረተሰቡ በምጣኔ-ሀብታዊ እድገቱ ከመቼ
ውም ጊዜ የበለጠ ሲያድግና በዚህም ምክንያት የህብረተሰቡ አብዛኛው
ክፍል ሲሆን ብቻ ነው ።



ይህ አስመሳይ የምእራብ አውሮፓ ሶሻል ዲሞክራቶች ጸረ-ወዝ
አደር አቋም በሌኒን የሶሻሊስት አብዮት ንድፈ-ሀሳብ ደግሞ ላያንሰ
ራራ ተደቁሷል ።

በአንድ አገር ውስጥ ሶሻሊስት አብዮት ድል ማድረግ መቻሉን
አስመልክቶ የሌኒን ንድፈ-ሀሳብ አንዳችም ቀጥተኛ የሆነ ማጠቃለያ
አልያዘም ። ነገር ግን እንደዚህ ዓይነቱን መደምደሚያ ለመስጠት የሚያ
ስችሉ አብዛኛውን ወይም ሁሉንም የያዙ መሠረታዊ ነገሮች ነበሩት ።

እንደምናውቀው ሌኒን ወደዚህ መደምደሚያ የደረሰው ከአሥር
ዓመት በኋላ በ1915 ዓ. ም. ነበር ።

በዲሞክራሲያዊ አብዮት ውስጥ የሶሻል ዲሞክራሲ ሁለት ታክቲ
ኮች በተሰኘው ታሪካዊ መጽሀፉ ሌኒን ያብራራቸው መሰረታዊ መመሪ
ያዎች እነዚህ ነበሩ ።

የዚህ ታሪካዊ መጽሀፍ ጠቃሚነት ከሁሉም በላይ በውስጡ የሚን
ሼቪኮችን የንዑስ ከበርቴ መስመር በርእዮተ-ዓለም በማንበርከክ ለቡር
ዧው አብዮት የበለጠ እድገት ፣ በዛሩ አገዛዝ ላይ የማይበገር ማጥቃት
ለማድረግ ፣ የሩስያን ሰራተኛ መደብ አስታጠቀ ። እንዲሁም የቡርዧ
ውን አብዮት ወደ ሶሻሊስት አብዮት የመሸጋገሩን አስፈላጊነት የሩስያ
ሶሻል ዲሞክራቶች በግልጽ እንዲያዩት ግልጥልጥ አደረገላቸው ።

ይሁን እንጂ በዚህ ብቻ የሌኒን መጽሐፍ ተፈላጊነቱን አላጣም ።
ዋናው ጠቀሜታው ማርክሲዝምን በአዲስ ንድፈ-ሀሳብ ከማበልጸጉም
ሌላ በ1917 የአገራችን ወዝአደሮች በካፒታሊዝም ላይ ድልን ለመቀዳ
ጀት የረዳውን የቦልሼቪክ ፓርቲ አብዮታዊ ታክቲኮች ጠንካራ
መሰረት ጣለ ።

4/ <u>የአብዮቱ በከፍተኛ ደረጃ መቀጣጠል ፣ የ1905ቱ ዓ. ም. የመላው
ሩሲያ ፖለቲካዊ የሥራ ማቆም አድማ ፣ የንጉሣዊው አገዛዝ ማፈግፈግ ፣
የዛሩ መግለጫ ፣ የሠራተኞች ተወካዮች ሶቭየቶች መመሥረት ፣</u>

በ1905 ዓ. ም. የበልግ ወራት አብዮታዊ ንቅናቄ መላውን አገር
አናወጠ ፣ ወዲያውም ጥንካሬ እያገኘ መጣ ።

በመስከረም 19 ቀን የአታሚዎች የሥራ ማቆም አድማ በሞስኮ
ውስጥ ፈንድቶ ወደ ቅዱስ ፒተርስበርግና ወደ ሌሎችም አያሌ ከተሞች
ተዛመተ ። ሌላው ይቅርና በዚያው በሞስኮ ውስጥ የአታሚዎችን የሥራ
ማቆም አድማ የሌላ ፋብሪካ ሰራተኞች ስለደገፉት ወደ አጠቃላይ ፖለቲ
ካዊ አድማ አደገ ።

በጥቅምት ወር መባቻ በሞስኮ–ካዛና የባቡር ሠራተኞች የተጀ
መረው የሥራ ማቆም አድማ በሁለት ቀናት ውስጥ የሞስኮ
የባቡር መስመር መጋጠሚያ ሠራተኞች ተባበሩት ። በዚህ ብቻ አላበ
ቃም ወዲያውኑ የመላው ሀገሪቷ የባቡር ሠራተኞች ከእንቅስቃሴው ጐን
ቆሙ ። የፖስታና የቴሌግራፍ አገልግሎቶች ተቋረጡ ። በእያሌ የሩስያ
ከተሞች ሰራተኞች ትላልቅ ስብሰባዎች በማድረግ ስራ ላለመስራት ወሰኑ፣
አድማው ከአንዱ ፋብሪካ ወደ ሌላኛው ፋብሪካ ፣ ከአንዱ ወፍጮ ፤ ወደሌ
ላኛው ወፍጮ ከአንዱ ከተማ ወደ ሌላው ከተማ ፣ ከአካባቢ ወደ አካባቢ
እየተዛመተ ተስፋፋ ። ተማሪዎችና ምሁራን ፡— ጠበቆች ፣ ኢንጂነሮ
ችና ዶክተሮች—የሰራተኛውን አድማ በመደገፍ ተሳተፉ ።

የጥቅምቱ ፖለቲካዊ አድማ መላውን ሀገር ፣ እጅግ ኋላቀሩን የሕ
ብረተሰብ ክፍል አዳምሮ ያቀፈ የመላው ሩስያ የሥራ ማቆም አድማ
ለመሆን በቃ ። በአጠቃላይ ፖለቲካዊ አድማው የባቡር ሰራተኞችን ፣
የፖስታና የቴሌግራፍ እንዲሁም ሌሎችንም ሠራተኞች ሳይጨምር በሚ
ሊዮን የሚቆጠሩ የኢንዱስትሪ ሰራተኞች ብቻ ተሳትፈውበታል ። መላው
የአገሪቷ እንቅስቃሴ ቀጥ አለ ። መንግሥቱ ተዳከመ ።

የንጉሡን ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ በመቃወም የሚደረገው የሰፊው
ሕዝብ እንቅስቃሴ በወዝ አደሩ ተመራ ።

የሰፊውን ሕዝብ ፖለቲካዊ አድማ የመራው የቦልሼቪኮች መፈክር
መልካም ፍሬ አፈራ ።

የጥቅምቱ አጠቃላይ አድማ የወዝአደሩ ጥንካሬ ምን ያህል እንደ
ሆነ ግልጥልጥ አድርጐ ከማሳየቱም ሌላ ሞራሉ የላሸቀው ዘውዳዊው አገ
ዛዝ የጥቅምት 17 ቀን 1905 ዓ. ም. መግለጫ እንዲያወጣ ተገደደ ። መግ
ለጫው « የማይናወጡትን የሲቪል አርነቶች የሰዎችን ልዕልናና የመ
ንቃት ፣ የመናገር ፣ የመሰብሰብና የመደራጀት ነጻነት» እንዲከበሩ ቃል
ከመግባቱም በላይ ሕግ መወሰኛ ለማሰባሰብና ለመላው የሕብረተሰብ
መደቦች የመምረጥ መብት እንደሚያሻሽል ቃል ገባ ።

ሆን ተብሎ የተዘጋጀው የቡልጂን ዱማ በአብዮቱ ማእበል ተሽቀ
ንጥሮ ተጣለ ። የቡልጂኑን ዱማ ላለመሳተፍ ቦልሼቪኮች የወሰዱት ታክ
ቲካዊ እርምጃዎች ትክክለኛነታቸው በሚገባ ተረጋገጠ ።

የጥቅምት አስራሰባቱ መግለጫ በሕዝቡ ላይ የማጭበርበር ወንጀል
የፈጸመ ፣ ይሆናል ባዮችን እሹሩሩ ለማለት እንዲያስችላቸው እሮይታ
ለማግኘት የንጉሡ አገዛዝ የሸረበው አሻጥር ቢሆንም ንጉሳዊ አገዛዙ
በቃላት ደረጃ አርነት ለመስጠት ቃል ገብቷል ። ይሁን እንጂ አንዳችም
ጐልቶ የሚታይ ነገር አላደረገም ። ለብዙ የፖለቲካ እስረኞች ምህረት ይደ
ረጋል ተብሎ ሲጠበቅ እጅግ ጥቂት ለሆኑ የፖለቲካ እስረኞች ብቻ በጥ
ቅምት 21 ቀን ምህረት ተደረገ ። ከዚሁ ጋር በማያያዝ ሕዝቡን በመከፋ



ፈል መንግሥቱ በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ ሰዎችን የገደሉ ደም የተጠሙ
እያሌ የአይሁድ የገዳይ ቡድኖችን ከማሰማራቱም በላይ አብዮቱን ለመቀ
ልበስ እንዲያስችለው የሩስያ ሕዝብ ሊግና የቅዱስ ሚካኤል ሊግ የተሰኙ
ትን በፖሊሶች ቁጥጥር ሥር የሆነ የቀማኞች ድርጅት አደራጀ ። የእነዚህ
ድርጅቶች ቁልፍ ስፍራዎች የተያዙት፣በመሬት ከበርቴዎች በነጋዴዎችና
ዱርዬ መሰል መካከለኛ ወንጀለኛ ክፍሎች ነበር ። ሕዝቡ እነዚህን ደም
የጠማቸው የግድያ ድርጅቶች « ጽልመተ መቶዎች » በሚል ስም ይጠ
ራቸዋል ። ጽልመተ መቶዎቹ በፖሊሶች እየተደገፉ በግልጽ ፖለቲካዊ
ንቃት ያላቸውን ሰራተኞች ፣ አብዮታዊ ምሁራንንና ተማሪዎችንምችን
እያሰቃዩ ኢሰብአዊ በሆነ መንገድ ገድሏቸዋል ። የመሰብሰቢያ ሥፍራ
በእሳት አጋይተዋል ። በተሰበሰቡ ሰራተኞች ላይ የጥይት ንዳድ አውርደ
ውባቸዋል ። እንግዲህ ብዙ የተወራለት የንጉሡ መግለጫ ውጤት
እስከዚሁ ድረስ ብቻ ነበር ።

በዚያን ቀውጢ ወቅት በየአካባቢው የሚዘመረው
« ንጉሥ ተብረክርኮ መግለጫ አወጣ
ለሞቱት አርነት ለቆሙት እስራት » የተሰኘው ታዋቂ ዜማ
ነበር ።

ቦልሼቪኮች የጥቅምት አስራ ሰባቱ መግለጫ ወጥመድ እንደነበረ
ለሰፊው ሕዝብ አብራርተዋል ። መግለጫው በይፋ ከታወጀ በኋላ የንጉ
ሣዊው አገዛዝ የጸብ አጫሪነት ጸባይ እንዳለው በሚገባ አስተዋሉ ። ቦል
ሼቪኮች እንዲታጠቁና ለትጥቃዊ ትግሉ እንዲሰናዱ ለሠራተኞች ጥሪ
አደረጉ ።

ሠራተኞቹ ከመቼውም ጊዜ ይልቅ የትጥቅ ቡድኖችን ለማደራጀት
ያላቸውን ጉልበት ሁሉ ተጠቀሙ ። የመጀመሪያው የጥቅምት 17 ድል
የተገኘው በአጠቃላይ ፖለቲካዊ የሥራ ማቆም አድማው ከፍተኛ ጥረት
በመሆኑ ገና ወደፊት ንጉሣዊ አገዛዙን ለመገርሰስ የሚጠብቀው ትግል
እጅግ ከፍተኛ ከበፊቱ የበለጠ መስዋእትነትን እንደሚሻ ተገነዘቡ ።

ሌኒን የጥቅምት 17ቱን መግለጫ የሀይሎች ጊዜያዊ ምጥጥናሽ
ነጸብራቅ በማድረግ ይመለከተዋል ። ወዝአደሩና ገበሬው ከንጉሡ የመግ
ለጫ ደወል ቢሰሙም ዘውዳዊውን አገዛዝ ገርስሶ ለመጣል አሁንም ቢሆን
ገና አቅም አላገኙም ። እንደዚሁም ዘውዳዊው አገዛዝ ከዚህ ቀደም በሚ
ገዙበት መንገድ አሁንም መግዛት ባለመቻሉ « የሲቪል ነጻነቶች » እን
ዲሁም « የሕግ መወሰኛ » ዱማ እንደሚፈቅድ የወረቀት ቃል ኪዳን እን
ዲያደርግ ተገደደ ።

በነዚያ የጥቅምቱ ፖለቲካዊ አድማ ሞገዳዊ ወቅቶች ዘውዳዊውን
አገዛዝ ለመገርሰስ በሚደረገው የትግል ንዳድ ውስጥ ሠራተኛው ሕዝብ
አብዮታዊ የፈጠራ ችሎታውን በመጠቀም አዲስና ጠንካራ መሳሪያ
ገነባ —የሠራተኞች ሶቭየቶች ተወካዮች ።

የሠራተኞች ሶቭየቶች ተወካዮች ከመላው ወፍጮዎችና ፋብሪካ
ዎች ተወካዮች የሚሰባሰቡ ሲሆኑ ዓለም ከዚህ ቀደም አይቶት ያላወቀው
አንድ ዓይነት የሰፊው የሠራተኛ መደብ ፖለቲካዊ ድርጅትን መስርተ
ዋል ። በ1905 ዓ.ም. በመጀመሪያ ያበቡት ሶቭየቶች በ1917 ዓ.ም. ወዝአደ
ሮች በቦልሼቪክ ፓርቲ እየተመሩ የመሠረቱት የሶቭየት ሥልጣን አስ
ኳል ነበሩ ። ሶቭየቶች የሕዝቡ የፈጠራ ችሎታ አዲስ አብዮታዊ መልክ
ሲሆኑ ፤ የዘውዱን አገዛዝ ትእዛዝና ሕጎች በመጣስ በሕዝቡ አብዮታዊ
ክፍሎች በተለየ መንገድ የተገነቡ ነበሩ ። እነዚህ የዘውዱን አገዛዝ
ለመታገል ቆርጠው የተነሱ የሕዝቡ ነጻ እንቅስቃሴ መግለጫ ናቸው ።

ቦልሼቪኮች ሶቭየቶችን የአብዮታዊ ሥልጣን ጽንስ አድርገው ይመ
ለከቷቸዋል ። የሶቭየቶች ጥንካሬና አስፈላጊነት በአመጸው ጥንካሬና
ድል አድራጊነት ላይ ብቻ መወሰኑን ያወሳሉ ።

ሜንሼቪኮች ግን ሶቭየቶችን የአብዮታዊው ሥልጣን ጽንሳዊ አካል
ወይም የአመጸው አንድ አካል በማድረግ አይቀበሏቸውም ። ሶቪየቶችን
በከተሞች የራስ አስተዳደር አካሎች ውስጥ ዲሞክራሲያዊ እንዲሆኑ የተ
በከተሞች የራስ አስተዳደር አድርገው ይመለከቷቸዋል ።
ደረጉ የአካባቢ የራስ አስተዳደር አድርገው ይመለከቷቸዋል ።

በቅዱስ ፒተርስበርግ ውስጥ ጥቅምት 13 ቀን 1905 ዓ. ም.
በቅዱስ ፒተርስበርግ ውስጥ ፋብሪካዎች የሠራተኞች ሶቪየቶች ተወካ
በመላው ወፍጮዎችና ፋብሪካዎች የሠራተኞች ሶቪየቶች ስብሰባ በዚያው እለት
ዮች ምርጫ ተካሄደ ። የመጀመሪያው የሶቪየቶች ስብሰባ በዚያው እለት
ምሽት ተካሄደ ። የቅዱስ ፒተርስበርግ የሠራተኞች ሶቪየቶች ተወካዮች
ምርጫ ፈለግ በመከተል ወዲያውኑም በሞስኮ ተካሄደ ።

የቅዱስ ፒተርስበርግ የሠራተኞች ሶቪየት ተወካዮች ከመላው ሩስያ
እጅግ ጠቃሚ ኢንዱስትሪያዊና የአብዮቱ ማእከል በመሆኑ የሁሉም ሶቪ
የቶች ማእከል ሆኗል ። ይህች የንጉሣዊው ግዛት ዋና ከተማ የሆነችው
ቅዱስ ፒተርስበርግ በ1905 ዓ. ም. የአብዮቱን ወሳኝ ሚና ተጫው
ታለች ። ያ ቢሆንም ቅሉ የሜንሼቪኮችን መጥፎ አመራር በመቃወም
ረገድ ማድረግ የሚገባቸውን ተግባር አላደረጉም ። እንደምናውቀው ሌኒን
እንደሆን ገና ወደ ቅዱስ ፒተርስበርግ አልተመለሰም ፤ አሁንም እዚያው
ባህር ማዶ ነበር ያለው ። ታዲያ የሌኒን በቅዱስ ፒተርስበርግ ያለመኖሩን
አጋጣሚ በመጠቀም ሜንሼቪኮች በቅዱስ ፒተርስበርግ ሶቪየት ውስጥ
ለመግባትና አመራሩን ለመጨበጥ መንገዳቸውን አመቻቹ ። እንደዚህ
ባለ አመቺ ሁኔታ ውስጥ ሜንሼቪኮች ክሁሩስታሌቪ ፣ ትሮትስኪ ፣ ፓር
ቮስና ፣ ሌሎችም የቅዱስ ፒተርስበርግ ሶቪየት የአመጸውን መመሪያ በመ
ቃወም ቢያነሳሱ ፍጹም ሊደንቀን አይችልም ፤ ወታደሮችን ከሶቪየት
ጋር የቀረበ ግንኙነት በመፍጠር የጋራ ከሆነው ትግል ጋር ማገናኘት
ሲገባቸው ወታደሮች ከቅዱስ ፒተርስበርግ እንዲለቁ ጠይቀዋል ።



ሶቪየቱ ሰራተኞችን ማሥታጠቅና ለአመጽ ማዘጋጀት ሲገባው ጭራሹን
ለአመጸው የሚደረገውን ዝግጅት በመቃወም ጊዜው እንደዚያ በሚነጉ
ድበት ወቅት እነርሱ ባሉበት ይረግጡ ነበር ።

ከሁሉም የተለየው የሞስኮ የሰራተኞች ሶቪየት ተወካዮች በአብዮቱ
ውስጥ የተጫወቱት ሚና ሲሆን ፤ ከመጀመሪያው ጀምሮ የሞስኮ ሶቪየት
ትክክለኛውን አብዮታዊ መመሪያ ያራምዱ ነበር ። የሞስኮ ሶቪየት አመ
ራር በቦልሼቪኮች እጅ ነበር ። ምስጋና ይግባቸውና ከሠራተኞች ሶቪየቶች
ተወካዮች ጐን ለጐን በሞስኮ ውስጥ የወታደሮች ሶቪየቶች ተወካዮች
ተመሠረቱ ። የሞስኮ ሶቪየት ለትጥቅ ትግሉ አካል ለመሆን በቃ ።

ከጥቅምት ወር ጀምሮ እስከ ታሀሣሥ 1905 ዓ.ም. ድረስ ያለው ወቅት
በትላልቅ ከተሞችና በመላው ሀገሪቷ ማለት ይቻላል የሠራተኞች ሶቪየ
ቶች ተወካዮች ተመሠረቱ ። የወታደሮችንና የመርከበኞችን ተወካዮች
ለማደርጀትና ከሠራተኞች ሶቪየቶች ተወካዮች ጋር ለማስተባበር ከፍ
ተኛ ጥረት ተደርጓል ። በአንዳንድ አካባቢዎችም የሠራተኞችና የገበሬ
ዎች ሶቪየቶች ተወካዮች ተመስርተው ነበር ።

የሶቪየቶች ተቀባይነት እጅግ ከፍተኛ ነበር ። ምንም እንኳ በየአካ
ባቢው ግብታዊ በሆነ መንገድ ቢመሰረቱም ፣ የተወሰነ መዋቅር ባይኖ
ራቸው እንዲሁም በሚገባ ባይደራጁ ድርጊቶቻቸው ሁሉ እንደ አንድ
መንግስታዊ ሀይል ነበር ። አንዳችም ሕጋዊ ሥልጣን ሳይኖራቸው የጽሑፍ
ነጻነትና በቀን 8 የሥራ ሰዓት እንዲከበር አሳወቁ ። ሕዝቡ ለንጉሳዊው
አገዛዝ አንዳችም ግብር እንዳይከፍል ጥሪ አደረጉ ። በአንዳንድ ሁኔታ
ውስጥም ለአንድ ነገር እንዲውል የተሰበሰበውን የመንግስት ገንዘብ በመ
ውረስ ለአብዮት ለሚያስፈልጉ ነገሮች ተጠቀሙባቸው ።

5/ <u>የታህሳሱ ትጥቃዊ አመጽ ፣ የአመጸው ሽንፈት ፣</u>
<u>የአብዮቱ ማፈግፈግ ፣ የመጀመሪያው መንግስታዊ ዱማ ፣</u>
<u>አራተኛው (አንድነት) የፓርቲ ኲንግረስ ፡—</u>

በጥቅምትና በሕዳር ወር 1905 ዓ.ም. ውስጥ የሰፊው ሕዝብ አብዮ
ታዊ ትግል በከፍተኛ ጥንካሬ እያደገ ሄደ ። የሠራተኞች የሥራ ማቆም
አድማ በሰፊው ቀጠለ ።

በ1905 ዓ.ም. የበልግ ወራት ገበሬው በመሬት ከበርቴዎች ላይ ያደ
ረገው ትግል ታላቅ ግምት የሚሰጠው ነበር ። የገበሬዎች ንቅናቄ ከአንድ
ሶስተኛ በላይ የሀገሪቷን ኡዬዝዶች ይዟል ። በሳራቶቭ ፤ በታምቦቭ ፣
በቼርኒጐቭ ፣ በቲፍሊስ ፣ በኩታይስና በሌሎችም አያሌ ጠቅላይ ግዛቶች
የገበሬ አመጾች ከመቼውም ጊዜ ይልቅ ጐልተው ይታዩባቸው ነበር ።
ይሁን እንጂ እነዚህ የገበሬ ንቅናቄዎች የድርጅትና የአመራር እጥረት
ነበረባቸው ።

በብዙ ከተሞች ማለትም በቲፍሊስ ፣ በቭላዲቮስቶክ ፣ በታሽኬንት ፣
በሰማርካንድ ፣ በኩርስክ ፣ በሱኩሁም ፣ በዋርሶው ፣ በኪየቭና በሪጋ የወ
ታደሮች እንቅስቃሴ ከመቼውም ጊዜ ይበልጥ ጨመረ ። በክሮንስታድና
በጥቁር ባሕር በሴቫስቶፖል መርከቦች መሀል አመጽ ፈነዳ (ህዳር 1905)
አመጹም የተቀነባበረ ባለመሆኑ የዛሩ መንግስት በቁጥጥሩ ሥር ሊያደር
ገው ቻለ ።

በጦር ሰራዊቱና በባህር ሀይል ክፍሎች ውስጥ በመኮንኖች አረመ
ኔያዊ ባህርይ ፣ በመጥፎ ምግቦችና ('የምግብ አመጽ') በመሰሉ ምክንያ
ቶች እየተደጋገሙ አመጾች ተደረጉ ። በአመጻው የተሳተፉ በርከት ያሉ
ት መርከበኞችና ወታደሮች የዛሩን አገዛዝ ለማውደም ለምን እንደሚያስ
ፈልግ ፣ ጠንካራ የትጥቅ ትግል በዛሩ ላይ ማካሄድ ለምን እንደሚያስፈልግ
ገና ጠንቅቀው አልተገነዘቡም ። እነርሱ አሁንም በጣም ሰላማውያንና
በራሳቸው የሚረኩ ስለነበሩ ፤ በአመጻው ምክንያት የታሰሩትን መኮን
ኖች ብዙ ጊዜ እየፈቱ ለቀቋቸው ። በአንዳንድ ጥቅሞች እንዲደለሉ ሆነና
በአለቆቻቸው በቀላሉ ተሸነገሉ ።

አብዮታዊው ንቅናቄ ከመቼውም ጊዜ ይበልጥ በትጥቅ ትግሉ አድ
ማስ ውስጥ መግባቱን በሚገባ አመለከተ ። ቦልሼቪኮችም ሰፊው ሕዝብ
በዛሩ አገዛዝ ፣ በመሬት ከበርቴዎች ላይ መሣሪያ እንዲያነሳ ጥሪ በማድ
ረግና ይህ ዓይነት ትግል ፍጹም ሊዘለል የማይገባው አስፈላጊ መሆኑን
በመተንተን አብራሩላቸው ። ቦልሼቪኮች በማይበገር ሁኔታ ትጥቃዊ
አመጽ አዘጋጁ ። በመርከበኞችና በወታደሮች መሀከል ከፍተኛ አብ
ዮታዊ ሥራዎች ተከናወኑ ። የፓርቲው ወታደራዊ ድርጅቶችም በነዚሁ
ክፍሎች ውስጥ ተመሠረቱ ። በአያሌ ከተሞች የሰራተኛ ተዋጊ ቡድኖች
ተቋቋሙና አባሎቻቸው ስለመሳሪያ አጠቃቀም አስፈላጊውን ትምህርት
እንዲማሩ ተደረገ ። ከውጪ መሣሪያ የሚገዛና ወደ ሩስያ የሚያስገባ
አካል ተደራጀ ፣ የፓርቲው ከፍተኛ ሰዎች ማጓጓዣዎችን ማዘጋጀት
ጀመሩ ።

በህዳር ወር 1905 ዓ.ም. ሌኒን ወደ ሩስያ ተመለሰ ። ከዛሩ አፋኞችና
ሰላዮች እራሱን በመሸሸግ የትጥቅ ትግሉን በማዘጋጀት ተግባር ውስጥ
በቀጥታ ተሳተፈ ። በቦልሼቪክ አዲሱ ጋዜጣ ኖቫያ—ዚዝን (አዲስ ሕይ
ወት) ላይ የሚያስፍራቸው ጽሁፎች የፓርቲውን የእለት በለት ሥራ በመ
ምራት አገለገሉ ።

በዚህ ወቅት ጓድ ስታሊን በትራንስካውካስያን ውስጥ ታላቅ አብ
ዮታዊ ተግባር በማካሄድ ላይ ነበር ። ሜንሼቪኮች የአብዮቱ ጠላቶች
መሆናቸውን በማጋለጥ ቆራጥ እርምጃ ወሰደ ። ልክ የዛሩ መግለጫ በወጣ
በት እለት በቲፍሊስ በተደረገው የሰራተኞች ስብሰባ ላይ ጓድ እስታሊን ፡-

«በእርግጥ ማሸነፍ ከፈለግን ምን ያስፈልገናል ? ሶስት ነገሮች ያስ
ፈልጉናል ፣ በመጀመሪያ ትጥቅ ፣ አሁንም ትጥቅ እንደገናም ትጥቅ !»



ብሎ በመናገር ፈላጭ ቆራጩን አገዛዝ ለመገርሰስ ለሚያደረገው ቆራጥ
ትግል ሠራተኞችን አዘጋጀ ።

በታህሳስ ወር 1905 ዓ.ም. በታመርፎርስ ፣ ፊንላንድ የቦልሼቪኮች
ስብሰባ ተደረገ ። ምንም እንኳ ቦልሼቪኮችና ሜንሼቪኮች በቅርጽ ደረጃ
የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ አካል ቢሆኑም አሁንም እያንዳንዳቸው የራ
ሳቸው መሪ ማእከል ያላቸው ሁለት የተለያዩ ፓርቲዎች ነበሩ ። በዚህ
ስብሰባ ሌኒንና ስታሊን ለመጀመሪያ ጊዜ ተገናኙ ። እስከዚያን ጊዜ
ድረስ በደብዳቤ ፣ በመላላክና በሌሎች ጓዶች አማካይነት ብቻ ነበር የሚ
ገናኙት ።

በታመርፎርስ ስብሰባ ላይ ከተላለፉት ውሳኔዎች ውስጥ ሁለቱ የሚ
ከተሉት ነበሩ ። አንደኛው በሁለት የተከፈለውን የፓርቲ አንድነት
ለመመለስ ሲሆን ሌላኛው ደግሞ ወይቲ ዱማ በመባል የሚታወቀው
የመጀመሪያውን ዱማ አለመሳተፍ ነበር ።

በዚያን ወቅት የትጥቅ አመጹ በሞስኮ ተጀምሮ ነበር ። በግለሰብ
ደረጃ ተወካዮች በአመጻው ውስጥ መሳተፍ እንዲችሉ ሌኒን ስብሰባው
በአስቸኳይ ተግባሩን ፈጽሞ እንዲበተን አሳሰበ ።

ነገር ግን የዛሩም አገዛዝ ቢሆን በነገሩ አላንቀላፋም ። ለወሳኙ ትግል
ይበልጡን ተዘጋጅቶ ነበር ። ከጃፓን ጋር የነበረውን ቅራኔ በእርቅ በመ
ፍታትና ችግሮቹን በማቃለል በወዝ አደሮችና በገበሬዎች ላይ የማጥቃት
እርምጃ ለመውሰድ አሰበ ። የገበሬዎች አመጽ በተስፋፋበት አያሌ ጠቅ
ላይ ግዛቶች የአስቸኳይ ጊዜ ሕግ አወጀ ። «አትሰራቸው» እና «ጥይትም
አታባክንባቸው» የሚል በጣም አረመኔያዊ ትእዛዝ ሰጠ ። እንዲሁም
የአብዮታዊውን ንቅናቄ መሪዎች እንዲታሰሩና የተቋቋሙት የሠራተኞች
ሶቭየቶች ተወካዮች እንዲፈርሱ ትእዛዝ ሰጠ ።

ለዚህ ምላሽ አመጻውን የመሩትና ከሰፊው ሕዝብ ጋር የጠበቀ ግን
ኙነት ያላቸው የሞስኮ ቦልሼቪኮችና የሞስኮ የሠራተኞች ሶቭየቶች ተወ
ካዮች አምጥተው በአስቸኳይ ለመዘጋጀት ወሰኑ ። በታህሳስ 5 ቀን የሞ
ስኮ ቦልሼቪክ ኮሚቴ ሶቭየቶችን ለመጥራትና አጠቃላይ ፖለቲካዊ የሥራ
ማቆም አድማ በማወጅ በአብዮቱ ትግል ውስጥ ትጥቃዊ አመጽ ለመጀ
መር ውሳኔ አደረገ ። ይህ ውሳኔ በሰራተኛው ስብሰባዎች በሚገባ ተደገፈ ።
ለሰራተኛው መደብ ጥሪም የሞስኮ ሶቭየት ምላሹን ሰጠ ። አጠቃላይ
ፖለቲካዊ አድማ ለመጀመርም በአንድ ድምጽ ተስማማ ።

የሞስኮ ወዝ አደሮች አመጻውን በጀመሩበት ወቅት ወደ አንድ ሺህ
የሚገመቱ ተዋጊዎች ከነዚህም ውስጥ ከግማሽ በላይ ቦልሼቪኮች የሚ
ገኙበት ተዋጊ ድርጅት ነበሩአቸው ። በተጨማሪም በአያሌ የሞስኮ ፋብ

ረካዎች ውስጥ በርካታ የትጥቅ ቡድኖች ይገኙ ነበር ። አጠቃላይ አመጿው ወደ ሁለት ሺህ የሚጠጉ ተዋጊዎች ነበሩት ። ሰራተኞች ወታደራዊ ካምፖችን ገለልተኛ ለማድረግና ከፊሉን ደግሞ ከጉናቸው እንደሚሰለፉ በተስፋ ይጠብቁ ነበር ።

በታህሳስ ሰባት ቀን በሞስኮ ፖለቲካዊ የሥራ ማቆም አድማ ተጀመረ ። ይሁን እንጂ አመጿውን ሀገር አቀፍ ለማድረግ ተደርጐ የነበረው ጥረት ከሸፈ ። የቅዱስ ፔተርስበርግ የሠራተኞች ድጋፍ በጣም ዝቅተኛ ነበርና የአመጿውን የማሸነፍ እድል ዝቅ አደረገው ። የኒኮ ላይቪስካያ (አሁን የጥቅምቱ) የቡባቡር ሀዲድ በዛሩ አገዛዝ እጅ ውስጥ እንደሆነ ቀረ ። መንግስቱ ከቅዱስ ፔተርስበርግ ዘቦች ወደ ሞስኮ በመዝጋት ትራፊኩ ለጊዜውም ቢሆን አላገደውም ።

በራሷ በሞስኮ ውስጥ ያሉ ወታደራዊ ሰፈሮች በማወላወል ላይ ነበሩ ። ሠራተኞች ሰፈር ድጋፍ እንደሚያገኙ ተስፋ በማድረግ አመጿውን ጀመሩት ። ነገር ግን አብዮታውያን እጅግ በጣም ስለዘገዩ መንግስቱ በጦር ሰፈር ውስጥ ምንም ጊዜ ሳይሰጥ በሚገባ ተጠቀመበት ።

በታህሳስ 9 ቀን የመጀመሪያው መሰናክሎች በሞስኮ ታዩ ። ወዲያው የከተማው አውራ ጐዳናዎች በአያሌ መሰናክሎች ተዘጉ ። የዛሩ አገዛዝ መድፎችን በተግባር አዋለ ። በአመጿ ላይ ከተሰለፉ አብዮታውያን ቁጥር እጅግ ብዙ ጊዜ የሚበልጥ ሀይል አሰማራ ። በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ የታጠቁ ሠራተኞች ለዘጠኝ ቀናት በቆራጥነትና በጀግንነት ተዋጉ ። የዛሩ አገዛዝ ይህንን ታላቅ አመጽ በቅዱስ ፒተርስበርግ ፣ በቲቨር እንዲሁም በምእራባዊ ግዛቶች ያሉትን የጦርሀይሎች አግበስብሶ በማምጣት ብቻ ነበር ሊገታው የቻለው ። ገና በአመጿው ዋዜማ የአመጿው መሪዎች በከፊል ሲታሰሩ ፣ ከፊሎቹም ከአመጿው ተገልለው ነበር ። የሞስኮ የቦልሼቪክ ኮሚቴ አባሎች ታሠሩ ። የትጥቅ ትግሉ የተነጣጠሉ አውራጃዎች ያልተቀናጀ የአመጽ መልክ ያዘ ። ማእከላዊ አመራር ባለመኖሩና ለመላው ከተማ የጋራ የሆነ የአሠራር እቅድ በማጣቱ አውራጃዎች ይበልጥ በመከላከሉ ተግባር ላይ ራሳቸውን ወሰኑ ። ለሞስኮው አመጽ መዳከም ዋነኛው ምንጭ የሆነው ይህ ሲሆን እንዲሁም ሌኒን በኋላ እንደጠቀሰው ለአመጿው ሽንፈት አንደኛው ምክንያት ነበር ።

በሞስኮ ውስጥ የአመጿው ከፍተኛ ጥንካሬ ያለበትና የአመጿውም አማካኝ ሥፍራ በሆነችው በክራስናያ ፕሬስናያ አውራጃ የተደረገው ትግል በተለይ እጅግ አስቸጋሪና መራራ ነበር ። በቦልሼቪክ የሚመሩ የትጥቅ ቡድኖች የተከማቻቸበት ይሁን እንጂ ክራስናያ ፕሬስናያ በእሳትና በአረመኔያዊ ሳንጃ ተጨፈጨፈች ። ከእነዚህ አስከፊ የዛር መሣሪያዎች በሚተፉት የእሳት ፍላጻዎች ነደደች ፣ በአያሌ ወዝአደሮች ደም ታጠበች ፣ የሞሥኮው አመጽ ለጊዜውም ቢሆን ተዳፈነ ።



አመጿው በሞስኮ ውስጥ ብቻ ተወስኖ አልቀረም ። አብዮታዊው አመጽ በአያሌ ከተሞችና አውራጃዎች ተቀጣጠለ ። በራስኖያርስክ ፣ በሞቶቪሊካ (ፔርም) ኖቮሮሲስክ ፣ በሰርሞቮ ሴቨስቶፓልና በሮቨስታዶት ትጥቃዊ አመጿው ተጧጡፎ ነበር ።

የሩስያ ጭቁን ብሔረሰቦችም ቢሆኑ አመጿውን ከውጪ ቆመው አልተመለከቱትም ፤ ይልቁንም ጠመንጃ በማንሣት በትጥቃዊው አመጽ ውስጥ ለመሳተፍ ተነሳሱ ። መላው ጆርጂያን ማለት ይቻላል ፣ ለአመጿው ትጥቅ አነሱ ። በጉርሎቭካ ፣ በአለክሳንድሮቭና በሉጋንስክ (አሁን ቮሮቪሎቭግራድ ተብሎ የሚጠራው ነው) በደንዝ ረግረጋማ አካባቢዎች በሚገኙት የኡክሬን ከተሞች ታላቅ አመጽ ተደረገ ። በላቲቪያ እጅግ ከባድ ትግል ተካሄደ ። የፊንላንድ ሠራተኞች የራሳቸውን ቀይ ታፊሮች በማዘጋጀት ለአመጽ ተነሳሱ ።

ይሁን እንጂ እነዚህ ሁሉ አመጿዎች እንደሞስኮው አመጽ ሁሉ በፈላጭ ቆራጩ አገዛዝ ኢ-ሰብአዊ በሆነ ጭካኔ ተደመሰሱ ።

የታህሣሱ ትጥቃዊ አመጽ መነሳት በቦልሼቪኮችና በሜንሼቪኮች የተለየ አዝማሚያ ነበረው ።

ከአመጿው በኋላ ፕሌክሀኖቭ « ትጥቅ ማንሳት አልነበረባቸውም » በማለት የሜንሼቪኮችን ትክክለኛነት መሰከረ ። ሜንሼቪኮች ቀደም ብለው ትጥቃዊ አመጽ ማድረግ አያስፈልግም ደግሞም አደገኛ ነው ፤ ድል ሊገኝ የሚችለው በትጥቃዊ አመጽ አይደለም ነገር ግን በሰላማዊ የትግል መንገድ ነው ፤ በማለት ያላቸውን አቋም ገለፁ ።

ቦልሼቪኮች ይህንን አቋም እንደከህደት ይመለከቱታል ። የሞስኮው የትጥቅ አመጽ ልምድ የሚያረጋግጥልን የሠራተኛው መደብ በተሳካ ሁኔታ የትጥቅ ትግል ማካሄድ እንደሚችል ነበር ። ፕሌክሀኖቭ «ትጥቅ ማንሳት አልነበረባቸውም» ለሚለው አባባሉ ሌኒን መልስ ሲሰጥ

«በተቃራኒው ፤ ይበልጥ በቆራጥነት ባለን ሀይል ሁሉ ትጥቅ አንስተን ወደፊት መግፋት ይገባናል ፤ ራሳችንን በሠላማዊ የሥራ ማቆም አድማ መካከል እንደማይቻለን ፤ ቆራጥና የማይበገር የትጥቅ ትግል የማንዘለው (የግድ አስፈላጊ) ተግባር መሆኑን ለሠፊው ሕዝብ መግለፅ ይኖርብናል ብሏል። »

(ሌኒን ምርጥ ሥራዎች ፣ እንግሊዝኛ እትም ፣ ሞስኮ ፣ 1947 ዓ. ም. ቅጽ 1 ፣ ገጽ 446)

በታህሣሥ ወር 1905 ዓ. ም. የተካሄደው አመጽ የአብዮቱ ከፍተኛ ደረጃ ነበር ። የዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ አመጹን በሙሉ እንዳይነሳ ያቆመው ባይሆንም አዳፈነው ፣ ከዚያ በኋላ አብዮቱ በተራው ማሽቆልቆል ጀመረ ፣ ያ የገነፈለው አብዮት ቀስ በቀስ እየበረደ ፣ ያ የነበረው ውጥረት እየረገበና እየላላ ሄደ ።

የዛሩ አገዛዝ ይህንን የአብዮት ሽንፈት ለመጠቀም ዳግም እንዳያንሰራራ ለአሁንና ለሁሉም የማያዳግም ምት ለመምታት ተፋጠነ ። የዛሩ እውቅ ነፍሰገዳዮችም በደም የተነከረ አረመኔያዊ ተግባራቸውን ማካሄድ ጀመሩ ፣ በፖላንድ በላቲቪያ በኢስቶኒያ ፣ በትራንስካውካሲያንና በሳይቤሪያ አማጮችን የሚቀጣ ወታደራዊ ቡድን ተላከ ።

ነገር ግንአብዮቱ ተዳፈነ እንጂ አልተደመሰሰም ። ሠራተኞችና አብዮታዊ ገበሬዎች ትግሉን ለመቀጠል በዝግታ አፈገፈጉ ። የሠራተኛው አዲስ ክፍሎች በትግሉ ውስጥ ገቡ ። በ1906 ዓ. ም. ከሚሊዮን በላይ የሚቆጠሩ ሠራተኞች በሥራ ማቆም አድማው ተሳተፉ ። በ1907 ዓ. ም. ደግሞ 74,0000 ያህሉ ተካፈሉ ። በመጀመሪያው 1906 ዓ. ም. የመጀመሪያው አጋማሽ ላይ የገበሬዎች እንቅስቃሴ የዛራዊት ሩስያን ከፊል ኡዬዝዶች የአቀፈና በአመቱ ሁለተኛው አጋማሽ ደግሞ አንድ አምስተኛውን ያቀፈ ነበር ። ይህ ሁኔታ ያለእረፍት በባህር ሀይሉና በጦር ሠራዊቱ ውስጥ ቀጠለ ።

የዛሩም አገዛዝ ቢሆን አብዮቱን ለመውጋት እስከፊ እርምጃዎች በማካሄድ ላይ ብቻ ራሱን መወሰን አልፈለገም ። በነዚያ አስከፊ እርምጃዎቹ የመጀመሪያውን ድል ካገኘ በኋላ አዲስ ዱማ « የሕግ መወሰኛ » ዱማ በመሰብሰብ አብዮቱን በአዲስ የማክተሚያ ምት ለመምታት ወሰነ ። በዚህ መንገድ ገበሬዎች ከአብዮቱ ጐን እንዳይሰለፉ ለመከላከልና ለአብዮቱ መደምደሚያ ለመስጠት ይቻላል ብሎ አመነበት ። በታኅሣሥ ወር 1905 ዓ. ም. የዛሩ አገዛዝ ቦልሼቪኮች በስብሰባው ውስጥ ባለመሳተፋቸው ምክንያት የቀረውን « ሆን ተብሎ የተዘጋጀው » ከቡልጂን ዱማ የተለየ አዲስ « የሕግ መወሰኛ » ዱማ ለመሰብሰብ የሚያስችል ሕግ አወጀ ። በርግጥ የዛሩ የምርጫ ህጐች ፀረ-ዲሞክራሲ ነበሩ ። ምርጫው ሁለንታዊ አልነበረም ። ከሕዝቡ ቁጥር ውስጥ ከግማሽ በላይ የሚሆኑት — ለምሳሌ ሴቶችና ከሁለት ሚሊዮን በላይ የሆኑ ሠራተኞች የመምረጥ መብታቸውን በአንድነት ተነፈጉ ። ምርጫዎቹ በእኩልነት ላይ የተመሠረቱ አልነበሩም ። መላው መራጮች እነዚያ እንደሚጠሩት በአራት ኵሪያስ ተከፍለዋል ። የገጠሩ (የመሬት ከበርቴዎች) የከተማው (ቡርዧዎች) ገበሬውና የወዝአደሩ ኵሪያስ ናቸው ። ምርጫው ቀጥተኛ ሳይሆን ፤ ነገር ግን በእያሌ ደረጃዎች የሚካሄድ ነበር ። በሚስጥር ድምጽ ለመስጠት የሚያስችሉ ሁኔታዎች አልነበሩም ። በዱማ ውስጥ በርካታውን ቁጥር ጭብጥ የማይሞሉ የመሬት ከበርቴዎችና ካፒታሊስቶች ከሚሊዮን በላይ በሚሆኑ ወዝአደሮችና ገበሬዎች ላይ የበላይነት እንደሚኖራቸው የምርጫው ህግ ያረጋግጣል ።

የዛሩ አገዛዝ ዱማውን የሚጠቀምበት ሰፊው ሕዝብ በአብዮቱ ላይ ያለውን ትኩረት ለመለወጥና ከአብዮቱ ለማራቅ በማለም ነበር ። በነዚያም ወቅቶች አብዛኛው ገበሬ በዱማው በኩል መሬት እናገኛለን በሚል



እምነት ውስጥ ተዘፈቀ ። ሕገ-መንግሥታዊ ዲሞክራቶች ፣ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች ሕዝቡ የሚፈልገው አይነት ሥርዓት ያለአንዳች አመጽ ምንም ዓይነት አብዮት ሳይደረግ ይኸው ተገኘ በማለት ሕዝቡን ሸንገሉ ። ይህንን በሕዝቡ ላይ የተደረገ አረመኔያዊ ተግባር ለመታገል ሲሉ ነበር ቦልሼቪኮች የመጀመሪያውን መንግሥታዊ ዱማ ያልተሳተፉትና ይህን የመሰሉ ታክቲኮች የቀየሱት ። ይህም በታሜርፎርሱ ጉባኤ ተወስኖ የፀደቀ ነበር ።

በሚያደርጉት ጸረ-ዛር ትግላቸው ሠራተኞቹ የፓርቲውን የተባበረ ሀይል ይሻሉ ። የወዝአደሩን ፓርቲ መዋሀድ አጥብቀው ይፈልጋሉ። በታሜርፎርሱ ጉባኤ ውሳኔ እርግጠኛውን ነገር በመያዝ ቦልሼቪኮች ይህን የሠራተኞችን ጥያቄ ደገፉት ። ፓርቲውን የሚያዋሀድ ስብሰባ መጠራት እንዳለበትም በማሰብ ቦልሼቪኮች ለሜንሸቪኮች ጥሪ አደረጉ ። ሠራተኞች በአደረጉት ታላቅ ጥረት ተገፍተው ሜንሼቪኮች ለአንድነቱ ተስማሙ ።

ሌኒን ይህን አንድነት በሚገባ ደግፎታል ። ይሁን እንጂ እንደዚህ ያለው አንድነት ብቻ በአብዮቱ ላይ ያሉትን ችግሮች ከቶም ሊሸፍን አይችልም ። በቦልሼቪክና በሜንሼቪኮች መሀከል ያለው ልዩነት ይህንን ያህል የጠነከረ አይደለም በማለት ሊያስታርቁ በሞከሩ ሽማግሌዎች (በግላኖቭ ፣ ክራሲንና ሌሎችንም) ሊዘነጋ የማይገባው አደጋ በፓርቲው ላይ ደርሷል ። ሌኒን ቦልሼቪኮች የራሳቸውን መድረክ በመያዝ ነው ወደ ኮንግሬሱ መምጣት ያለባቸው ስለሆነም ሠራተኛው የቦልሼቪኮች አቋም ምን እንደሆነ በሚገባ አበጥሮ መገንዘብ ይቻለዋል ። በዚህም አንድነቱ በምን ላይ እንዲሚመሰረት ይረዳዋል ። በማለት እያስገነዘበ አስታራቂ ሽማግሌዎችን በሚገባ ታገለ ። ቦልሼቪኮች ይህንን የመሰለ መድረክ በመክፈት ለፓርቲ አባሎች እንዲወያዩበት አቀረቡ ።

የአንድነት ኮንግሬስ ተብሎ የሚታወቀው አራተኛው የሩ. ሶ. ዲ. ሠ. ፓ. ኮንግሬስ በእስቶክሆልም (ስዊድን) ውስጥ በሚያዝያ ወር 1906 ዓ. ም. ተደረገ ። 111 ተወካዮች ድምጽ ከመስጠት መብታቸው ጋር 57 የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲን የአካባቢ ድርጅቶች በመወከል ተገኝተው ነበር ። ሶስት ከቡንድ ፣ ሶስት ከፖሊሽ ሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ እንዲሁም ሶስቱ ከሌቲሽ ሶሻል ዲሞክራቲክ ድርጅት የመጡ ነበሩ ።

በታህሳስ አመጽና ከአመጸው በኋላ በቦልሼቪክ ድርጅቶች ላይ በደረሰው መመታት ሳቢያ ሁሉም ድርጅቶች የራሳቸውን ተወካዮች ለመላክ አልቻሉም ። ከዚያም በላይ በ1905 ዓ.ም. «የእርነት ቀናት» ወቅቶች ከአብዮታዊ ማርክሲዝም ጋር አንዳችም የማያገናኛቸው የንዑስ ከበርቴ እያሌ ምሁራን በአመራራቸው ውስጥ እንዲገቡ ሜንሼቪኮች ፈቅደው ነበርና የፈለጉትን አገኙ ማለት ይቻላል ። የቲፍሊስ ሜንሼቪኮች (በጣም ጥቂት የፋብሪካ ሰራተኞች ነበሩ) ከትልቁ የሰራተኞች ድርጅት—ከቅዱስ

ፒተርስበርግ ድርጅት በበለጠ-አያሌ ተወካዮችን ወደ ኮንግረሱ ላኩ ። የዚህም ውጤት በስቶክሆልም ኮንግሬስ ሜንሼቪኮች አብዛኛውን ድምጽ እንዲይዙ ሆነ ። ይህ ምንም እንኳ እውነት ቢሆን ፣ ይህን ያህል ጐልቶ የሚታይ አልነበረም ።

የዚህ ኰንግረስ መቀላቀል አያሌ የሜንሼቪኮች የጥያቄዎች ውሳኔዎችን ባህርይ ገለጸ ።

በዚህ ኮንግረስ አንድነቱ በቅርጽ ደረጃ ብቻ ነበር ። ስለእውነቱ ከሆነ ቦልሼቪኮችና ሜንሼቪኮች የየራሳቸውን አመለካከትና የግላቸውን ነጻ ድርጅት ማራመዳቸውን አልተውም ።

በአራተኛው ኮንግረስ ላይ የተወያዩባቸው አቢይ ጥያቄዎች የገጠሩን ጥያቄ ፣ የወቅቱን ሁኔታ ፣ የወዝአደሩ መደባዊ ተግባር ፣ መንግስታዊውን ዱማ አስመልክቶ መወሰድ ስለሚገባው መመሪያና ድርጅታዊ ጥያቄዎች ነበሩ ።

ምንም እንኳ የኮንግረሱን አብዛኛውን ድምጽ የያዙት ሜንሼቪኮች ቢሆኑም ቅሉ ፣ በዚህ ኮንግረስ ላይ ሠራተኞችን ላለማቃረን ሲሉ ሌኒን የቀመረውን ስለፓርቲው ህግ በሚያወሳው የመጀመሪያ አንቀጽ የሰፈረውን የፓርቲ አባልነት ሀሳብ እንዲስማሙ ተገደዱ ።

የገጠርን ጥያቄ አስመልክቶ ሌኒን መሬት ብሔራዊ መሆን እንዳለበት አሳሰቦ ፣ ይህ መሬትን ብሔራዊ የማድረግ ተግባር የሚቻለው አብዮቱ ድል ሲያደርግ ፣ የዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ተገርስሶ ሲወድቅ ብቻ እንደሆነ አስገንዝቧል ። ከእንደዚህ አይነት ሁኔታ ውስጥ የመሬት ብሔራዊ መደረግ ለወዝአደሩ ከድሀ አርሶአደሮች ጋር ህብረት ለመፍጠርና ወደ ሶሻሊዝም ለመሸጋገር ሁኔታውን ቀላል ያደርግለታል ። መሬትን ብሔራዊ ማድረግ ማለት መላውን የመሬት ባለቤትነት ያለ አንዳችካሳ በመውረስ ለአርሶአደሮች መስጠት ማለት ነው ። የቦልሼቪኮች የገጠር መርሀ ግብር አርሶአደሮች ጸረ-ዛርና ጸረ-መሬት ከበርቴ ትግላቸውን እንዲያጧጡፉ ጥሪ ያደርጋል ።

ሜንሼቪኮች የተለየ አቋም ወሰዱ ። እነርሱ በማዘጋጃ ቤት የማድረግን መርሀ-ግብር አራመዱ ። እንደ መርሀ-ግብሩ አባባል የመሬት ባለቤትነት በመንደር ኮሚቴዎች ቁጥጥር ሥር እንዲሆን አይደረግም ወይም ለመንደር ኮሚቴዎች ጥቅም እንዲውል አይሰጥም ነገር ግን በማዘጋጃ ቤት (የራስ በራስ አገዛዝ አካባቢያዊ ድርጅት የሆነው ወይም ዜሚስቶቭ) ቁጥጥር ሥር መደረግ አለበት ። እያንዳንዱ ገበሬ ከዚህ መሬት በሚያገኘው መጠን ኪራይ መክፈል አለበት ።



በማዘጋጃ ቤት ቁጥጥር ስር ማድረጉ የሜንሼቪኮች መርሀ-ግብር አንድ ዓይነት እርቅና ድርድር ስለነበረ አብዮቱን አደጋ ላይ ለመጣል ምክንያት ይሆናል ። ገበሬዎችን ለአብዮታዊ ትግል አያንሳሳም ፤ እንዲሁም የመሬት ከበርቴዎችን በመሬት ላይ ያላቸውን የባለቤትነት መብት ጨርሶ በማስቀረት የተነደፈ አልነበረም ። ይልቁንም የሜንሼቪኮች መርሀ-ግብር አብዮቱን በግማሽ መንገድ ላይ ለማስቀረት የተነደፈ ነበር ። ሜንሼቪኮች ገበሬዎችን ለማነሳሳት አልፈለጉም ።

በኮንግረሱ ላይ የሜንሼቪኮች መርሀ-ግብር አብዛኛውን ድምጽ አገኘ ።

ሜንሼቪኮች በተለይ ጸረ-ወዝአደርነታቸውን በጊዜያዊ ሁኔታ ላይ በተላለፈው ውሳኔ ውይይት በተደረገበት ወቅት በመንግስታዊ ዱማ የነበራቸውን አድርባይነት ባህርይ አጥብቀው ካዱ ። የሜንሼቪኩ ማርቲኖቭ በአብዮቱ ውስጥ የወዝአደሩን የበላይነት በግልጽ በመቃወም ተናገረ ። ጓድ ስታሊን ግልጽ ባለ ሁኔታ ለሜንሼቪኮች ሲመልስ ፦—

«የወዝአደሩ የበላይነት ወይስ የዲሞክራቲክ ቡርዧው የበላይነት— በፓርቲው ውስጥ ጥያቄው የተነሳው በእንደዚህ ዓይነት ሲሆን ፣ ይህ የምንለይበት አበይት ነጥብ ነው»

ሜንሼቪኮች በውሳኔያቸው ላይ መንግስታዊው ዱማ የአብዮቱን ችግሮች ለማቃለልና ሕዝቡን ከዛሩ አገዛዝ ሥር ለማግለል ምርጥ መገልገያ መሆኑን ከፍተኛ ዋጋ ይሰጡታል ። ቦልሼቪኮች ደግሞ በተቃራኒው ዱማውን የዛሩ አገዛዝ መገልገያ ፣ የዛሩ አገዛዝ ሕቡዕ አረመኔያዊ ተግባሮችን ለመሸፈን የተዘጋጀ አድርገው ይመለከቱታል ።

በአራተኛው ኮንግረስ የተመረጠው ማእከላዊ ኮሚቴ ሶስት ቦልሼቪኮችንና ስድስት ሜንሼቪኮችን የያዘ ነበር ። የማእከላዊ ልሳን የሚያመጣው የሥነ ጽሁፍ ቦርድ በመላ በሜንሼቪኮች የተያዘ ነበር ።

ውስጠ ፓርቲው ትግል እንደሚቀጥል የማያጠያይቅ ነበር ።

ከአራተኛው ኮንግረስ በኋላ በቦልሼቪኮችና በሜንሼቪኮች መሀከል አዲስ ጠንካራ ግጭት ተፈጠረ ። ቀደም ሲሉ በተባበሩ የአካባቢ ድርጅቶች ውስጥ የኮንግረሱ ዘገባዎች በሁለት ሰዎች ማለትም አንድ ከቦልሼቪክ ሌላው ከሜንሼቪክ እንዲቀርቡ ተደረገ ። በዚህ የሁለት መስመር ውይይት ውጤት አብዛኛው ነጥቦች የድርጅቱን አባላት ማለትም አብዛኛውን ክፍል ከቦልሼቪኮች ጐን እንዲቆሙ አደረጋቸው ።

ድርጊቶች ራሳቸው ቦልሼቪኮች እውነተኛ እንደነበሩ መሰከረ ። በአራተኛው ኮንግረስ የተመረጡት የሜንሼቪክ የማእከላዊ ኮሚቴ አባሎች አድር ባይነታቸውን እየጨመሩ አጐሉት ። የሰፊውን ሕዝብ አብዮት መምራት አለመቻላቸውም እየተረጋገጠ መጣ ። በ1906 የበጋና የበልግ

ጦራት ውስጥ የሰፊው ሕዝብ አብዮት አዲስ ጥንካሬ አገኘ ። በክሮንስታድትና በሳባበርግ የመርከበኞች አመጻዎች ፈነዱ ፣ ገበሬዎች በመሬት ከበርቴዎች ላይ የሚያደርጉት ትግል ተቀጣጠለ ። ሜንሼቪካዊው ማእከላዊ ኮሚቴ ሰፊው ሕዝብ የማይከተለውን አድርባይ መፈክር አንግቦ ተነሣ ።

<u>6/ የመጀመሪያው መንግስታዊ ዱማ መበተን ፣ የሁለተኛው መንግስታዊ ዱማ መጠራት ፤ አምስተኛው የፓርቲ ኮንግረስ ፤ የሁለተኛው መንግስታዊ ዱማ መበተን ፣ ለመጀመሪያው የሩሲያ አብዮት ሽንፈት ምክንያቶች ፦—</u>

የመጀመሪያው መንግስታዊ ዱማ በቂ ታዛዥነቱን ባለማሳየቱ በ1906 ዓ.ም. የበጋ ወራት የዛሩ አስተዳደር እንዲበተን አደረገው ። መንግስቱ ይበልጥ በሕዝቡ ላይ ጥብቅ ጭቆና ማካሄዱን ቀጠለ ። ቅጣት የሚሰጡ ወታደራዊ ቡድኖችን በየሀገሩ በመላክ ከፍተኛ ጥፋታዊ ተግባር ፈጸመና ወዲያውኑ በአጭር ጊዜ ውስጥ ሁለተኛውን መንግስታዊ ዱማ እንደሚጠራ አስታወቀ ። የዛሩ አገዛዝ ይበልጥ የለየለት ጨቋኝ እየሆነ መምጣቱ በግልጽ የሚታይ ሆነ ። አብዮቱ እየረገበ መሄዱን በማየት አብዮቱን መፍራቱን ተወ ።

ቦልሼቪኮች በሁለተኛው ዱማ ውስጥ መሳተፍ ይኖርባቸው እንደሆነ ወይም የማይሳተፉ መሆናቸውን መወሰን ነበረባቸው ። አለመሳተፍ ሲባል ቦልሼቪኮች የሚሉት ንቁውን ዓይነት (ሙሉ በሙሉ) አለመካፈል ማለታቸው እንጂ በምርጫው ውስጥ ድምጽ ባለመስጠት የሚደረገውን ተሳትፎ አልባ ዓይነቱን አይደለም ። ቦልሼቪኮች ሙሉ ለሙሉ አለመካፈልን የዛሩ አገዛዝ ሕዝቡን ከአብዮቱ ፈለግ ለማውጣትና አቅጣጫቸውን በመቀየር የዛራዊ «ሕገ መንግስት» ፈለግ እንዲከተል ለማድረግ እንደ መሳሪያ የሚያደርገውን ጥረት ለማክሸፍ ሕዝቡን ከዛሩ ፍላጐት በተቃራኒ እንዲቆም ለማስገንዘብና አዲስ የማይበገር ማጥቃት በዛሩ ላይ ለማንሳት የሚያስችል አብዮታዊ መሣሪያ አድርገው ተመለከቱት ።

የቡልጂንን ዱማ ካለመካፈል የተገኘው ልምድ እንዳሳየው አለመሳተፍ «በዚያን ወቅት ብቸኛና ትክክለኛ የሆነ ታክቲክ እንዲሁም ድርጊቶች እራሳቸው በሚገባ የመሰከሩለት ነበር ።»
(ሌኒን ምርጥ ስራዎች እንግሊዘኛ እትም ፤ ቅጽ 1 ፤ ገጽ 45)

ይህ አለመካፈል ጥሩ ውጤት ሊያገኝ የቻለበት ምክንያት የዛሩን ሕገ መንግስታዊነት ፈለግ ሕዝቡ እንዲቃወም በማሳሰቡ ብቻ ሳይሆን ነገር ግን ገና የሚፈጠረውን ዱማ እጅግ በማስጨነቁም ጭምር ነበር ። አለመሳተፉ መልካም ውጤት ሊያገኝ የቻለው አብዮታዊ ሞገድ ባሻቀበበት ወቅት በመደረጉና በዚህም ማእበል በመደገፉ ፤ እንዲሁም አብዮቱ በረገበበት ወቅት በሌላ አባባል አብዮቱ እያቆለቆለ በሄደበት ወቅት ባለመሆኑ ነበር ።



ዱማውን መሰብሰብ እጅግ የሚያስፈራ የሚሆነው አብዮቱ በከፍተኛ ማእበል በአደገበት ወቅት ብቻ ሊሆን ይችላል ።

የዊቴ ዱማ ማለትም የመጀመሪያውን ዱማ ያለመሳተፍ የተከናወነው ከታህሣሡ አመጽ ሽንፈት ፣ ዛር ድሉን መቀዳጀቱን ካረጋገጠ ፣ ይኸውም አብዮቱ ለማሽቆልቆል በቂ ምክንያት እንዳለው ከታመነበት በኋላ ነበር ።

«ነገር ግን» ይላል ሌኒን ሲጽፍ «በዚያን ወቅት ይህንን ድል (የዛሩን ማለት ነው ተርጓሚው) እንደ ወሳኝ ድል ተደርጎ የሚያስወስድ ገና አንዳችም መሰረት አለመኖሩ የማያጠያይቅ ሲሆን ፣ የ1905 ዓ. ም. የታህሳሱ አመጽ የተነጣጠሉና ከፊል ወታደራዊ የሆኑ ተከታታይ አመጻዎችንና የሥራ ማቆም አድማዎችን በ1906 ዓ.ም. በበጋው ወራት ያስከተለ ነበር ። ዊቴ ዱማን ላለመሳተፍ የተደረገው ጥሪ ይህን አመጽ ወደ አንድ አቅጣጫ ለማሰባሰብና አጠቃላይ ለማድረግ የተደረገ ጥሪ ነበር ።»
(የሌኒን ስብስብ ሥራዎች ፤ ሩሲያ ፤ እትም ፤ ቅጽ ፤ 12 ገጽ ፤ 20)

የዊቴ ዱማን አለመካፈል ምንም እንኳ የተወሰኑ የሕብረተሰብ ክፍሎች በዚህ ላይ ያላቸውን እምነት ማዳከም ቢችልም የስብሰባውን ጥሪ ማደናቀፍ አልቻለም ። አለመሳተፉ የዱማውን ጥሪ ሊያደናቅፈው ያልቻለበት ምክንያት በማከታተል እየጐላ እንደመጣው አብዮቱ በማሽቆልቆል ላይ ባለበት ፣ አብዮቱ በተዳከመበት ወቅት በመደረጉ ነበር ። በዚህም የተነሳ የ1906ቱ የመጀመሪያውን ዱማ አለመሳተፍ ውጤት አልባ ሊሆን ቻለ ። ከዚህም ጋር በመያያዝ «ግራ ክንፍ ኮሚኒዝምና ጨቅላ ምስቅልቅልነት » በተሰኘው እውቅ ጽሁፉ ሌኒን ሲጽፍ ፦—

« የ1905 ዓ. ምህረቱ የቦልሼቪኮች » በፓርላማው አለመሳተፍ አብዮታዊውን ወዝአደር ከፍተኛ ዋጋ ባለው ፖለቲካዊ ልምድ አበልጽጎታል ። እንዲሁም ሕጋዊውን ከህቡእ ፣ ፓርላማዊውን ከፓርላማ ውጪ ከሆኑ የትግል መስኮችን በማዋሀድ አሳይቷል ። አንዳንድ ጊዜ ፓርላማዊ የትግል መስኮችን መቃወም ጠቃሚና እንዲያውም አስፈላጊ ይሆናል ። . . . በ1906 ዓ. ም. ቦልሼቪኮች በዱማው ውስጥ አለመሳተፍ ያምሆነ ይህ ትንሽና ቀላል የሚቃና ስህተት ነበር . . . ለግለሰቡ የምንጠቀምበትን —አስፈላጊውን ማሻሻል ተደርጐ—ለፖለቲካውና ለፓርቲው እንጠቀምበታለን ። ስህተት ያልፈጸመ አዋቂ ነው ማለት አይደለም ፣ እንደዚህ ዓይነት ሰዎች አልነበሩም ፣ ደግሞም ሊኖሩ አይችሉም ። እጅግ ከባድ ስህተቶችን የማይፈጽምና ስህተቶቹን በቀላሉና በፍጥነት እንዴት እንደሚያርማቸው ካወቀ እሱ አዋቂ ሊባል ይገባል »
(የሌኒን ምርጥ ሥራዎች ፣ እንግሊዝኛ እትም ፣ ሞስኮ ፣ 1947 ፣ ቅጽ 2 ፣ ገጽ 582—83)

እንደ ሁለተኛው መንግሥታዊ ዱማ ከሆነ በሁኔታው መለወጥና በአብዮት ማሽቆልቆል አይን ሲታይ ቦልሼቪኮች « መንግሥታዊውን

ዱማ ያለመሳተፉን ጥያቄ እንደገና እንስተው ሊወያዩበት ይገባቸዋል » ሲል ሌኒን አስገንዘበ ። (ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ቅጽ 1 ገጽ 450)

« ታሪክ በሚገባ እንዳሣየን » ይላል ሌኒን ሲጽፍ « ዱማው በተሰበሰበበት ጊዜ እጅግ ጠቃሚ የሆን ቅስቀሳ በዱማው ውስጥም ሆነ እንዲሁም ከዚሁ ጋር በማያያዝ ከዱማው ውጪ ለማካሄድ መልካም አጋጣሚ ከተፈጠረ—ሀይሎችን ከአብዮታዊ ገበሬዎች ጋር የማያያዙ ታክቲኮች በሕገ-መንግሥታዊ ዲሞክራቶች (አፍቃሪ ሕገ-መንግሥት ያደረባቸው ከተርጓሚው) ላይ በዱማው ውስጥ ሊውሉ ይችላሉ ። »
(ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 453)

ይህ ሁሉ የሚያሳየው አንድ ሰው ማወቅ ያለበት አብዮቱ በአደጋ ላይ በወደቀበት ወቅት በቆራጥነት ወደፊት መራመዱን ብቻ ፣ ማጥቃቱን ብቻ ሳይሆን ነገር ግን በተገቢው ወቅት እንዴት በሚገባ ማፈግፈግ እንዳለበት ጭምር ማወቅ ይኖርበታል ። ማፈግፈጉ የግድ የማይቀር ሲሆን አብዮቱ ከመጣበት አደጋ ሊያመልጥ በማይቻልበት ጊዜ ፣ ከሁኔታው ጋር ታክቲኮችንም በመቀየር በተመሰቃቀለ ሳይሆን በተደራጀ መንገድ ፣ በተረጋጋና ፣ ያለአንዳች መረበሽ እያንዳንዱን የደቂቃ አጋጣሚ በሚገባ በመጠቀም ካድሬዎችን ከሚዥጐደጐደው የጠላት እሳት ፍላጻ በማሸሽ አመራሩን ላለማጣት ፣ ሀይል ለማከማቸትና በጠላት ላይ አዲስ የማጥቃት ምላሽ ለመውሰድ ለመዘጋጀት ማፈግፈጉ ተገቢ ነው ።

ቦልሼቪኮች በሁለተኛው ዱማ ውስጥ ከሚደረገው ምርጫ ለመሳተፍ ወሰኑ ።

ይሁን እንጂ ቦልሼቪኮች ወደ ዱማው የገቡት ሜንሼቪኮች እንዳደረጉት ከሕገ-መንግስታዊ ዲሞክራቶች ጋር በመቀላቀል የ « ሕግ መወሰኛ » አካላዊ ተግባር ለማከናወን አልነበረም ። ነገር ግን ለአብዮቱ ዓላማ እንደመጠቀሚያ መድረክ ሊገለገሉበት ሲሉ ነው እንጂ ።

የሜንሼቪክ ማእከላዊ ኮሚቴ በተቃራኒ የምርጫ ስምምነቶች ከሕገ-መንግሥታዊ ዲሞክራቶች ጋር እንዲደረግና በዱማው ውስጥ ለህገ-መንግሥታዊ ዲሞክራቶች ድጋፍ እንዲሰጥ ታላቅ ግፊት አደረጉ ። በነርሱ አመለካከት ዱማው የዛሩን አገዛዝ ሊለጉመው የሚችል የሕግ መወሰኛ አካል ነበር ።

አብዛኛው የፓርቲው ድርጅቶች ከሜንሼቪኮች ማእከላዊ ኮሚቴ መምሪያ በተቃራኒ የቆሙ መሆናቸውን አረጋግጠዋል ።

ቦልሼቪኮችም አዲስ የፓርቲ ኮንግረስ እንዲጠራ ጥያቄ አቀረቡ ።

በግንቦት ወር 1907 ዓ. ም. አምስተኛው የፓርቲ ኮንግረስ በለንደን ተካሄደ ። ይህ ኮንግረስ በተደረገበት ወቅት የሩ.ስ.ዲ.ሠ.ፓ (ከብሔ



ራዊ ሶሻል-ዲሞክራቲክ ድርጅቶች ጋር በመዳመር) ወደ 150,000 የሚጠጉ አባላት ነበራቸው ። በአጠቃላይ 336 ተወካዮች ኮንግረሱን ሲካፈሉ 150ዎቹ ቦልሼቪኮችና 97 ሜንሼቪኮች ነበሩ ። የተቀሩት ተወካዮች ብሔራዊ ሶሻል-ዲሞክራቲክ ድርጅቶችን የሚወክሉ ፤—የፖላንድ ፤ የላቲቭ ሶሻል-ዲሞክራቶችና ቡንዶች ሲሆኑ ፤ እነዚህም ባለፈው ኮንግረስ ወደ ሩ.ሶ.ዲ.ሠ.ፓ. እንዲገቡ ተፈቅዶላቸዋል ።

ትሮትስኪ በኮንግረሱ ውስጥ የራሱን ቡድን ፤ ከማእከላውያን ፤ ማለትም ከፊል ሜንሼቪክ የሆነ ቡድን በፍጥነት ለማስተባበር ሞክሮ ነበር ። ነገር ግን አንዳችም የሚከተለው አጣና ያሰበው ሳይሳካለት ቀረ ።

ቦልሼቪኮች የፖላንዶችና የላቲቮች የጠበቀ ድጋፍ አላቸውና በኮንግረሱ ውስጥ የማይናወጥ የበላይነት ነበራቸው ።

በኮንግረሱ ውስጥ ከተነሱ ጠቃሚ ነጥቦች አንዱ የቡርዧውን ፓርቲ አስመልክቶ ስለሚኖረው መመሪያ ነበር ። እንደሚታወሰው በሁለተኛው ኮንግረስ ላይ በዚሁ ጥያቄ በሜንሼቪኮችና በቦልሼቪኮች መሀከል ትግል ተካሄዶበት ነበር ። አምስተኛው ኮንግረስ ለመላው ወዝ አደር አልባ ፓርቲዎች ቦልሼቪካዊ አስተሳሰብ ሰነዘረ ። — ጽልመተ መቶዎች ጥቅምታውያን (የጥቅምት አስራ ሰባቱ አንድነት ) ፣ ሕገ መንግሥታዊ ዲሞክራቶችና ሶሻሊስት አብዮታውያን-ፓርቲዎችን አስመልክቶ ቦልሼቪካዊ ታክቲኮችን ለማራመድ ቀመረ ።

ኮንግረሱ የቦልሼቪኮችን መመሪያ አረጋገጠና የጽልመተ መቶዎችን ፓርቲ-የሩስያ ሕዝብ ሊግ ፣ ዘውደኞቹ ፣ የተባበሩት የመኳንንቶች ምክር ቤት-እንዲሁም ጥቅምታውያን ፣ ንግዳዊና ኢንዱስትሪያዊ ፓርቲና የሠላማዊ ግንባታ ፓርቲ ላይ በአንድነት ጠንካራ የተቃውሞ ትግል ለማድረግ ወሰነ ። እነዚህ ሁሉ ፓርቲዎች የለየላቸው ጸረ-አብዮታውያን ናቸው ።

ለዘብተኛ ቡርዧውን ፤ ይህም ፣ ሕገ መንግስታዊው ዲሞክራቲክ ፓርቲን በሚመለከት ረገድ ኮንግረሱ የማይታረቅ የማጋለጥ መመሪያ አወጣ ። የሕገ-መንግስታዊ-ዲሞክራቲክ ፓርቲን ውሸታምና አስመሳይ « ዲሞክራሲን » ማጋለጥና ለዘብተኛ ቡርዧው የገበሬውን ንቅናቄ በቁጥጥር ሥር ለማድረግ የሚያደርገውን ጥረት በሚገባ የመዋጋት መመሪያ ነበር ።

ናሮድኒክ ወይም ትሩዶቪክ የተሰኙትን ፓርቲዎች (ሕዝባዊ ሶሻሊስቶች ፣ የትሩዶቪክ ቡድኖችና ሶሻሊስት አብዮተኞች) አስመልክቶ ኮንግረሱ ሶሻሊስት ለመምሰል የሚያደርጉት ደባ መጋለጥ እንዳለበት አሳሰበ ። እነዚህ ፓርቲዎች ዲሞክራሲያዊ ፓርቲዎች እንደመሆናቸው (ትሮዶቪክ ፣—በ1906 ዓ. ም. በሶሻሊስት አብዮታዊ ምሁራን የሚመራ የመጀመሪያው መንግሥታዊ ዱማ አባል የሆኑ ገበሬዎችን በከፊል በመያዝ የተመሠረተ የንዑስ ከበርቴ ቡድን ነው ።)

መጠን በከተሞችና በመላው ሀገሪቷ ያሉትን የንዑስ ከበርቴዎች ፍላ
ጐት የሚያንፀባርቁ ናቸውና አሁንና በዚያን ወቅት ከነዚህ ፓርቲዎች
ጋር ለመተባበር ለመስማማትና በአንድነት የዛሩን አገዛዝና ሕገ-መንግ
ሥታዊ ዲሞክራቲክ ቡርዧውን ለመውጋት እንደሚቻል ኩንግረሱ
ተመለከተ ።

እንዲያውም ከዚህ ኮንግረስ በፊት ሜንሺቪኮች « የሠራተኛ ኮንግ
ረስ» የተሰኘው እንዲጠራ አሳስበው ነበር ። ይህን ሲሉ የሜንሺቪኮች
ሀሳብ ሶሻል ዲሞክራቶች ፣ ሶሻሊስት አብዮተኞችና ሥርዓተ አልበ
ኞች የሚሳተፉበትን ኮንግረስ ለመጥራት ነበር ። ይህ «የሠራተኛ» ኮን
ግረስ « አፍቅሮተ ፓርቲ — አልባ » ባህርይ ያለው አንድ ዓይነት ነገር
ወይም መርሀ-ግብር የሌለው « ሠፊ » የንዑስ ከበርቴ ፓርቲ ለመመስረት
ነበር ። ሌኒን በሜንሺቪኮች በኩል የሶሻል ዲሞክራቲክ የሠራተኞች
ፓርቲ ለመበተንና የሠራተኛውን መደብ ግንባር ቀደም በንዑስ ከበርቴ
ጥርቃሞዎች ለማጀል የሚያደርጉትን ይህን ፍጹም ጉጂ የሆነ ተግባር
አጋለጠ ። ኮንግረሱ ሜንሺቪኮች « የሠራተኛ ኮንግረስ » እንዲጠራ ያቀ
ረቡትን ጥያቄ በጽኑ አወገዘ ።

በኮንግረሱ ውስጥ የተለየ ትኩረት የተደረገበት በሙያ ማህበራት
ርዕሰ ላይ ነበር ። ሜንሺቪኮች የሙያ ማህበራት « ገለልተኞች » መሆን
እንዳለባቸው ያወሳሉ ። በሌላ አባባል ፣ በሙያ ማህበራት ውስጥ ፓርቲው
የመሪነት ሚና መጫወቱን አጥብቀው ይቃወማሉ ። ኮንግረሱ የሜንሺቪ
ኮችን ውሳኔ በማውገዝ በቦልሺቪኮች የቀረበውን ውሳኔ አጽድቆ ተቀበለ ።
ይህ ውሳኔ እንደሚያወሳው ፓርቲው በሙያ ማህበራት ውስጥ የርእዮተ-
ዓለምና የፖለቲካ መሪነት ማግኘት አለበት ።

አምስተኛው ኮንግረስ በሠራተኛው መደብ ንቅናቄ ውስጥ ለቦልሺ
ቪኮች ታላቅ ድል አስገኘ ። ይሁን እንጂ ይህ የተገኘው ድል ቦልሺቪኮቹ
ራሳቸውን እንዲያዞሩ ወይም በአገኙት ድል እንዲዘናጉ አላደረጋቸውም ።
እንደዚያ እንዲያደርጉ ሌኒን አላስተማራቸውምና ።

ቦልሺቪኮች ገና ከሜንሺቪኮች ጋር ጠንካራ ትግል እንደሚጠብ
ቃቸው ጠንቅቀው ያውቃሉ ።

«የተወካይ ማስታወሻ» በተሰኘው በ1907 ዓ. ም. በወጣችው ጽሁፉ
ጓድ ስታሊን የኮንግረሱን ውጤት እንደሚከተለው ገምግሞታል ።

«የመላው ሩሲያ የተራመዱ ሠራተኞች በአንድ የሶሻል-ዲሞክራሲ
አብዮታዊ ሰንደቅ ሥር መሰለፋቸው-ያ ነው የሎንዶኑ ኮንግረስ ትርጉም ፣
ያ ነው አጠቃላይ ባሕሪው ።»



በዚህ ጽሁፍ ውስጥ ጓድ ስታሊን የኮንግረሱን ተሳትፎ መረጃዎችን
እያስቀመጠ አሳየ ። መረጃዎቹ እንደሚያሳዩት የቦልሺቪክ ተወካዮች
ተመርጠው ለኮንግረሱ አብዛኛውን ከትላልቅ ኢንዱስትሪያዊ ማእከል
(ከቅዱስ ፒተርስበርግ ፣ ከሞስኮ ፣ ከዑራልስ ፣ ኢባኖቮዝ—ኔሴንስክ ወዘተ...)
ሲሆኑ ሜንሺቪኮች ደግሞ ተወካዮቻቸውን ያገኙት ጥቃቅን ምርት ከተስ
ፋፋበት አካባቢ ፣ ከእደ ጥበብ ባለሙያዎች ፣ ከፊል ወዝአደሮች ከበዙበት
እንዲሁም ከአያሌ የገጠር አካባቢዎች ነበር ።

«በግልጽ እንደሚታየው» ይላል ጓድ ስታሊን የኮንግረሱን ውጤት
በመገምገም ፤ «የቦልሺቪኮች ታክቲኮች በትላልቅ ኢንዱስትሪ ውስጥ
ያሉ ወዝአደሮች ታክቲኮች ፣ መደባዊ ቅራኔው በገሀድ የሚታይበትና
የመደብ ትግሉ በተለይ የከረረበት የነዚህ አካባቢዎች ታክቲኮች ናቸው ።
በሌላ በኩል ደግሞ የሜንሺቪኮች ታክቲኮች በቅድሚያ የእደ ጥበብ ሰራ
ተኞችና የገበሬ ከፊል ወዝአደሮች ታክቲኮች እንዲሁም የመደብ ትግሉ
ግልጽ ያልሆነበትና የተድበሰበሰበት አካባቢ ታክቲኮች ናቸው ። ሜንሺቪ
ካዊነት በወዝአደሩ መሀከል ያሉ የመለስተኛ ቡርዧ ታክቲኮች» ናቸው ።
(የሩ.ሶ.ዲ.ሠ.ፓ አምስተኛ ኩንግረስ ያቀረበው የጽሑፍ ዘገባ ፣ የሩሲያ እትም1935፣ገጽ11-12)

ዛሩ የመጀመሪያውን መንግስታዊ ዱማ በበተነበት ወቅት ሁለተ
ኛው ዱማ ያለአንዳች ችግር በቀላሉ በቁጥጥር ስር ሊውል የሚችል አድ
ርጐ ገምቶ ነበር ። ነገር ግን ሁለተኛው ዱማ እንዲሁ አስተሳሰቡ የተሳሳተ
መሆኑን አሳየ ። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ ዛሩ ይህንንም እንዲሁ በመበተን
ይበልጥ መብቱን በመወሰን ሶስተኛውን ዱማ ለማሰባሰብ ሲወስን ይህ
የሚመሰረተው ዱማ በቁጥጥር ሥር ለመሆን የሚችል መሆኑን ተጎናፉ
በማድረግ ነበር ።

በአጭሩ ከአምስተኛው ኮንግረስ በኋላ የዛሩ አገዛዝ የሰኔ 3ቱ መፈን
ቅለ መንግስት የተሰኘው መጥፎ አጋጣሚ ደረሰበት ። በሰኔ 3 ቀን 1907
ዓ.ም. ዛሩ ሁለተኛውን መንግስታዊ ዱማ በተነ ። በዱማው ውስጥ የነበሩ
65 የሶሻል-ዲሞክራቲክ ቡድን ተወካዮች ታስረው ወደ ሳይቤሪያ ተጋዙ ።
አዲስ የምርጫ ሕግ ታወጀ ። ወዝአደሮችና ገበሬዎች የነበሩአቸው መብ
ቶች አሁንም በበለጠ ሁኔታ ታፈኑባቸው ። የዛሩ አገዛዝ አሁንም ማጥቃ
ቱን ቀጠለ ።

የዛሩ ሚኒስተር የነበረው ስቶልፒን በሠራተኞችና በገበሬዎች ላይ
በደም የተነከረ ግፉን አስፋፋ ። በሺህ የሚቆጠሩ ወዝአደሮችና ገበሬዎች
በወታደራዊ ቡድኖች ተረሸኑ ፣ ወይም ተሰቀሉ ። በዛረስት ሩሲያ ውስጥ
አብዮታውያን በእእምሯቸውም ሆነ በአካላቸው ኢ-ሰብአዊ በሆነ መን
ገድ ተሰቃዩ ። በተለይ ደግሞ እጅግ አረመኔነት የተሞላበት ጭፍጨፋ
የተካሄደው በሰራተኛው-መደብ ድርጅቶች በተለይ ደግሞ ቦልሼቪኮች
ላይ ነበር ። የዛሩ የደም ጥመኞች በፊንላንድ ራሱን ለመደበቅ የተሰደደውን

ሌኒንን ለማግኘት ይቅበዘበዙ ነበር ። በአብዮታዊ መሪዎች ላይ የበቀል እርምጃ ለመውሰድ ታላቅ ፍላጐት ነበራቸው ። በታህሣሥ ወር 1907 ዓ.ም. ውስጥ ሌኒን ከሚያንገርብብበት አደጋ በማምለጥ ሕይወቱን ለማዳን ወደ ባህር ማዶ እንዲሰደድ ተገደደ ።

የስቶልፒን አድሀሪ የጽልመት መረብ ረበበ ።
የመጀመሪያውም የሩሲያውያን አብዮት በሽንፈት አከተመ ።
ይህንን ሽንፈት ያስከተሉ ምክንያቶች የሚከተሉት ነበሩ ።

1. በአብዮቱ ውስጥ በወዝአደሩና በገበሬው መሀከል የዛሩን አገዛዝ ለመቃወም እስካሁን ጠንካራ አንድነት አልተመሰረተም ። ገበሬዎች የመሬት ከበርቴዎችን በመቃወም ለሚደረገው ትግል በቆራጥነት ተነሱና እነዚህን ጠላቶቻቸውን ለማንበርከክ ከሠራተኞች ጋር ሕብረት ለመፍጠር ፈለጉ ። ነገር ግን እነዚያ ደመኛ ጠላቶቻቸው የሆኑት የመሬት ከበርቴዎች የዛሩ አገዛዝ ካልተደመሰሰ በቀር ሊንበረከኩ እንደማይችሉ ገና አላጤኑትም ። የዛሩ አገዛዝ ከመሬት ከበርቴዎች ጋር ትከሻ ለትከሻ ተደጋግፈው እጅ ለእጅ ተስሳረው አፍ ለአፍ ተመሳጥረው እንደሚሰሩ አልተረዱትምና በብዙ የሚቆጠሩ ገበሬዎች አሁንም በዛሩ ላይ ታላቅ እምነት ጥለዋል ። እንዲሁም በዛሩ መንግሥታዊ ዱማ ላይ ከፍተኛ ተስፋ አሳድረዋል ። ለዚህ ነው የማይናቁ የገበሬ ክፍሎች የዛሩን አረመኔያዊ አገዛዝ ገርስሶ ለመጣል ከሰራተኞች ጋር ሕብረት ለመፍጠር ያላዘነበሉት ። ገበሬዎች ከእውነተኛ አብዮታውያን-ከቦልሼቪኮች-ይልቅ እርቅ ፈላጊዎች ሶሻሊስት-አብዮተኞችን የበለጠ ያምኑ ነበር ። በዚህም የተነሳ የመሬት ከበርቴዎችን በመቃወም ገበሬዎች ያደረጉት ትግል በሚገባ የተደራጀ አልነበረም ።

ሌኒን እንዳለው «የገበሬዎች እንቅስቃሴ በጣም የተበታተነ ፣ ይበልጥ ያልተደራጀና በሚገባ ያልተጠናከረ ነበርና ለአብዮቱ ሽንፈት አንዱ መሰረታዊ ምክንያት ሲሆን በቃ» (የሌኒን ስብስብ ሥራዎች ፣ የሩስያ እትም ቅጽ 19 ፣ ገጽ 354)

2. የዛሩን አገዛዝ ገርስሶ ለመጣል የገበሬው አብዛኛው ክፍል ከሰራተኛው ጋር ሕብረት ለመፍጠር ዝንባሌ አለማሳየቱ እንዲሁ የተቦጫጨቀ ወታደራዊ ዩኒፎርም የለበሱ የገበሬ ልጆች በሚገኙበት የጦር ሰራዊቱ ባሕርይ ላይ ተጽእኖ አሳደረበት ። በአንዳንድ የዛር ወታደራዊ ክፍሎች አመጽ ቢፈነዳም ፣ አብዛኛው ወታደራዊ ክፍል አሁንም የሠራተኞችን የሥራ ማቆም አድማና አመጸውን ለማፈን ዛሩን ይረዳል ።

3. የሠራተኛውም ተግባር ቢሆን በሚገባ የተባበረ አልነበረም ። የሰራተኛው መደብ የተራመዱ ክፍሎች በ1905 ዓ.ም. ውስጥ በጀግንነት አብዮታዊ ትግሉን ጀመሩ ። እጅግ ኋላ ቀር የሆኑ ክፍሎች በኢንዱስትሪ



ያቸው ዝቅተኛ የሆኑ ጠቅላይ ግዛቶች የሚገኙ ሠራተኞች ፣ በመንደሮች የሚኖሩት—እንቅስቃሴውን መሳተፍ የጀመሩት ዘግየት ብለው ሲሆን ፤ እነርሱ በአብዮታዊ ትግል ውስጥ የተሳተፉት በተለይ በ1906 ዓ.ም. ላይ ነበር ። ይሁን እንጂ በዚያን ወቅት የሠራተኛው መደብ ግንባር ቀደም በጣም ተዳክሞ ነበር ።

4. የሠራተኛው መደብ ትልቁና ዋንኛው የአብዮቱ ሀይል ሲሆን ፣ ነገር ግን አስፈላጊው አንድነትና ሕብረት በሠራተኛው መደብ ፓርቲ ውስጥ አልነበረም ። የሩ.ሶ.ዲ.ሠ.ፓ የሠራተኛው መደብ ፓርቲ በሁለት ቡድኖች ተከፍሎ ነበር — ቦልሼቪኮችና ሜንሼቪኮች ። ቦልሼቪኮች ጠንካራ አብዮታዊ መስመር ያራምዳሉና የዛሩን ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ለመገርሰስ ለሰራተኞች ሁሉ ጥሪ አደረጉ ። ሜንሼቪኮች ደግሞ በዚያ ታራቂ ታክቲኮቻቸው አብዮቱን አሰናከሉት ፣ በብዙ በሚቆጠሩ ሠራተኞች ሀሊና ላይ ውዥንብር በመንዛት የሠራተኛውን መደብ ከፋፈሉት ፣ ስለዚህም ሠራተኞቹ በአብዮቱ ውስጥ ዘወትር የተቀናጀ ተግባር እያካሄዱም እና በአመራሩ ውስጥ አሁንም አንድነት ከራቀው የሠራተኛው መደብ የአብዮቱ እውነተኛ መሪ ሲሆን ከቶም አልቻለም ።

5. የዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ የ1905 ዓ.ም. አብዮት ለማክሸፍ ከምእራብ አውሮፓ ኢምፔሪያሊስቶች ጠንካራ ድጋፍ አግኝቶ ነበር ። ከሩሲያ ውጪ ያሉ ካፒታሊስቶች በሩስያ ላስቀመጡት መዋእለ ነዋይና ከፍተኛ ትርፎች ሥጋት ገባቸው ። ከዚያም በላይ በሩስያ አብዮቱ ድል የተጐናጸፈ እንደሆን የሌላም አገር ሠራተኞች አብዮት እንደነርሱ ያስነሳሉ ሲሉ ብርክ ያዛቸው ። በዚህም የተነሳ የምእራብ አውሮፓ ኢምፔሪያሊስቶች ሰው በላውን የዛር አገዛዝ መደገፍን ተያያዙት ። የፈረንሳይ ባለባንኮች የዛሩ አገዛዝ አብዮቱን ማፈን እንዲያስችለው ታላቅ ገንዘብ ሰጡት ። የጀርመኑ ቄሳር የዛሩን አገዛዝ ለመርዳት በሩስያ ጉዳይ ጣልቃ ለመግባት ወታደሮቹን በተጠንቀቅ አስቀመጠ ።

6. በመስከረም ወር 1905 ዓ.ም. ከጃፓን ጋር እርቅ ለማውረድ የተደረገው እርምጃ በማያጠያይቅ ሁኔታ የዛሩን አገዛዝ ረዳ ። በጦርነት መሸነፍና የአብዮቱ አደገኛነት እያደገ መሄድ የሰላሙ ድርድር እንዲፋጠን ዛሩን አስገደደ ። በጦርነት መሸነፉ የዛሩን አገዛዝ አዳከመው ። ሰላም ለማውረድ የተደረገው መደምደሚያ የዛሩን አቋም አጠናከረው ።

## አጭር ድርሞ

የመጀመሪያው የሩሲያ አብዮት የሀገራችንን እድገት መላውን ታሪካዊ ደረጃ ያጠቃልላል ። ይህንን ታሪካዊ ደረጃ በሁለት ወቅቶች ከፍሎ ማየት ይቻላል ፤ የመጀመሪያው ወቅት በጥቅምት የፈነዳው አብዮት ከአጠቃላይ ፖለቲካዊ የሥራ ማቆም አድማ ወደ ታህሳሱ የትጥቅ አመጽ የማደጉ ፤ በማንቹሪያ የጦር ሜዳ ላይ ዛር ድል የመመታቱ ፤ የቡልጂን ዱማ

መበተንና ዛር ከአንድ ድርድር ወደ ሌላው የሚራወጥበት ወቅት ሲሆን ፤ ሁለተኛው ደግሞ ፤ የዛሩ አገዛዝ ከጃፓን ጋር እርቅ ካወረደ በኋላ ፤ ለዘብተኛው ቡርዧው በአብዮቱ ላይ ያለውን ፍርሃትና የገበሬውን ወላዋይነት በመጠቀም የዊቴ ዱማን እንደችግር ማቃለያ አድርጐ በማቅረብ በሰራተኛው መደብ ፤ በአብዮቱ ላይ የጥቃት እርምጃ ለማድረግ የተሸጋገረበት ወቅት ነበር ።

በሶስት ዓመት አጭር ጊዜ ውስጥ (1905—07) የሠራተኛው መደብና ገበሬዎች በ30 ዓመት የሠላማዊ እድገት ዘመን ውስጥ ሊያገኙ የማይችሉትን የፖለቲካ ትምህርት ቀሰሙ ። በብዙ ዓመታት ሰላማዊ ሂደት ወቅቶች የማይገለጹ ነገሮች በጥቂት የአብዮት አመታት ውስጥ ጉልህ ይሆናሉ ።

አብዮቱ ፡-የዛሩ አገዛዝ መቃብር ብቻ እንደሚያቃናው ጉባጣ የጠመመ የሕዝቡ ቀንደኛ ጠላት መሆኑን በሚገባ አጋለጠ ።

አብዮቱ ፡-ለዘብተኛ ቡርዧው ከሕዝቡ ሳይሆን ከዛሩ ጋር ሕብረት ለመፍጠር እንደሚሻ በግልጽ አሳየ ። በመሆኑም ለዘብተኛ ቡርዧው ጸረ-አብዮተኛ ሀይል ነበርና ከርሱ ጋር ሕብረት መፍጠር ሕዝቡንና አብዮቱን እንደመካድ ይቆጠራል ።

አብዮቱ ፡— የቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት መሪ ሊሆን የሚችለው የሠራተኛው መደብ ብቻ እንደሆነ በሚገባ አሳየ ። ለዘብተኛው ሕገ መንግሥታዊ—ዲሞክራቲክ ቡርዧው በማግለል በገበሬው ላይ የሚኖረው የቡርዧውን ተጽእኖ በመደርመስ፣የመሬት ከበርቴዎችን ድባቅ በመምታት ፤ አብዮቱን ለማጠናቀቅና ለሶሻሊዝም ጥርጊያ መንገድ ለመክፈት የሚችለው እርሱ ብቻ መሆኑን አመለከተ ።

በመጨረሻም አብዮቱ ሠራተኛው ገበሬ ከማወላወሉ በቀር ከሠራተኛው መደብ ጋር ሕብረት ለመፍጠር የሚችል አንድ ብቸኛ ጠቃሚ ሀይል መሆኑን አረጋግጧል ።

በአብዮቱ ወቅት በሩ.ሶ.ዲ.ሠ.ፓ.ውስጥ ሁለት የሚያጨቃጭቁ መስመሮች ማለትም የቦልሼቪኮችና የሚንሼቪኮች የፖለቲካ መስመሮች ነበሩ። ቦልሼቪኮች በራሳቸው በኩል የአብዮቱን መቀጠል ፤ የዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ በትጥቃዊ አመጽ እንዲደመሰስና የሠራተኛው መደብ የበላይነት እንዲረጋገጥ ፤ ሕገ መንግሥታዊ—ዲሞክራቲክ ቡርዧውን በማግለል ፤ ከገበሬው ጋር ጠንካራ ሕብረት በመፍጠር ፤ የሚመሠረተው ጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥት የሠራተኛውንና የገበሬውን ተወካዮች ያቀፈ እንዲሆንና ብሎም አብዮቱን በድል አድራጊነት ለማጠናቀቅ ነበር ። በተቃራኒው ደግሞ ሜንሼቪኮች የወሰዱት አቋም አብዮቱን መደምሰስ ሲሆን፤ የዛሩን ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ በትጥቃዊ አመጽ በመገርሰስ ፋንታ «እናሻሽለው» በሚል ፈሊጥ ከወዝአደሩ የበላይነት ይልቅ የለዘብተኛ ቡርዧው የበላይነት እንዲመሠረት አሳሰቡ ። ከገበሬው ጋር የጠነከረ ሕብረት ከመፍጠር ይልቅ ከሕገ መንግሥታዊ — ዲሞክራቲክ ቡርዧ ጋር ሕብረት መፍጠሩን መረጡ ፤ ከጊዜያዊ አብዮታዊ መንግሥት ይልቅ መንግሥታዊ ዱማን እንደ የሀገሪቱ « አብዮታዊ ሀይሎች » ማእከል እንዲሆን አሳሰቡ ።

ስለሆነም ሜንሼቪኮች በእርቅ ማጥ ውስጥ ዘቀጡና ቡርዧው በወዝአደሩ ላይ ለሚያደርገው ተጽእኖ ልክ በሠራተኛው መደብ ውስጥ እንደሚገኝ ሠላዮች ፀዋሬ ሆኑ ።

በሀገሪቷና በፓርቲው ውስጥ ቦልሼቪኮች ብቸኛ አብዮታውያን መሆናቸው ተረጋገጠ ።

በዚህ በሰፋ ልዩነት ውስጥ የሩ.ሲ.ዲ.ሠ.ፓ ወደ ሁለት ፓርቲ የመከፈሉ የግድ እንዳለበት ተረጋገጠ—የሜንሼቪኮች ፓርቲና የቦልሼቪኮች ፓርቲ ነገር ነው ። አራተኛው የፓርቲ ኮንግረስ በፓርቲው ውስጥ ያለውን እውነተኛ ጉዳይ አንዳችም አለወጠውም፤ በቅርጽ ብቻ የተደገፈውን የፓርቲ አንድነት በመጠበቅ አጠናከረውእንጂ ። አምስተኛው የፓርቲ ኮንግረስ እውነተኛውን አንድነት፤ በቦልሼቪኮች ሰንደቅ ስር የተገኘውን አንድነት አንድ እርምጃ ወደፊት አራምዷል ።

አብዮቱን ስንመረምር አምስተኛው የፓርቲ ኮንግረስ የሜንሼቪኮች መስመር እንደ አንዱ ታሪቂ በማድረግ ሲያወግዘው በአንጻሩ የቦልሼቪኮችን መስመር አብዮታዊና ማርክሳዊ መስመር በማድረግ ተቀብሎታል። ይህን አቋም በመውሰዱ የመጀመሪያው የሩስያ አብዮት መላው ሂደት ያጠናከረውን ደግሞ ይበልጥ አጠናከረ ።

ቦልሼቪኮች ሁኔታው የጠየቀውን ነገር ማራመድ እንደሚችል በግንባር ቀደም ማሰለፍና መላውን ሕዝብ ለማጥቃት መምራት በሚገባ ጠንቅቀው እንደሚያውቁ አብዮቱ በገሀድ አሳይቷል ።

ይሁን እንጂ ቦልሼቪኮች ሁኔታው መጥፎ በሆነበትና፤ አብዮቱ ባሽቆለቆለበት ወቅት በተገቢው መንገድ እንዴት ማፈግፈግ እንዳለባቸው ጠንቅቀው ያውቃሉና ቦልሼቪኮች ካድሬዎቻቸውን ለማዳን ፤ ሀይላቸውን ለማከማቸትና ከአዲሱ ሁኔታ ጋር ራሳቸውን ለማጣጣምና እንደገና በጠላት ላይ የማጥቃት እርምጃ ለመውሰድ እንዲያስችላቸው ያለአንዳች መደናገጥ ፤ ያለአንዳች ሽብር ማፈግፈግን ተምረዋል ።

እንዴት ማጥቃት እንደሚቻል ጠንቅቀው ካላወቁ ጠላትን ማሸነፍ ከቶም አይቻልም ።

በሽንፈት ወቅት ያለመደናገጥና ያለአንዳች መሸበር እንዴት በሚገባ ማፈግፈግ እንደሚቻል ጠንቅቀው ካላወቁ አጠቃላይ ሽንፈትን ለማስቀረት ከቶም አይቻልም ።

ምእራፍ አራት ።

# ቦልሼቪኮችና ሜንሼቪኮች በስቶልፒን የአድህሮት እንቅስቃሴ ወቅት ፤ ቦልሼቪኮች እራሳቸውን ነጻ ማርክሳዊ ፓርቲ አድርገው ማቋቋማቸው ፤

(1908—1912)

1/የስቶልፒን አድህሮት እንቅስቃሴ በተቃዋሚ ምሁራን መሀከል የተፈጠረው አለመግባባት ማዝቀጥ፣የፓርቲው አንዱ የምሁራን ክፍል ከማርክሲስት ጠላቶች ጋር በመቀላቀል መክዳትና የማርክሲዝምን ንድፈ-ሀሳብ ለመከለስ ያደረገው ጥረት ፣ ሌኒን «ቁስ አካላዊነትና ተግባራዊ ትችት» በተሰኘው ጽሑፉ የከላሾችን ክርክር ድባቅ መምታቱና ለማርክሲስት ፓርቲ ንድፈ-ሀሳባዊ መሠረቶችን ለመጠበቅ ያደረገው መቋቋም ፣

ሁለተኛው መንግሥታዊ ዱማ በሰኔ 3 ቀን 1907 ዓ. ም. በዛሩ አገዛዝ እንዲበተን ተደረገ ። ይህ በተለምዶ የሰኔ ሶስቱ መፈንቅለ መንግሥት በማለት በታሪክ ውስጥ ይወሳል ። የዛሩ አገዛዝ ለሶስተኛው መንግሥታዊ ዱማ ምርጫ አዲስ ህግ እንዲረቅ በማድረግ አዲስ ህግ ሊጸድቅ የሚችለው በዱማው ውሳኔ ብቻ ነው ሲል በጥቅምት 17/1905 ዓ. ም. ያወጣውን የራሱን መግለጫ ተጻረረ ። በሁለተኛው ዱማ ውስጥ የነበሩ የሶሻል ዲሞክራሲ ቡድን አባሎች ለፍርድ ሲቀርቡ የሠራተኛው መደብ ተወካዮችም በግዞት መልክ እንዲቀጡ ተደረገ ።

አዲሱ የምርጫው ሕግ በዱማው ውስጥ የሚገቡትን የመሬት ከበርቴዎችና የንግድና የኢንዱስትሪ ቡርዧ ተወካዮች ቁጥር እንዲጨምር በሚያስችል መንገድ ተነደፈ ። ከዚሁ ጋር የገበሬውና የሠራተኛው ውክልና ቀድሞ ከነበረው ዝቅተኛ ቁጥር ወደ ቀድሞ መጠኑ ዝቅ እንዲል ተደረገ ።

ጽልመተ መቶዎችና ሕገመንግሥታዊ ዲሞክራቶች በሶስተኛው ዱማ ውስጥ አብዛኛውን ቁጥር ያዙ ። ከነበሩት 442 ተወካዮች 171 ቀኞች (ጽልመተ መቶዎች)፣133 ደግሞ ጥቅምታውያን አሊያም ተዛምዶ ያላቸው ቡድኖች ሲሆኑ 13 ትሩዶቪክ ፣ እንዲሁም 18 ሶሻል-ዲሞክራቶች ነበሩ ።

ቀኞች (እንዲህ ተብለው የሚጠሩት በዱማው ውስጥ በቀኝ በኩል ያለውን መቀመጫዎች ይዘው ስለነበረ ነው) የሠራተኛውንና የገበሬውን ቀንደኛ ጠላቶች ይወክላሉ ። በገበሬዎች አመጽ ጊዜ አመጻውን ለማፈን በጅምላ ጀርባቸው እስኪተላ የገረፉና በጥይት ዶፍ አያሌ ገበሬዎችን የረፈረፉ ፣ የአይሁድ የገዳይ ቡድኖችን በማደራጀት ሠራተኞች ሠላማዊ ሰልፍ ሲያደርጉ የጨፈጨፉ ፣ በአብዮቱ ወቅት ስብሰባዎች የሚካሄድባቸውን ትላልቅ ቤቶችና ህንጻዎች በእሳት ያጋዩት አረመኔዎቹ ጽል



መተ-መቶዎች መልከኛ የመሬት ከበርቴዎች ነበር ። ቀኞች የቆሙት በሠራተኞች ላይ ለሚፈጽመው ኢ-ሰብአዊ ጭቆና እና ወሰን ለሌለው የዛሩ ሥልጣን ነውና ጥቅምት 17/1905 ዓ. ም ዛሩ ያወጣውን መግለጫ ተቃውመዋል ።

የጥቅምታውያኑ ፓርቲ ወይም የጥቅምት አስራ ሰባቱ አንድነት በዱማ ውስጥ ይበልጡን ከቀኞች ጋር ይቀራረባል ። ጥቅምታውያን ትልቁን የኢንዱስትሪያዊ ካፒታልና ሁዳዶቻቸውን በካፒታሊስቶች መስመር የሚያራምዱትን የትላልቅ የመሬት ከበርቴዎችን ጥቅም (በአብዮቱ መጀመሪያ ላይ ማለትም በ1905 ዓ. ም.) አያሌ ትላልቅ የመሬት ከበርቴዎች የሕገመንግሥታዊ ዲሞክራቲክ ፓርቲ አባል የነበሩት ለጥቅምታውያን ጥቅም የሚያስጠብቁ ነበሩ ። ጥቅምታውያንን ከቀኞች የሚለያቸው አንድ ብቸኛ ነጥብ ቢኖር የጥቅምት 17ቱን መግለጫ በቃላት ብቻ መቀበላቸው ሲሆን ። ጥቅምታውያን የዛሩን የውስጥና የውጪ መመሪያ በሚገባ ይደግ ነበር ።

ሕገ መንግሥታዊው ዲሞክራቲክ ፓርቲ በሶስተኛው ዱማ የነበረው ቦታ ከመጀመሪያውና ከሁለተኛው ዱማ አንጻር በጣም ትንሽ መቀመጫዎች ነበሩት ። ይህ ሊሆን የቻለው የመሬት ከበርቴዎች ከፊሉ ድምጽ ከሕገ መንግሥታዊ ዲሞክራቶች ወደ ጥቅምታውያን በመተላለፉ ነው ።

ትሩዶቪኪ በመባል የሚጠሩ ጥቂት የንዑስ ከበርቴ ዲሞክራቶች ቡድንም በሶስተኛው ዱማው ውስጥ ነበር ። እነርሱም በሕገመንግሥታዊ ዲሞክራቶችና በሠራተኛ ዲሞክራቶች (ቦልሼቪኮች) መሀከል ይዋዥቁ ነበር ። ምንም እንኳ ትሩዶቪኪ በዱማ ውስጥ ያለቅጥ ደካሞች ቢሆኑም ሰፊውን ሕዝብ ፣ ሰፊውን ገበሬ ይወክላሉ ሲል ሌኒን አስገንዝቧል ። የትሩዶቪኪ በሕገመንግስታዊ ዴሞክራቶችና በሠራተኛው ዲሞክራቶች መሀከል መዋለል የአነስተኛ ንብረት ባለቤትነት የማይቀር መደባዊ አቋም ነው ። ቀደም ብሎ ሌኒን የቦልሼቪክ ተወካዮችን ሠራተኛ ዲሞክራቶችን ፣ «በለዘብተኞች ከሚደርስባቸው እጅግ መጥፎ ተጽእኖ ለማላቀቅ ዲሞክራሲያዊ ካምፓችን በጸረ-አብዮተኞች በቀኞች ብቻ ሳይሆን በሕገ መንግስታዊ ዲሞክራቶችም ጭምር በማስነሳት ደካማ የንዑስ ከበርቴ ዲሞክራቶችን እርዱ. . . . .» የሚለውን ተግባር ከፊታቸው አስቀመጠ ።
(ሌኒን ምርጥ ሥራዎች ፣ እንግሊዘኛ እትም ፣ ሞስኮ ፣ 1947 ዓ. ም. ቅጽ 1 ገጽ 533)

በ1905 ዓ.ም. የአብዮት ወቅት በተለይ ከሽንፈቱ በኋላ ፣ ሕገ መንግሥታዊ ዲሞክራቶች ከመቼውም ጊዜ ይልቅ የለበሱትን «ዲሞክራሲያዊ ካባ በማውለቅ የጸረ-አብዮት ሀይል መሆናቸውን አሳወቁ ። እርግጠኛ ዘውደኞች የዛሩ ቀኪላካዮች የሚያስመስሉ ተግባሮችን መፈጸም ጀመሩ ። በ1909 ዓ.ም. የሕገመንግስታዊ-ዲሞክራቶች ቡድን ሺክሂ (ወሰን) በሚል ርእስ አንድ ቅጽ ጽሁፍ ጽፈው አቶሙ ። ይህ ጽሁፍ ለቡርዧው ፍላጐት ሲባል የዛሩ አገዛዝ አብዮቱን በማውደሙ ታላቅ ምስጋና እያቀረቡ ሕገ መንግስታዊ ዲሞክራቶች በጽሁፋቸው ውስጥ «በሰይፉና በወህኒ ቤቱ

ከሕዝብ አመጿዊ ቁጣ የሚጠብቀንን (ለዘብተኛ ቡርዧውን) መንግሥት ልናመሰግነው ይገባል» ሲሉ ጻፉ ።

ሁለተኛው መንግስታዊ ዱማ ከተበተነና በዱማው ውስጥ የሶሻል ዲሞክራሲ ቡድናች ሁኔታውን ካመቻቹ በኋላ የዛሩ አገዛዝ በታላቅ ስሜት የወዝአደሩን ፖለቲካዊና ምጣኔ ሀብታዊ ድርጅቶች ስለማጥፋት ጉዳይ አነሳ ። ምሽጎችና እስር ቤቶችን ያስጨንቁ አብዮታውያን እስረኞች ለፍርድ እንዲቀርቡ እጅግ አስከፊ በሆነ ሁኔታ ተደብድበዋል፣ተሰቃይ ተዋል ።የጽልመተ መቶዎችን ሽብር ለመቆጣጠር የሚቻል አልነበረም ። የዛሩ ሚኒስትር ስቶልፒን በመላው ሀገሪቷ የመስቀያ ቅስቶችን አዘጋጀ ። እጅግ ብዙ አብዮተኞች ተገደሉ ። በዚያን ወቅት እነዚህ የመስቀያ ቅስቶች በወቅቱ «የስቶልፒን ከረባቶች» ተብለው ይታወቁ ነበር ።

የገበሬውና የሠራተኛውን አብዮታዊ ንቅናቄ ለማፈን የዛሩ አገዛዝ በዚህ ዓይነቱ ጭቆና ላይ ብቻ ራሱን አልወሰነም ፡—ቅጣት ሰጪ ቡድኖችን በመላክ በመረሸን፣በማሰርና አስገድዶ በማሰራት ስቃዮች በማስጨነቅ ብዛት የገበሬዎችን የዋህ እምነት አጣ ። «ትንሹ አባት ዛሩ» መባሉ እያኰተመና እየራቀ ሄደ ።በገጠር ውስጥ በገጠር የቡርዧዎች ትልቅ ክፍል ማለትም በሐብታም ገበሬዎች ዘንድ ጠንካራ ድጋፍ ለማግኘት አሰበ ።

በኅዳር 9 ቀን 1906 ዓ.ም. ስቶልፒን ገበሬው የሕብረት እርሻዎችን በሙተው የተነጣጠሉ እርሻዎች እንዲጀምር የሚያስችል አዲስ የገጠር ሕግ አወጣ ። የስቶልፒን የገጠር ሕግ የሕብረት ባለቤትነትን ሥርዓት አፈራረሰ ። ገበሬዎች በመከፋፈል የደረሳቸውን ድርሻ እንደራሳቸው ንብረት እንዲወስዱ ተጋበዙና ከሕብረቱ እንዲለቁ ተደረገ ። አሁን ይህ ከሆነ በኋላ የራሳቸውን ድርሻ በፊት እንዲያደርጉ የማይፈቀድላቸውን አሁን እንደግል ንብረት መሸጥ እንዲችሉ ተደረገ ። እርሶ አደሩም ሕብረቱን ከለቀቀ በኋላ አንዲት የእርሻ አካባቢ እንዲወሰድ ተገደደ ።

አሁን ሀብታም ገበሬዎች ኩላኮች የደሀ ገበሬዎችን መሬት በርካሽ ዋጋ የመግዛት መልካም አጋጣሚ አገኙ ። አዋጁ ከታወጀ ከጥቂት አመታት በኋላ ከሚሊዮን በላይ የሚሆኑ ደሀ ገበሬዎች የራሳቸውን መሬት በአንድነት ለቀው ፍጹም ተዳከሙ ። ደሀ ገበሬዎች መሬታቸውን እንደለቀቁ አያሌ የሀብታም ገበሬዎች የእርሻ ይዞታ አደገ ። ይህ አንዳንድ ጊዜ የነርሱን ሙንጋ ጉልበት የሚቀጥር ቋሚ ይዞታ ሆነ ። መንግስቱ የሕብረቱን ምርጥ የእርሻ ቦታዎች ለሀብታም ገበሬዎች እንዲያስረክቡ አስገደዳቸው ።

በገበሬዎች «ነጻ መውጣት» ወቅት የራሳቸው የነበረውን የመሬት ከበርቴዎች መሬት ገበሬ ዎች ሲወስዱ አሁን ደግሞ ኩላኮች (ሀብታም ገበሬዎች) በሕብረት የተደራጀውን መሬታቸውን ጥሩውን የእርሻ ማሳ በመምረጥና ለገበሬዎች የተሰጣቸውንም ጭምር በርካሽ ዋጋ በመግዛት መዝረፍ ጀመሩ ። የዛሩ አገዛዝ ከደሀ ገበሬዎች ላይ መሬት እንዲገ



ዙና እርሻውን እንዲያደራጁ ለኩላኮች ከፍተኛ የገንዘብ ብድር ማበደሩን ተያያዘው ። ስቶልፒን የመሬት ከበርቴዎችን ወደ ትናንሽ የመሬት ከበርቴዎች በመለወጥ የዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ታማኝ ተከራካሪ ሊያደርጋቸው ፈለገ ።

ከ1906—15 ዓ.ም. ባሉት ዘጠኝ ዓመታት ብቻ ከሁለት ሚሊዮን የሚበልጡ ቤተሰቦች ሕብረቱን ለቀቁ ።

በስቶልፒን መመሪያ ምክንያት በገበሬዎችና ትናንሽ መሬት ተሸንሽኖ በተሰጣቸው እንዲሁም በደሀ ገበሬዎች መሀከል ያለው ሁኔታ እጅግ መጥፎ እየሆነ ሄደ ። በገበሬዎች መሀከል ያለው ልዩነት ይበልጥ ጉላ ። ገበሬዎቹ ከኩላክ አራሾች ጋር ግጭት መፍጠር ጀመሩ ።

ከዚሁ ጋር የዛሩ አገዛዝና መንግስታዊ ዱማው እንዲሁም ሕገመንግሥታዊ ዲሞክራቶች እስካሉ ድረስ ገበሬዎች የመሬት ባለቤትነትን ፍጹም ማግኘት እንደማይችሉ መገንዘብ ጀመሩ ።

የኩላኮች (ሀብታም ገበሬዎች) የእርሻ ይዞታ በታላቅ ደረጃ በተመሰረተበት ወቅት (1907-09) ዓ.ም. የገበሬዎች ንቅናቄ ማሽቆልቆሉን ጀመረ ። ይሁን እንጂ ወዲያውኑ በ1910-1911 ዓ.ም ፤ እንዲሁም በኋላ ፣ በመንደር ሕብረቱ አባሎችና ሐብታም አራሾች መሀከል በተነሳው ግጭት ሳቢያ የመሬት ከበርቴዎችንና የኩላክ አራሾችን በመቃወም የሚደረገው የገበሬው ንቅናቄ በታላቅ ሁኔታ አደገ ።

ከአብዮቱ በኋላ በኢንዱስትሪውም መስክ ቢሆን እንዲሁ ትልቅ ለውጦች ነበሩ ። ትላልቅ ድርጅቶችና ማእከላዊ የሆኑ ኢንዱስትሪዎች በተፋጠነ ሁኔታ በማደግ ላይ ባሉት ጠንካራ የካፒታሊስት ቡድኖች እጅ ገቡ ። ከ1905 ዓ.ም. አብዮት በፊት እንኳን ቢሆን ካፒታሊስቶች ድርጅቶችን በማቋቋም በሀገሪቷ ውስጥ ዋጋ በማናርና ከዚህም በሚያገኙት ግዙፍ የሆነ ትርፍ የውጪ ገበያውን በመገፋፋት እቃዎችን ውጪ በመሸጥ የውጪውን ገበያ በቁጥጥራቸው ሥር ለማድረግ ይጥሩ ነበር ። እነዚህ የካፒታሊስት ማህበሮች (ሞኖፖሊዎች) ትረስቶችና ሲንዲኪቶች ተብለው ይጠራሉ ። ከአብዮቱ በኋላ ቁጥራቸው እየጨመረ በመሄድ ላይ ነበር ። እንዲሁም በኢንዱስትሪው መስክ ታላቅ ሚና የሚጫወቱት ትላልቅ ባንኮችም ቁጥራቸው እየጨመረ መጣ ። የባእዳን ካፒታል ወደ ሩሲያ ውስጥ የመግባት ደረጃው በጣም ጨመረ ።

ስለሆነም በሩሲያ ውስጥ ካፒታሊዝም በእድገት ደረጃው ወደ ሞኖፖሊ ካፒታሊዝም ፣ ኢምፔሪያሊስት ካፒታሊዝም ተቀየረ ።

ለብዙ ዓመታት ባለበት ሲረግጥ የነበረው ኢንዱስትሪ አሁን ማንሠራራት ጀመረ ። የድንጋይ ከሰል የብረትና የነዳጅ እንዲሁም የጨርቃጨርቅ የስኳር ምርቶች ጨመሩ ። ትልቁን ደረጃ ይዞ ወደውጪ ይላክ የነበረው እህል ነበር ማለት ይቻላል ።

ምንም እንኳን ሩሲያ በዚያን ወቅት ጥቂት የኢንዱስትሪ ዕድገት
ብታሳይም ፣ ከምዕራብ አውሮፓ ጋር ስትነጻጸር አሁንም ገና ኋላ ቀርና
በባዕዳን ካፒታሊስቶች ላይ ጥገኛ ነበረች ። ሩሲያ መኪናዎችንና የመኪና
መሣሪያዎችን አታመርትም—ከውጪ ነበር የምታስመጣው ። የአውቶሞ
ቢል ኢንዱስትሪ ወይም የቅመማ ቅመም ኢንዱስትሪ የላትም ። ሰው
ሰራሽ ማዳበሪያዎችን አታመርትም ። በጦር መሣሪያዎች የማምረት ተግ
ባርም እንዲሁ ከሌሎች የካፒታሊስት አገሮች ወደ ኋላ የቀረች ነበረች ።

በሩሲያ ውስጥ የብረታ ብረት ፍጆታ ዝቅተኛነት የሀገሪቷን ኋላቀ
ርነት የሚያመለክት መሆኑን በመጠቆም ሌኒን ሲጽፍ ፡—

«የገበሬዎችን ነጻ መውጣት ተከትሎ ባለው ግማሽ ምእተ ዓመት በሩ
ሲያ ውስጥ የብረታ ብረት ፍጆታ በአምስት እጥፍ ጨምሮ ነበር ። ይህም
ቢሆን ገና ሩሲያ ከዚህ በፊት ታይቶ በማይታወቅ ድህነት የላሸቀች ፣
ከፊል አረማዊ ኋላቀር አገር ብትሆንም የእንግሊዝ አንድ አራተኛ ፣ የጀር
መንን አንድ አምስተኛና የአሜሪካንን አንድ አስረኛ ሊሆን በሚችል
ዘመናዊ የምርት ውጤቶች የተሞላች ነበረች»
(ሌኒን ስብስብ ሥራዎች የሩሲያ እትም ፣ ቅጽ 16 ፣ ገጽ 543)

የሩሲያ በምጣኔ-ሀብትና በፖለቲካ ኋላቀርነት አንደኛውና ቀጥተኛው
ውጤት የሩሲያ ካፒታሊዝምና ዛሩ እራሱ በምእራብ አውሮፓ ካፒታሊ
ዝም ላይ ጥገኛ የመሆኑ ነበር ።

ይህ ደግሞ እጅግ ጠቃሚ የሆኑ የኢንዱስትሪ ቅርንጫፎች ማለትም
እንደ ድንጋይ ከሰል ነዳጅና ኤሌክትሪካዊ መሣሪያዎች እንዲሁም ብረ
ትን ከጥሬ ማእድኑ አንጥሮ የማውጣት ጥበቦች ሁሉ በባእዳን ካፒታሊስ
ቶች እጅ እንዲሆኑ በመደረጉ ይገለጻል ። እንዲሁም ዛራዊት ሩሲያ መላ
ውን የኢንዱስትሪ መሣሪያዎችን ማለት ይቻላል ከውጪ አገር ማስመጣት
ነበረባት ።

እንዲሁም በባእዳን የብድር እግረ ሙቅ መጠፈራቸው በዚሁ የሚ
ገለጥ ነው ። የብድሩን ወለድ ለመክፈል የዛሩ አገዛዝ ከመቶ ሚሊዮን የበ
ለጠ ሩብል ከሕዝቡ የዓመት ገቢ ላይ ይገፋል ።

በተጨማሪም የዛሩ መንግስት ምስጢራዊ ስምምነቶችን ከሩሲያ
«ተባባሪዎች» ጋር በማድረግ በጦርነት ወቅት በሚሊዮን የሚቆጠሩ
የሩሲያ ወታደሮችን «ለተባባሪዎቿ» ድጋፍ ለመስጠት ወደ ኢምፔሪያ
ሊስት አገሮች በመላኩ ሲገለጽ ፤ ይህም የእንግሊዝና የፈረንሳይ ካፒታ
ሊስቶችን የተትረፈረፈ ትርፍ ለመንከባከብ ያደረገውን ጥረት ያሳየናል ።

የስቶልፒን የአድሀሮት ወቅት በተለይም የሚታወቀው የደም ሱሰ
ኞቹ ገዳዮችና ፣ ፖሊሶች የዛሩ ሰላዮችና ሰው—በላዎቹ ጽልመተ መቶ
ዎች በሠራተኛው መደብ ላይ ያደረጉት አረመኔያዊ ፍጅት የተፈጸመበት



ወቅት በመሆኑ ነው ። ነገር ግን ሠራተኞችን በአሰቃየው በዛሩ ብቻ አይ
ደለም ይህ ወቅት ታሪክ ጥቁር መስመር ከሥሩ ያስመረበት ። ከዚሁ ጋር
ሲነጻጸር የማይተናነሰው በሠራተኛው መደብ ላይ የተወሰደው የማጥቃት
እርምጃም ጭምር ነበር ። አዎን ! የፋብሪካና የወፍጮ ባለንብረቶች ኢን
ዱስትሪያዊ እድገት በአሉበት በሚረግጡበት ወቅት ፣ እድገት ባላሳዩበት
ወቅትና የሥራ አጡ ቁጥር እጅግ ባሻቀበበት ወቅት የፋብሪካ ባለቤቶች
የሥራ እገዳ በማወጃቸውና በተለይም ቀደም ባሉት የሥራ ማቆም አድ
ማዎች ውስጥ የተሳተፉ በመደብ ንቃታቸው የተራመዱትን ሠራተኞች
የስም ዝርዝራቸውን ከጥቁር መዝገብ ውስጥ እየለቀሙ ከሥራ አሰናበቷ
ቸው ። እንደሚታወቀው አንዴ አንድ ሰው በዚያ ጥቁር መዝገብ ውስጥ
ስሙ ከሠፈረ የአምራቾች ድርጅት አባል በሆኑ በማናቸውም የኢንዱስ
ትሪ ቅርንጫፎች ውስጥ ባሉ የሥራ ቦታዎች ውስጥ ፍጹም መቀጠር
አይችልም ። በ1908 ዓ. ም. ከ10 እስከ 15 በመቶ የሚሆን የደሞዝ ቅነሣ
ሲደረግ ፣ የቀን የሥራ ሰዓት በሁሉም ቦታዎች ወደ 10 ወይም 12
ሰዓቶች ከፍ አለ ። ያ አሰቃቂ የመቀጫዎች ሥርዓት እንደገና ጀመረ ።

የ1905 ዓ. ም. አብዮት ሽንፈት የተንኘር መንገደኞችን (ፌሎ ትራቭ
ለርስ) መበታተንና ማዝቀጥ አስከተለ ። የማዝቀጡና የማሽቆልቆሉ ገዝን
ባሌ በተለይ በምሁራን አካባቢ እያደገ መምጣቱ በጉልህ የሚታይ ነበር ።
ከቡርዧው ቀዬ የወጡት ተንኘር መንገደኞች በአብዮቱ ወቅት ፓርቲው
ውስጥ ሊሳተፉ የተራወጡትን ያህል በአድሀሮቱ ወቅት ፓርቲውን ለመከ
ዳት የመጀመሪያዎቹ ሆኑ ። ጥቂቶቹ የአብዮቱ ግልጽ ጠላቶች ከሆኑት
ጋር ተቀላቀሉ ። ሌሎቹም ደግሞ ሕጋዊ መድረክ ይዘው በሚሰሩት የሠ
ራተኛው መደብ ማህበሮች ውስጥ ራሳቸውን መሽገው ከአብዮቱ ፈለግ
የሠራተኞችን አቅጣጫ ለመለወጥ ከፍተኛ ጥረት በማድረግ የወዝአደ
ሩን አብዮታዊ ፓርቲ ዝቅ አድርገው አስገመቱ ። ተንኘር መንገደኞች አብ
ዮቱን በመክዳት ከዛሩ አገዛዝ ጋር በሰላም ለመኖር የአድሀሮትን መል
ካም ፈቃድ ለማግኘት ከፍተኛ ጥረት አደረጉ ።

የዛሩ አገዛዝ የአብዮቱን ሽንፈት በመጠቀም እጅግ ፈሪና ራስ
ወዳድ የሆኑትን የአብዮቱ ተንኘር መንገደኞች የራሱ ሰላዮች በማድረግ መለ
መላቸው ። እነዚህ ዝቅ ያሉ ከሀዲዎች አብዮቱን በመክዳትና ከውስጥ
ሆነው መሠለል በሚያስችላቸው በሠራተኛው መደብና ፓርቲ ድርጅ
ቶች ውስጥ እንዲሠርጉ በዛሪስቱ አክሀራና ተላኩ ።

የአድሀሮትን ማጥቃት በዚሁ መስኮች ብቻ አልተወሰነም ፤ እንዲ
ሁም በርእዮተ-ዓለሙ መስክ የማጥቃት ዘመቻ ተያያዘው ። ይህ ደግሞ
ማርክሲዝምን « በመተቸት » ና « ውድቅ በማድረግ » አብዮቱን በሚሽ
ሚጠጥና በማፌዝ ፣ ክዳትን በማመስገን ፤ «የግለሰብ አምልኮ » በሚል

ሽፋን ስር የሩካቤ ስጋ ብልግናን በማጉላት ዘመን አመጣሽ የጸሀፊዎች መንጋ ብቅ አሉ ።

በፍልስፍና አድማስ ውስጥ ማርክሲዝምን « የመተቸት » እና የመ ከለስ ጥረቶች ሄዱ ። እንዲሁም ሁሉም ዓይነት ሀይማኖታዊ አዝማሚ ያዎች በአስመሳይ ሳይንሳዊ ንድፈ-ሀሳቦች ተመሳስለው ቀረቡ ።

ማርክሲዝምን « መተቸት » ና መከለስ ዘመን አመጣሽ ተግባር ሆነ ። እነዚህ የተከበሩ ሰዎች ከተለያዩ ዓይነት ቀለሞቻቸው ሌላ የጋራ የሆነ አንድ ዓላማ ይከተላሉ ። ይህም ዓላማቸው የሰፊውን ሕዝብ አብ ዮታዊ አቅጣጫ መለወጥ ነበር ።

እነዚህ ራሳቸውን ማርክሲስት አርገው የሚገምቱ ነገር ግን ጠንካራ ማርክሳዊ አቋም ያልያዙ የፓርቲው ምሁራን ክፍሎች በውድቀትና በተ ጠራጣሪነት ውስጥ ተዘፈቁ ። ከነዚህም ውስጥ እንደነ ቦግዳኖቭ ፣ ባዘ ሮቭ ፣ ሉናቻርስኪይ በ1905 ዓ. ም. ከቦልሼቪኮች ጐን ቆመው የነበሩ ፤ ዮቀኪቪችና ባሌንቲኖቪ ፣ (ሜንሼቪክ) የመሰሉ ጸሀፊዎች ነበሩ ። በአ ንድ ጊዜ በማርክሲዝም ንድፈ-ሀሳብ የፍልስፍና መሠረተ ሀሳቦች ላይ ማለትም በዲያሌክቲካዊ ቁስ አካላዊነትና በታሪካዊ ሳይንስ ማርክሳዊ መመሪያዎች መሰረተ ሃሳብ ላይ ማለት በቁስአካላዊነት ላይ « ትችት » ከፈቱ ። ይህ የቀከፈተው ትችት በግልጽ የቀካሄደና ሀቀኛ ባለመሆኑ ከተለመደው ዓይነት የተለየ ነበር ። ይሁን እንጂ የማርክሲዝምን መሰረታዊ አቋም «ለመጠበቅ» በሚል ሽፋን ሥር አግቦና ግብዛዊነት በተሞላ መንገድ የቀካሄደ ሲሆን ፤ እነዚህ ሰዎች ማርክሲስቶች ነን በማለት የማርክሲዝ ምን አንዳንድ መሰረታዊ መመሪያዎች በማውጣት ማርክሲዝምን «እና ሻሽላለን » አሉ ። እንደ እውነቱ ከሆነ ግን እነዚህ ሰዎች የማርክሲዝም እውነተኛ ጠላቶች ነበሩ ። ምክንያቱም ምንም እንኳን የማርክሲዝም ጠላ ቶች መሆናቸውን ግብዝነት በተሞላበት መንገድ ቢክዱም የማርክሲዝ ምን ንድፈ-ሃሳባዊ መሰረቶቹን ዝቅ አድርገዋል ። አበው በሁለት ባላ ተስቀል አንዱ ሲሰበር በአንዱ ቀንጠልጠል እንዲሉ በሁለት ገፃቸው በመቀጠል ራሳቸውን ማርክሲስቶች አድርገው ያቀርባሉ ። ይህ ግብዛዊ ትችት አደገኝነት አለው ። አደጋው በፓርቲው መላ አባላት ላይ የታለመና ምናልባትም የሚያሳስት በመሆኑ ላይ ያረፈ ሲሆን ፤ የማርክሲዝም ንድፈ ሀሳባዊ መሰረቶችን ዝቅ በማድረግ ላይ የታለመው ይህ ግብዝነት የቀሞ ላው ትችት ይበልጥ እያደገ ሲመጣ ለፓርቲው ይበልጥ አደገኛ እየሆነ ይሄዳል ። ሌሎች የአድሀሮት ሀይሎች በማስተባበር በፓርቲው ላይ ይነ ሳል ። በአብዮቱ ላይ ያሳምጸል ። ማርክሲዝምን የካዱ አንዳንድ ምሁራን አዲስ ሃይማኖት (እነዚህ ሰዎች «ጣኦት አምላኪዎች» ና «ጣኦት አና ጮች» በመባል ይታወቃሉ) እስከ መስበክ ርቀው ሄደው ነበር ።



ከማርክሲዝም ንድፈ-ሀሳብ ለከዱት ለነዚህ ከሀዲዎች ተመጣጣኝ ምላሽ መስጠቱ ፤ የለበሱትን የሀሰት ካባ ከላያቸው ላይ በመግፈፍ ማንነ ታቸውን በማጋለጥ የማርክሲስት ፓርቲን ንድፈ—ሀሳባዊ መሰረት ከአደጋ መጠበቅ የማርክሲስቶች አጣዳፊ ተግባር እየሆነ መጣ ።

አንዳንዶቻችን ይህ ዓይነት ተግባር ራሳቸውን «የበቁ ማርክሲስት ንድፈ-ሀሳባውያን» አርገው በሚመለከቱ በፕሌክሀኖቭ የርሱ ጓደኞች ለሆ ኑት ሜንሼቪኮች የተከናወነ ተግባር ነው እንል ይሆናል ፤ ነገር ግን እነርሱ ከጋዜጣ ዓይነት ውስጥ ከግምት የማይገቡ አሳሳቢ ማስታወሻዎችን ለመ ጣልና መስኩን ለመተው መረጡ ።

ሌኒን ነበር በ1909 ዓ.ም. ታትሞ በወጣው «ቁስ አካላዊነትና ቤተ-ሙከራዊ» በተሰኘው ጽሁፍ ይህን ተግባር ያከናወነው ።

«ግማሽ ዓመት ባልሆነ ጊዜ ውስጥ» ይላል ሌኒን ሲጽፍ «በዲያሌ ክቲካዊ ቁስ አካልነት ላይ ለተደረጉት የማጥቃት ዘመቻዎች አራት መጽሀፍት ተጻፉ ። እነዚህም የማርክሲዝም ፍልስፍና ማጥናት ፤ (የርሱ «ተቃዋሚ» ብሎ መጥራቱ ይሻላል) የተሰኘ የተጠራቀሙ ሥራዎችን የያዘ መጽሐፍ (ቅዱስ ፒተርስበርግ ፣ 1908 ዓ.ም.) በባዛሮቭ በቦግዳኖቭ ፣ በሉናቻርስኪይ ፣ በበረማን ፣ ቦሂልኖርድ ፣ በዩሽኬቪችና በሱቮሮቭ ተዘ ጋጅቶ የወጣውን ፣ የዩሽኬቪች ቁስ አካላዊነትና ወሳኝ ዕውነታ ፤ የበር ማንን ዲያሌክቲክስ በዘመናዊ የእውቀት ንድፈ-ሀሳብ መነጽር ሲታይ የቫሌንቲኖቭና የማርክሲዝም ፍልስፍናዊ ግንባታ የተባሉ መጻሕፍትን ጠቅለው ይይዛሉ ። እነዚህ ሁሉ ሰዎች አመለካከታቸውን በሰላም መንገድ ከመለወጡ በቀር ለዲያሌክቲካዊ ቁስአካላዊነት ባላቸው ጠላትነት የተንሳ አንድነትን መስርተዋል ። ከዚህም ጋር የፍልስፍና ማርክሲስቶች ነን ሲሉ የኤንግልስ ዲያሌክቲክስ 'ተአምራዊነት' ነው በማለት በርማን ተናገረ ። ልክ ራሱን በራሱ እንደሚገልጽ እውነት ሁሉ የኤንግልስን አስ ተሳሰብ «ጊዜው ያለፈበት» ነው ሲል በዘሮቭ ተናገረ ። ቁስ አካላዊነት ስለ «እውቀት ዘመናዊ ንድፈ-ሀሳብ» ስለ«ወቅቱ ፍልስፍና» (ወይም የወቅቱ አሸታዊነት—ፖስቲቪዝም) «ስለዘመናዊ የተፈጥሮ ሳይንስ» ወይም እንዲያውም ስለ ሃያኛው ክፍል ዘመን የተፈጥሮ ሳይንስ «በሙሉ ልባቸው በሚያወሱት በኛ ቆራጥ ጦረኞቻችን የተጠላና የተነቀፈ ሆነ ።»

(ሌኒን ቁስ አካላዊነትና ተግባራዊ ትችት ፤ እንግሊዝኛ እትም ፤ ሞስኮ 1947 ዓ ም ገጽ 9)

በጓደኞቹ ምክንያት — የፍልስፍና ከላሾች ናቸው «ምናልባት በስ ሀተት ውስጥ ገብተን ይሆናል ነገር ግን አሁንም በመጣር ላይ እንገኛለን» ሲል ሉናቻርስኪይ ለተናገረው ምላሽ ሲሰጥ ሌኒን እንደሚከተለው ጽፎ አል ።

«እንደ እኔ ከሆነ ለፍልስፍና «ከሚጥሩት» ውስጥ አንዱ ነኝ ። ለማንሳት ያሀል በሰጡሁት ትችት ላይ (ማለትም ቁስ አካላዊነትና

ቤተ-ሙከራዊ ትችት—ተርጓሚው) ራሴን እንዳተኩር ማድረጌ በማርክሲዝም ሸፋን ሥር የተምታቱ ፤ የተወናበዱና እድሀሪ የሆኑ አንዳንድ ነገሮችን የሚያራምዱ ሰዎች እንቅፋት የሆናቸው ምን እንደነበረ ለማወቅ ነው»

(ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ፤ ገጽ ፤ 10)

ነገር ግን እንደ እውነቱ ከሆነ የሌኒን መጽሀፍ ከዚህ መጠነኛ ተግባር በስቲያ ርቆ የሚሄድ ነበር ። መጽሀፉ በግዳናቸ ዩሺኬቪች ፣ ባዙሮቸና ባሌንቲኖቸ እንዲሁም የፍልስፍና መምህሮቻቸውን ማለትም ማርክሳዊ ቁስ አካላዊነትን በመቃወም የጠራና ግልጽ የሆነ ሀሳባዊነት በጽሁፋቸው ለማቅረብ የጣሩትን አሼናሪየስንና ማችን ከመተቸት የላቀ አንድ ነገር ነበር ። በዚሁ አኳያ ይህ መጽሀፍ የማርክሲዝምን ንድፈ-ሀሳባዊ መሠረት ዲያሊክቲካዊነትና ታሪካዊ ቁስአካላዊነት የሚንከባከብና ከኤንግልስ ሞት ጀምሮ ቁስአካላዊና ቤተ-ሙከራዊ ትችት የተሰኘው የሌኒን መጽሀፍ እስ ከታየበት ጊዜ ድረስ ፣ በአጠቃላይ ታሪካዊ የጊዜ ፈለግ ውስጥ ሳይንስ በተለይም የተፈጥሮ ሳይንስ ያገኛቸውን አቢይና አስፈላጊ የሆኑ ነገሮች ሁሉ ቁስ አካላዊ በሆነ መንገድ የሚያጠቃልል ነው ።

በዚህ መጽሀፍ ውስጥ በሚገባ የተተቹት የሩስያ ተግባራዊ ተቺዎችና የባህር ማዶው መምህሮቻቸው ሲሆኑ ፤ ሌኒን ፍልስፍናዊና ንድፈ-ሀሳባዊ ከላሾችን አስመልክቶ እንደሚከተለው ይደመድማል ።

1. « ከመቼውም ጊዜ ይልቅ የረቀቀ ማርክሲዝምን ሀሳባዊ ማድረግ ፣ ከመቼውም ጊዜ ይልቅ በማርክሲዝም ሸፋን ስር የረቀቀ ጸረ-ቁስአካላዊነት አስተምሮ ማቅረብ በፖለቲካዊ ምጣኔ-ሀብት ፣ በታክቲካዊ ጥያቄዎች ላይና በፍልስፍና በአጠቃላይ ይህ የዘመናዊ ከላሾች ባህሪያዊ ገጾታቸው ነው »

(ከላይ በተጠቀሰው መጽሐፍ ገጽ 342—43)

2—« የማኸና የአቬናሪያስ መላው ትምህርት ቤቶች ወደ ሀሳባዊነት አቅጣጫ በመጓዝ ላይ ናቸው »

(በዚህ መጽሐፍ ገጽ 370)

3. « የኛ ማችያውን (የማች ተከታዮች ተርጓሚው) በሙሉ በሀሳባዊነት ወጥመድ ውስጥ ተጠምደዋል ። »

(በዚህ መጽሐፍ ገጽ 359)

4. «በቤተ-ሙከራው ትችት ልማዳዊ የእውቀት ጥናት (ኢፒስቲማሎጂካል ስኮላስቲሲዝም) በስተጀርባ በመጨረሻው ትንተና እንደተንጸባረቀው በዘመናዊ ህብረተሰብ ውስጥ የተጻራሪ መደቦች አዝማሚያና ርእዮተ-ዓለም ትግል በፍልስፍናው መስክ በፓርቲዎች የተደረገውን ትግል ማየት ይቻላል »

(በዚህ መጽሐፍ ገጽ 371)



5. « ተጨባጭ የተግባራዊ ትችት መደባዊ ሚና በጥልቀት ያተኮረው ቁስአካላዊነትን በተናጠል በመቃወም በሚያደርጉት ውስጥ ለፊዳሊስቶች (ከሳይንስ በላይ የሚያመልኩ አድሀሪያን —ተርጓሚው)እምነት የተሞላበት አገልግሎት ለመስጠት ነው።

(በዚህ መጽሐፍ ገጽ 371)

6. « ፍልስፍናዊ ሀሳባዊነት . . . ወደ ቤተ ክርስቲያን ደብር የሚወስድ ጭፍን ጉዳና ነው ።

(የሌኒን ስብስብ ሥራዎች ሩስያ እትም ቅጽ 13 ገጽ 304)

በፓርቲያችን ታሪክ ውስጥ የሌኒን መጽሐፍ የተጫወተውን ታላቅ ሚና ለማድነቅና ሌኒን ከተለያዩ መንጋ ከላሾችና ከስልፒና የአድሀሮት ወቅት ከዳተኞች በመከላከል ያቆየውን ንድፈ-ሀሳባዊ ቅርስ ለማረጋገጥ በጣም አጭር በሆነው በዲያሌክቲካዊና ታሪካዊ ቁስ አካላዊነት ገለጻ ላይ እናተኩራለን ።

ይህ ሁሉ እጅግ አስፈላጊ ነው ። ምክንያቱም ዲያሌክቲካዊና ታሪካዊ ቁስአካላዊነት የኮሚኒዝም ንድፈ-ሀሳባዊ ምንጭ የማርክሳዊ ፓርቲ ንድፈ-ሀሳባዊ መሠረት የሚገዛ ነውና መላው ንቁ የፓርቲ አባሎቻችን እነዚህን መመሪያዎች ጠንቅቀው ማወቅ ተግባራቸው ነውና ያጠናሉ ።

ታዲያ ፤

1. ዲያሌክቲካዊ ቁስ አካላዊነት ምንድን ነው ?
2. ታሪካዊ ቁስ አካላዊነት ምንድን ነው ?

## 2. ዲያሌክቲካዊና ታሪካዊ ቁስ አካላዊነት ፤

ዲያሌክታካዊ ቁስ አካልነት የማርክሲስት ሌኒኒስት ፓርቲ ርእዮተ ዓለም ነው ። ዲያሌክቲካዊ ቁስ አካልነት የተባለበትም ምክንያት የተፈጥሮን ክስተቶች የሚመረምርበት ፣ እነዚህንም ክስተቶች የሚረዳበት ዘዴ ዲያሌክቲካዊ በመሆኑ ሲሆን እነዚህን የተፈጥሮ ክስተቶች የሚተረጉምበት ፣ የሚገነዘብበት የሚያስተነትንበት ንድፈ—ሐሳቡ ፣ ቁስ አካላዊ ስለሆነ ነው ። ታሪካዊ ቁስ አካልነት ደግሞ ፤ የዲያሌክቲካዊ ቁስ አካልነት መርሆዎች ለሕብረተሰብ ምርምር እንዲያገለግሉ ሆነው ሲተረጎሙ ነው ፤ የዲያሌክቲካዊ ቁስ አካልነት መርሆዎች የሕብረተሰብን የኑሮ ክስተቶች ሕብረተሰብና ታሪኩንም ለመመርመር ለማጥናት ሲውሉ ታሪካዊ ቁስአካልነት ይሻሉ ።

ማርክስና ኤንግልስ ስለዲያሌኬቲካዊ ዘዴያቸው በሚያትቱበት ጊዜ ብዙ ጊዜ ሄገልን በመጥቀስ የዲያሌክቲክስን ዋና ዋና መለዮዎች የቀመረው ፈላስፋ እሱ መሆኑን ይናገራሉ ። እንዲህ መባሉ ግን የማርክስና የኤንግልስ ዲያሌክቲክስ ከሄግል ዲያሌክቲክስ ጋር መሳ ለመሳ የሚገጥም ፍጹም አንድ ነው ማለት አይደለም ። እንዲያውም ማርክስና ኤንግልስ

የሄግልን ዲያሌክቲክስ መርምረው ከውስጡ ይበጃል ብለው የወሰዱለትና የተቀበሉት « ምርመራዊ ዘይቤውን » ሲሆን ተላብሶት የነበረውን ሐሳባዊ ማህደሩን አውልቀው ወዲያ በመጣል የዲያሌክቲክስን እድገት ወደፊት አራምደው ዘመናዊውን ሳይንሳዊ መልክ አሲዘውታል ።

ማርክስ በዚሁ ረገድ የሚከተለውን ይለናል ፤ « የኔ ዲያሌክቲካዊ ዘዴ ከሄግል ዲያሌክቲካዊ ዘዴ በሥረ መሠረቱ የተለየ ብቻ ሳይሆን ፤ እንዲያውም ፍጹም ተቃራኒው ነው ። ሄግል ቢሆን ፣ የአስተሳሰብን ሂደት « ኃልዩ » የሚል ስያሜ ከሰጠው በኋላ ራሱን የቻለ ከምንም ነገር ነጻ የሆነ ባለቤት አድርጐ በመመልከት የተጨባጭ ዓለም ፈጣሪ አምላክ መሆኑን ተጨባጩ ዓለም ደግሞ በፈንታው የዚህ የ « ኀልዩ » መከሰቻ የሚሆን አፍአዊ ገጽ መሆኑን ያቀነቅናል ። በዚህ አንጻር ግን እኔ እንደ ማቀንቅነው ከሆነ ሐሳባዊው ተጨባጭ ዓለም በሰው ልቦና ተቀርጾ የሐሳብ ጽንስ መሆኑን እንጂ ሌላ የሚያመለክተው ነገር የለም ። »
(ካርል ማርክስ ካፒታል ቅጽ 1 ፣ ገጽ 30 ፣ ጆርጅ አለን እና ዩንዊን ሊሚትድ ፣ 1938)

ማርክስና ኤንግልስ ቁስ አካላዊ አስተሳሰባቸውን በሚያትቱበት ጊዜ ብዙውን ጊዜ ፌወርባኽን በመጥቀስ ቁስ አካልነትን ተገቢውን ሥፍራ መልሶ እንዲይዝ ያደረገው ፈላስፋ እሱ መሆኑን ይናገራሉ ። እንዲህ መባሉ ግን የማርክስና የኤንግልስ ቁስ አካላዊ ሥልት ከፌወርባኽ ቁስ አካላዊ ሥልት ጋር መሳ ለመሳ የሚገጥም ፍጹም አንድ ነው ማለት አይደለም ። እንዲያውም ማርክስና ኤንግልስ የፌወርባኽን ቁስ አካላዊ ሥልት መርምረው ከውስጡ የወሰዱለት ፣ የተቀበሉት « ፍሬ ነገሩን » ብቻ ነው በተቀረ ግን ተላብሶት የነበረውን ሐሳባዊና ሀይማኖታዊ ሥነ ምግባራዊ ኩተቱን ወዲያ ገፈው በመጣል ሳይንሳዊ ወደሚሆን የቁስአካልነት የፍልስፍና ንድፈ-ሐሳብ ደረጃ ከፍ አድርገውታል ። ፌወርባኽ ምንም እንኳን በመሠረቱ የቁስ አካልነትን ፍልስፍና የሚያበክር ቢሆንም ፤ ቁስ አካልነት የሚለውን ስያሜ እንደማይቀበል እናውቃለን ። ኤንግልስም ካንዴም ሁለት ሶስቴ እንዲህ ሲል ያስታውቀናል « ምንም እንኳ የፍልስፍናው መሠረት ቁስ አካላዊ ቢሆንም ፤ ፌወርባኽ የዘመናት ቅርስ ባወረሰው የሐሳባዊነት ቁራኛ እንደተያዘ ነው ። » ደግሞም እንዲህ ይለናል ኤንግልስ « የፌወርባኽ ሐሳባዊነት ባንዳፍታ ግልጽ የሚሆንልን ፣ ስለ ሀይማኖትና ስለሥነ ምግባር የሚያበክረውን ፍልስፍና ስንመለከት ነው» ።
(ፍሬድሪክ ኤንግልስ ፣ ሉድዊንግ ፌወርባኽ ፤)

ዲያሌክቲክስ የሚለው ቃል መሠረቱ ዲያሎጐ የሚለው የጽርእ ቃል ነው ፣ ትርጉሙም በጥሬው መወያየት መከራከር ማለት ነው ። በጥንት ዘመን ሰዎች ክርክር ሲገጥሙ ፣ ከባላንጣ የሚሰነዘረው ሐሳብ ያዘላቸውን ቅራኔዎች እያጋለጡ እያፍታቱ ቅራኔዎችን በማስወገድ እውነቱን



ለመጨበጥ የሚጠቀሙበት ጥበብ ዲያሌክቲክስ ነበር ። አንድ ሀሳብ የሚይዛቸው ቅራኔዎችን ማጋለጥና ተጻራሪ አስተያየቶችን እያጋለጡ ማብላላት ነው ብለው የሚያምኑ ፈላስፎች በጥንት ዘመን ኖረው አልፈዋል ። ታዲያም ፣ ለሃሳብ ምርምር ብቻ ይውል የነበረው ይህ ዲያሌክቲካዊ ዘዴ ከጊዜ በኋላ የተፈጥሮ ክስተቶችን ለመመርመር እንዲበጅ ሆኖ በመስፋፋት ተፈጥሮን ለመረዳት የሚያስችል ዲያሌክቲካዊ ዘዴ ወደሚሆንበት ደረጃ ከፍ እንዲል ሆነ ፣ በዚህም ዘዴ መሠረት የተፈጥሮ ክስተቶች ያለማቋረጥ የሚንቀሳቀሱ ፣ ያለማቋረጥ የሚለዋወጡ መሆናቸውን የተፈጥሮ እድገት በውስጡ ባሉት ቅራኔዎች መጐልመስ ምክንያት ፣ ማለትም በውስጡ ባሉ ተጻራሪ ኃይሎች የርስ በርስ ግጭት የሚከናወን መሆኑን እንገነዘባለን ።

ዲያሌክቲክስ በመሠረቱ የሜታፊዚክስ ቀጥተኛ ተቃራኒ ነው ።

1/ የማርክሲስት ዲያሌክቲካዊ ዘዴ ዋና ዋና የሚባሉት መለዮዎቹ የሚከተሉት ናቸው ።

ሀ/ ዲያሌክቲክስ ከሜታፊዚክስ ጋር ተጻራሪ እንደ መሆኑ መጠን ተፈጥሮን የሚመለከታት እንዲያው በዘፈቀደ የተጠራቀሙ እርስ በርሳቸው ያልተያያዙና የተገነጣጠሉ ሁሉም በየፊናቸው ራሳቸውን ችለው ሌጣቸውን የቆሙ ነባራዊ ነገሮች ወይም ክስተቶች ክምችት አድርጐ አይደለም ፤ በሜታፊዚክስ አንጻር ዲያሌክቲክስ ተፈጥሮን ሲመለከት እነዚህን ነባራዊ ነገሮች ወይም ክስተቶች ተዋቅረው ፣ ተደጋግፈው ፣ ተቃቅፈው ተደጋግፈው ፣ ተካክበው ፣ አንዱ የሌላውን ሁኔታ እየወሰነ የሚገኙበት የተያያዘ አንድ ሙሉ አካል አድርጐ ነው ።

ስለዚህም በተፈጥሮ ውስጥ የሚገኝ ማንኛውም ዓይነት ክስተት ራሱን ችሎ ባካባቢው ከሚገኙ ሌሎች ክስተቶች ተገንጥሎ ሌጣውን ብቻ ቢመረመር ሊታወቅ እንደማይችል ዲያሌክቲክስ የሚያስተምረን ነገር ነው ፣ በማንኛውም የተፈጥሮ መስክ የሚገኝ ክስተትን ካካባቢው ሁኔታ ጋር ሳናገናዝብ ከሌላው ነጥለን እንዲሁ ሌጣውን ብቻ እናጢንህ ብንለው ትርጉም አልባ ይሆንብናልና ነው ፣ ነገሩን መልሰን በመልከስናየው ዲያሌክቲክስ ማንኛውም ክስተት ምንነቱ ሊረዳንና ሊገለጽልን የሚችለው ምንጊዜም ቢሆን ምንም ተገንጥሎ ሊታይ ከማይችልበትና የራሱንም ሁኔታ ከሚወስኑት የአካባቢው ክስተቶች ጋር አገናዝበን ስናጤነው ብቻ መሆኑን ነው የሚያጸድቅልን ።

ለ/ ዲያሌክቲክስ ከሜታፊዚክስ ጋር ተጻራሪ በመሆኑ መጠን ተፈጥሮን የሚመለከታት ጸጥ ያለና የማይንቀሳቀስ የረጋና የማይለወጥ ነገር አድርጐ አይደለም ። በሜታፊዚክስ አንጻር ዲያሌክቲክስ ተፈጥሮን የሚመለከታት ያለማቋረጥ የሚንቀሳቀስና የሚለዋወጥ ፣ ያለ ማቋረጥ የሚታደስና የሚጐለምስ በውስጡም ሁልጊዜ አንድ ነገር ተወልዶ የሚያድግበት ሌላ ነገር ደግሞ የሚፈርስበትና የሚጠፋበት ነገር አድርጐ ነው ።

ስለሆነም ክስተቶችን ስናጤን እርስ በርስ የተሳሰሩና የሚደጋገፉ መሆናቸውን ብቻ ሳይሆን የሚንቀሳቀሱ ፣ የሚለዋወጡ ፣ የሚጐለምሱ ፣ የሚወለዱና የሚጠፉ መሆናቸውንም ጭምር እንድናስተውል ዲያሌክቲካዊ ዘዴ ግድ ይለናል ።

ዲያሌክቲካዊ ዘዴ ከፍተኛ አድርጐ በቅድሚያ የሚመለከተው ባንድ በተወሰነ ወቅት ሲመለከቱት ለጊዜው ነዋሪ ዘላቂ መስሎ እየታየ ግና ደግሞ በማቆልቆል በመጥፋት ላይ ያለውን ሳይሆን ለጊዜው ሲያዩት ነዋሪ ዘላቂ መሆኑ ባይገለጽም ገና አቆጥቁጦ በመጐልመስ ላይ ያለውን ሁኔታ ነው ፤ ምክንያቱም ዲያሌክቲካዊነት የማይበገር ነው ብሎ የሚመለከተው ገና የሚያቆጠቁጠውን በመጐልመስ ላይ ያለውን ስለሆነ ነው ።

ኤንግልስ እንዲህ ሲል ጽፎአል ፡ « ተፈጥሮ በመላ ደቂቅ ከሚባለው ትንሽ ነገር ልሂቅ እስከሚባለው ትልቅ ነገር ድረስ ካንዲቷ የአሸዋ ቅንጣት እስከ ትልቂቱ ጸሐይ ከቀዳማዊ ህዋስ እስከ ታላቁ ሰው ድረስ ያለው ማንኛውም ነገር ወትሮ ያለማቋረጥ ህልው ይሆናል ፤ ተመልሶ ይጠፋል ፤ ያለማቋረጥ ያዘግማል ፣ ያለማቋረጥ ይንቀሳቀሳል ፣ ይለወጣልም ፤ ወትሮ የሚገኝበት ሁኔታ ይህ ነው » (ኤንግልስ ፣ የተፈጥሮ ዲያሌክቲክስ)

ስለዚህም ዲያሌክቲክስ ኤንግልስ እንደሚነግረን «ነባራዊ ነገሮችንና በአእምሮ የሚቀረጹ ምስሎቻቸውንም የሚመለከተው በባህሪያቸው ባላቸው መተሳሰር ፤ መጣመር ፤ በመንቀሳቀሳቸው ፤ ህልው በመሆናቸውና በመጥፋታቸው መሠረት ነው ። » (ኤንግልስ ፣ ፀረ-ዱሪንግ)

ሐ/ ከሜታፊዚክስ ጋር ተፃራሪ በመሆኑ መጠን ዲያሌክቲክስ እድገት እንደቀላል እንደስድ ሂደት የመጠን ለውጥ ምንም የዓይነት ለውጥ ሳያስከትል አካል በአካል ላይ ዝም ብሎ እንደሚነባበርበት ግዝፈት ብቻ የሚጨምርበት ተራ ሂደት አድርጐ አይመለከተውም ። በሜታፊዚክስ አንፃር በዲያሌክቲክስ እድገት ሲባል አንድ ነገር ይህ ነው ከማንለውና ጐልቶ ከማይታይ ተደራራቢ የመጠን ለውጥ ኋላ ጉልህ ሆኖ ወደሚከሰት መሠረታዊ ለውጥ—ወደ ዓይነት ለውጥ—ያመራል ማለት ነው ፤ በእድገት ሂደትም ውስጥ የዓይነት ለውጥ የሚያዘግም ሳይሆን በፍጥነትና በቅጽበት የሚሆን ካንድ ይዞታ ወደ ሌላ ዓይነት ይዞታ ሊሻገር በእመርታ መሆኑን ይህ የዓይነት ለውጥም እንዲያው ያጋጣሚ ፣ የዘፈቀደ ነገር ሳይሆን ጐልቶ የማይታይ የመጠን ለውጥ ተደራርቦ ተጠራቅሞ ባንድ ላይ ባንድ በተወሰነ ደረጃ የሚያስከትለው ውጤት መሆኑን ዲያሌክቲክስ ያጸድቅልናል ።

ስለዚህም ደግሞ ዲያሌክቲካዊ ዘዴ የእድገት ሂደት ሲባል አንድ ነገር ዞሮ ዞሮ ጥንት ከነበረበት የሚመለስበት አንዴ የተደረገው ያለፈው ልክ እንደነበረ የሚደጋገምበት ባለበት የሚረግጥበት ንቅናቄ ሳይሆን ፣



ሁልጊዜም ወደፊት ፣ ሁልጊዜም ወደ ከፍተኛ ደረጃ የሚጓዝበት እንቅስቃሴ አሮጌ ከሆነው ይዞታ አዲስ ወደሆነበት የዓይነት ይዞታ የሚሸጋገርበት ቀላል ወይም ነጠላ ከሆነ ሁኔታ ወደተወሳሰበ ሁኔታ የሚገባበት ከዝቅተኛው ወደ ከፍተኛው የሚራመድበት የለውጥ ሂደት መሆኑን ያስተምረናል ።

ኤንግልስ እንዲህ ይላል ፡ « ተፈጥሮ የዲያሌክቲክስ መፈተኛ ነው ፤ የዘመኑም የሥነ ተፈጥሮ ሳይንስ ለዚሁ መፈተኛ በየእለቱ እየጨመሩ የሚሄዱ አጥጋቢ መረጃዎችን ይዞልን ቀርቧል ፤ በዚህም መሠረት እነሆ የተፈጥሮ ሂደት ዲያሌክቲካዊ እንጂ ሜታፊዚካዊ አለመሆኑን ፣ ዘላለም ሳይለወጥ ከተነሳበት ቦታ ተመልሶ እዚያው የሚረግጥ ያለማቋረጥ በአንድ ክበብ ሲሽከረከር የሚኖር ሳይሆን ደንበኛ የእድገት ታሪክ ያለው መሆኑን አረጋግጦልናል ። እዚህ ላይ በቅድሚያ ሊጠቀስ የሚገባው ተፈጥሮን ሜታፊዚካዊ በሆነ መንገድ ይመለከት የነበረውን አስተሳሰብ ከሥረ-መሠረቱ ያናጋውና ይህ ዛሬ የምናየው ህያው ፍጥረት ሁሉ ማለትም እጽዋት እንስሳትና ሰውም ራሱ ሳይቀር ለእያሌ ሚሊዮን ዓመታት ሲካሄድ የኖረ የእድገት ሂደት ውጤት መሆኑን በማስረጃ ያረጋገጠልን ዳርዊን ነው ። (ኤንግልስ ፣ የተፈጥሮ ዲያሌክቲክስ)

ዲያሌክቲካዊ እድገት ከመጠን ለውጥ ወደ ዓይነት ለውጥ መሸጋገር መሆኑን በመግለጽ ኤንግልስ የሚከተለውን ይላል ፤

« በፊዚክስ . . . ማንኛውም ለውጥ ከመጠን ወደ ዓይነት የመሻገር ለውጥ ነው ፣ ይህም የሚሆነው አንድ አካል ወይም ባሕርይ ወይም በሌላ አካል ተጽእኖ በሚያደርገው እንቅስቃሴ የመጠን ለውጥ ሲያከናውን ነው ። ለምሳሌ አንድ የተወሰነ የሙቀት ደረጃ በውኃ የፈሳሽነት ባሕርይ ላይ ምንም ዓይነት ለውጥ አያመጣም ፣ ግን የውኃው የሙቀት ደረጃ ከፍ እያለ ወይም ዝቅ እያለ ሲሄድ የፈሳሹ ውኃ ውሁድና ተለውጦ እንደሙቀቱ መጨመር ውኃው ወደ እንፋሎትነት አለዚያም እንደሙቀቱ መቀነስ ወደበረዶነት የሚለወጥበት ቅጽበት ይመጣል . . . ። የፕላቲነም ሽቦ ብርሀን እንዲሰጥ ለማድረግ የተወሰነ የኤሌክትሪክ ኃይል ያስፈልጋል ፣ ማንኛውም ንጥረ ብረት የሚቀልጥበት የተወሰነ የሙቀት ደረጃ አለው ፣ ማንኛውም ፈሳሽ ነገር ቢሆን ባለን የመሣሪያ አቅም አስፈላጊውን ሙቀት እንዲያገኝ ማድረግ እስከቻልን ባንድ በተወሰነ የአየር ግፊት መጠን ቀዝቅዞ የሚጋገርበት ወይም ፈልቶ የሚተንበት ባሕርይን የሚመጥን የተወሰነ የሙቀት ደረጃ አለው ማንኛውም ዓይነት ተን የሚበቃውን ያህል ግፊትና ቅዝቃዜ እንዲያገኝ ከተደረገ ወደ ፈሳሽነት የሚለወጥበት የተወሰነ ደረጃ አለው . . . ። በፊዚክስ ውስጥ ነባሮች የሚባሉት ነገሮች ብዙውን ጊዜ የመጠን መጨመር ወይም መቀነስ ከአንድ ከተወሰነ ደረጃ ላይ ሲደርስ በአንድ አካል ላይ የዓይነት ለውጥ የሚያስከትልበትን ድንበር ወይም ቅጽበት የሚያመለክቱ ማለትም መጠን ወደ ዓይነት

የሚሻገርበትን ወሰን የሚጠቁሙ ነቁጦች ናቸው ። » (ይኸም እንደላይኛው) ወደ ኬሚስትሪ በመሻገር ደግሞ ፣ ኤንግልስ የሚከተለውን ይላል ፤

« ኬሚስትሪ ባንድ አካል ውስጥ በመጠን ይዞታው ላይ በሚደረግ ለውጥ ምክንያት የሚመጣውን የዓይነት ለውጥ የምናጠናበት ሳይንስ ነው ማለት ይቻላል ። ይኸን ሄግልም ተገንዝቦታል ። . . . ለምሳሌ ያህል ኦክስጂን የሚባለውን ተን እንውሰድ ፣ አንድ ሞሊኪዮል የተለመደውን ሁለት አቶም በመያዝ ፈንታ ሶስት አቶም ከያዘ ኦዞን ይሆናል ፣ ይህም አካል በሽታውም ሆነ በባሕርይ ከመደበኛው ኦክስጂን ፍጹም የተለየ ነው ። ደግሞም ኦክስጂን ከናይትሮጂን ወይም ከድኝ (ሰልፈር) ጋር በተለያዩ መጠን ሲዋሀድ የምናገኘው ውጤት በሁሉም በኩል ቢሆን ከሌላው ሁሉ ፍጹም የተለየ አካል መሆኑ ግልጽ ነው ። » (ይህም እንደላይኛው)

በመጨረሻም ያን ያህል ጠቃሚ ምርምር ያበረከተውን ሄግልን እንደዚያ ዘልፎ ግና ደግሞ በዚያው ብእሩ መልሶ ኢ ለባዊ ከሆነው ነገር ፍጥረት ለባዊ ወደ ሆነው ከግዑዝ ሕያው ወደ ሆነው የተደረገው ሽግግር ወደአዲስ ሁኔታ የተደረገ እመርታ ስለመሆኑ የቀመረውን መሠረተ ሐሳብ ከዚሁ ከሄግል ላይ የሰረቀውን ዱሪንግን በተቸበት ጊዜ ኤንግልስ እንዲህ ብሏል ፤

« ይህማ » (ዱሪንግ የጠቀሰውን) « በለውጥ ሂደት ውስጥ መጠን ብቻውን እያደገ ወይም እያነሰ ሂዶ በተወሰኑ ነቁጦች ወይም ምዕራፎች ላይ ሲደርስ የዓይነት እመርታን ማስከተሉን የሚጠቁመው የለውጥ ምጣኔና ነቁጥ የሚገለጽበት ሄግሊያዊው ቀመር ነው ፣ ለምሳሌ ውኃን ወስደን ስናሞቀው ወይም ስናቀዘቅዘው ውኃው ሞቆ የሚፈላበት ወይም በርዶ የሚጋገርበት ነቁጥ ግፊቱ መጠነኛ ሆኖ እስከቆየ ድረስ አዲስ አካል የሚፈጠርበት ብሎም መጠን ወደ ዓይነት የሚለወጥበት እመርታ እንደሚሆነው ሁሉ ማለት ነው ። » (ኤንግልስ ጸረ-ዱሪንግ)

መ/ ዲያሌክቲክስ ከሚታፊዚክስ ጋር ተጻራሪ በመሆኑ ውስጣዊ ቅራኔ የነባራዊ ነገሮችና ክስተቶች ሁሉ ቀዋሚ ባህርይ መሆኑን ይገልጻል ፤ እነዚህ ነገሮችና ክስተቶች ሁሉ አፍራሽና ገንቢ ገጾች ፤ ቀዳሚና ተከታይ ታሪክ ፤ በመጥፋት ላይ ያለና በመጐልመስ ላይ ያለ ነገር አላቸው ። በነዚህ ተጻራሪ ኃይሎች መሀል የሚካሄደው ትግል ባሮጌውና በአዲሱ ፤ በሞትና በልደት ፤ በመጥፋትና በመልማት ወይም በመጐልመስ ላይ ባሉ ነገሮች መሀል የሚካሄድ የውስጣዊ እድገት ሂደትና ከመጠን ወደ ዓይነት የሚደረገው ውስጣዊ ለውጥ የሚመነጭበት መሆኑን ያስተምረናል ።

ስለዚህም የዲያሌክቲክስ ዘዴ ከዝቅተኛ ወደ ከፍተኛ የእድገት ደረጃ የሚደረገው ለውጥ ክስተቶች በኅብር ወይም በስምረት የሚያደርጉት



ጉዞ ሳይሆን በነባራዊ ነገሮችና ክስቶች ውስጥ በሚገኙ ቅራኔዎች መፈታት ፤ በነዚህ ተጻራሪ ኃይሎች መሠረት ላይ በሚከናወን የተቃራኒ አዝማሚያዎች « ትግል » አማካይነት የሚካሄድ ሂደት መሆኑን ይገልጻል ።

ሌኒን እንዲህ ይላል ፣ « በትክክል ሲተረጐም ዲያሌክቲክስ ነባራዊ ነገሮች በባህሪያቸው ያለባቸውን ቅራኔ የምናጠናበት ዘዴ ነው ። » (ሌኒን የፍልስፍና ማስታወሻዎች)
ለጠቅ አድርጐም ፤

« እድገት ማለት የተጻራሪ ኃይሎች « ትግል » ነው »
(ሌኒን ቁስ አካላዊነትና ቤተ-ሙከራዊ ትችት)

ባጭሩ እንግዲህ የማርክሲስት ዲያሌክቲካዊ ዘዴ መለያ ባሕርዮች እነዚህ ናቸው ።

እንግዲህ የዲያሌክቲካዊ ዘዴ መርሆዎች ሕብረተሰብንና ታሪኩን ለማጥናት ምን ያህል አስፈላጊ እንደሆኑና ከፍተኛ ጠቀሜታ እንዳላቸው እነዚህ መሠረተ-ሐሳቦች የሕብረተሰብን ታሪክና የወዝአደሩን ፓርቲ ተግባሮች ለመመርመርና ለማጥናት አስፈላጊነታቸው የቱን ያህል እንደሆነ መገመቱ አያስቸግርም ።

በዓለም ላይ ሌጣቸውን በተናጠል የሚቆሙ ክስቶች የሉም ካልን ክስቶች በሙሉ እርስ በርስ የተሳሰሩና ተካካቢ ከሆኑ ፤ እንግዲያውስ በታሪክ ውስጥ ያለ ማንኛውንም የሕብረተሰብ ሥርዓት በማንኛውንም የሕብረተሰብ እንቅስቃሴ የምንገመግመውና የምንዳኘው ፤ ታሪክ ጸሐፊዎች ብዙውን ጊዜ ሲያደርጉት እንደቆዩት ከ« ዘላለማዊ ትርዕይት » ወይም በአእምሮ ከተጸነሰ ቅድመ-ሐሳብ አንጻር ሳይሆን ሥርዓቱ ወይም የሕብረተሰቡ እንቅስቃሴ ከመነጨባቸውና ከሥርዓቱ ወይም ከእንቅስቃሴው ጋር ተያይዘው ከሚገኙት ሁኔታዎች አንጻር ነው ።

አሁን ባለንበት ዘመንና ሁኔታ የባርነት ሥርዓት ብሎ ነገር ከሁኔታ ጋር የማይዛመድ የማይሰምር ቅጥ የለሽ ትርጉም አልባ ይሆናል ። በመፈራረስ ላይ በነበረው ጥንታዊ የጋርዮሽ ሥርዓት ዘመን ግን የባርነት ሥርዓት መኖሩ ከጊዜውና ከሁኔታው ጋር ግጥም የሆነ ልንቀበለው የምንችል ነገር ነው ፣ ምክንያቱም በጥንታዊው የጋርዮሽ ሥርዓት አንጻር በከፍተኛ የእድገት ደረጃ ላይ ይገኛልና ነው ።

የዛሩ አገዛዝና የቡርዧ ሕብረተሰብ በነበረበት ሁኔታ ለምሳሌ በ1905 ዓ/ ም በሩስያ ቡርዧ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ እንዲቋቋም ማለቱ ምክንያት ያለው ተገቢና አብዮታዊም የሆነ ጥያቄ ነበር ፣ ምክንያቱም በዚያን ጊዜ የቡርዧ ሪፓብሊክ መኖሩ ታሪክን ወደፊት አንድ ምዕራፍ የሚያራምድ ነገር ነበርና ነው ። ባሁኑ ወቅት ቢባል ግን ማለትም የሶቭየት ሕብረት ሶሻሊስት ሪፓብሊክ ተቋቁሞ በሚገኝበት ሁኔታ የቡ

ርዧ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ብሎ ነገር ጸረ-አብዮታዊ የሆነ ትርጉም አልባ ጥያቄ ይሆናል ፡ ምነው ቢባል ከሶቭየት ሪፓብሊክ እንጻር ሲታይ የቡርዧ ሪፓብሊክ ማለት ወደኋላ መጐተት አድሮ ቁልቁል ማለት ይሆ ናሊና ነው ።

ማንኛውም ነገር ባለበት ሁኔታ ጊዜና ቦታ የሚወሰን ነው ።

የሕብረተሰብ ክስተቶች እንዲህ ባለ ታሪካዊ እንጻር ካልታዩ በቀር የታሪክ ሳይንስ ሊኖረንና ሊዳብር አይችልም ፤ ምክንያቱም የታሪክ ሳይንስ ያጋጣሚ ነገሮች ጥርቅምና ቅጥ የለሽ ስህተቶች የታጐሩበት የኮተት ማጠራቀሚያ ከመሆን ሊድን የሚችለው እንዲህ ያለ አቀራረብ ሲኖረን ብቻ ነው ።

በተጨማሪም ዓለም በማያቋርጥ የእንቅስቃሴና የእድገት ሁኔታ ላይ የሚገኝ ከሆነ ያረጀው መሞቱ ፤ አዲሱ መወለዱ ደግሞ የእድገት ሕግ ከሆነ « የማይለወጥ » የሕብረተሰብ ሥርዓት ብሎ ነገር የግል ሀብትንና ብዝበዛን የሚያጸድቁ « ዘላለማዊ ብሂሎች (Principle) » ብሎ ነገር ሊኖር አይችልም ።

ስለሆነም የፊውዳሉ ሥርዓት በካፒታሊስቱ ሥርዓት እንደተተካ ሁሉ የካፒታሊስቱም ሥርዓት በሶሻሊስት ሥርዓት ይተካል ።

ስለሆነም ደግሞ አስተሳሰባችንን መቃኘት ያለብን ባሁኑ ወቅት አይለው ቢታዩም እንኳን እድገታቸው ባከተመው የሕብረተሰብ ክፍሎች እንጻር ሳይሆን በወቅቱ ገና ያየሉ ባይሆኑም እንኳን ለእንግዲሁ ታዳጊ በሆኑትና የወደፊት ተስፋ ባላቸው ክፍሎች እንጻር መሆን አለበት ።

ባለፈው ምእተ-ዓመት በ80ኛዎቹ ዓመታት በማርክሲስቶችና በናሮድኒኮች መሐል ትግል ይካሄድ በነበረበት ወቅት የሩስያ ወዝአደር በብዛቱ ከቁም ነገር የማይገባ በጣም አነስተኛው የሕብረተሰብ ክፍል ነበር ፤ በአንጻሩ አርሶ አደሩ አብዛኛው የሕብረተሰብ ክፍል ነበር ። ሆኖም ታዲያ ወዝአደሩ ለገናው በማደግ ላይ የነበረ መደብ ሲሆን አርሶ አደሩ ግን በመፈራረስ ላይ የነበረ መደብ ነው ። ታዲያ ወዝአደሩ ታዳጊ መደብ በመሆኑ ማርክሲስቶች አስተሳሰባቸውን የቃኙት በወዝአደሩ እንጻር ሆነ ። ይህንን በማድረጋቸው ደግሞ አልተሳሳቱም ፤ ምክንያቱም እንደምናውቀው ሁሉ ወዝአደሩ የኋላ ኋላ ይህ ነው ከማይባል አነስተኛ ኃይል ተነስቶ እነሆ ዛሬ የመጀመሪያውን ደረጃ የያዘ የታሪክና የፖለቲካ ኃይል ለመሆን በቅቷል ።

ስለዚህም በመመሪያችን ስህተት ከማድረግ እንጠነቀቅ ዘንድ የወደፊቱን እንጂ ወደኋላ መመልከት የለብንም ።

በተጨማሪም ፤ እያዘገመ የሚሄድ የመጠን ለውጥ ፈጣንና ቅጽበታዊ የዓይነት ለውጥ ማስከተሉ የእድገት ሕግ ከሆነ ጭቁን መደ



ቦች የሚያካሄዱት አብዮትም እንግዲያው ፤ ምክንያት ያለውና የማይቀር ክስተት መሆኑ ግልጽ ነው ።

ስለዚህም ከካፒታሊዝም ወደ ሶሻሊዝም የሚደረገው ሽግግርና የወዝ አደሩ መደብ ከካፒታሊዝም ቀንበር ነጻ የሚወጣበት ሁኔታ የሚፈጠረው በሚያዘግም ለውጥ ማለትም በጥገና ለውጥ ሳይሆን በካፒታሊስት ሥርዓት ላይ በሚመጣ የዓይነት ለውጥ በአብዮት አማካይነት ብቻ ነው ።

ስለሆነም በመመሪያችን በኩል ስህተት፤ከማድረግ እንድን ዘንድ አብዮታውያን እንጂ የጥገና ዘይቤ ተከታይ መሆን የለብንም ።

ደግሞም እድገት የሚካሄደው ውስጣዊ ቅራኔዎች ሲፍታቱ ተጻራሪ ኃይሎችም በነዚህ ቅራኔዎች ላይ ተመርኩዘው ቅራኔዎቹን ለመወጣት ለመፍታትና በሚያደርጉት የርስ በርስ ግጭት ነው ከተባለ ፤ የወዝአደሩ የመደብ ትግልም ምክንያት የተከተለ የማይቀር ክስተት መሆኑ ግልጽ ነው ።

ስለሆነም የካፒታሊስቱን ሥርዓት መሸፋፈን የለብንም ፡ እያፍታታን ማጋለጥ አለብን እንጂ ፡ የመደብ ትግሉንም መግታት የለብንም ፤ ከመጨረሻ ግቡ ማድረስ እንጂ ።

ስለዚህም ፤ በመመሪያችን በኩል ስሕተት እንዳናደርግ የማያወላውል ወዝአደራዊ የመደብ አቅጣጫ እንጂ በወዝአደሩና በቡርዧው መሀከል የጥቅም አንድነት መኖሩን የሚለፍፈውን የጥገና ዘይቤ « ካፒታሊዝም ራሱ ቀስ በቀስ እያደገ ሶሻሊዝም ይሆናል » የሚለውን የደላሎች መመሪያ መከተል የለብንም ።

እነሆ ማርክሲስት የሆነውን ዲያሌክቲካዊ ዘዴ ማኅበራዊ ኑሮን ፡ የሕብረተሰብን ታሪክ ስንመረምርበትና ስንተረጉምበት ይህን የመሰለ መልክ ይኖረዋል ።

ማርክሲስት ቁስ አካላዊ ፍልስፍና የሐሳባዊ ፍልስፍና ቀጥተኛ ተቃራኒ ነው ።

<u>2/ የማርክሲስት ቁስ አካላዊ ፍልስፍና ዋና ዋና የሚባሉት መለዮዎቹ የሚከተሉት ናቸው ፤</u>

ሀ/ ዓለምን « ፍጹም ሐሳብ » ፡ « ሁለንታዊ መንፈስ » ፡ « ኅሊና » የሚከሰትበት አድርጐ በሚተረጉመው ሐሳባዊነት እንጻር የማርክስ ቁስ አካላዊ ፍልስፍና ዓለም በመሠረተ ባሕርዩ <u>ቁስ አካላዊ</u> መሆኑን በዓለም ላይ ያሉት ኅልቆ መሳፍርት ክስተቶች በእንቅስቃሴ ላይ ያለ ቁስ አካልን በተለያየ መልክ ቀምረው የያዙ መሆናቸውን ዲያሌክቲካዊ ዘዴ እንዳጸደቀውም የክስተቶች ውስጣዊ ግንኙነትና የርስ በርስ መደጋገፍ ወይም

መካካብ በመንቀሳቀስ ላይ ያለ ቁስአካል የእድገት ሕግ መሆኑን ፤ ዓለምም የምታድገው በቁስ አካል እንቅስቃሴ ሕግጋት መሠረት እንጂ « የሁለንታዊ መንፈስ » ልዩ ግፊት የሚያሻት አለመሆኑን ያቀነቅናል ።

«ቁስ አካላዊ ርእዮተ-ዓለም » ይላል ኤንግልስ « ተፈጥሮን ያለምንም ማመንታት ፣ እንዳለ መገንዘብ ከማለት ሌላ የተለየ ትርጉም የለውም ።» (ሉድዊግ ፊወርባኽ የሚለው ጽሑፍ ሥራዎች)

« ይህ ሁለንታዊ የሆነው ዓለም ምንም ዓይነት አምላክ ወይም ማንም ሰው የፈጠረው ሳይሆን ፣ ሥርዓት ተከትሎ ቦግና እልም እያለ የኖረ ፣ አሁንም ያለ ወደፊትም የሚኖር ህያው ነበልባል ነው » የሚለውን ሐሳብ ሲያቀነቅን ኖሮ ስለአለፈው ጥንታዊ ፈላስፋ ስለሄራቅሊጦስ ቁስ አካላዊ ዐውደ-ሐሳብ እንሥቶ ሲተች ሌኒን «የዲያሌክቲካዊ ቁስአካልነትን ፊደለ ሐዋርያ ደህና አድርጐ ገልጾታል » ይላል ። (ሌኒን ፤ የፍልስፍና ማስታወሻዎች)

ለ/ በእርግጥ ሕልው የሆነው ልቡናችን ብቻ መሆኑንና ፣ ቁስአካላዊው ዓለም ፤ ግዝፈትና ተፈጥሮ ቢሉ ግን በልቡናችን በሕዋሳታዊ ስሜቶቻችን በሀሳባችንና በዐይነ ኅሊናችን ብቻ የሚገኙ መሆናቸውን በሚያጸድቀው ሀሳባዊነት አንጻር ማርክሲስት ቁስአካላዊ ፍልስፍና ፣ ቁስ አካል ፣ ተፈጥሮ ፣ ግዝፈት ፣ ይህ ሁሉ ከልቡናችን ውጭ ከልቡናችን ነጻ ሆኖ ራሱን ችሎ የሚገኝ ነባራዊ እውነት መሆኑን ፣ ብሎም ቁስ አካል የሕዋሳታዊ ስሜቶች ፣ የሐሳብ ፣ የልቡና ምንጭ እንደመሆኑ መጠን ቀዳማይ መሆኑን ፣ እንዲሁም ደግሞ ፣ ልቡና ፣ የቁስ አካል ፣ የግዝፈት ነጸብራቅ ወይም ምስል እንደመሆኑ ተከታይ መሆኑን ፣ አንድም ሐሳብ በእድገቱ ሂደት ከፍተኛ የፍጹምነት ደረጃ የተቀዳጀ ቁስ አካል ማለትም የአንጎል ውጤት መሆኑን ፣ አንጎልም የሀሳብ ማፍለቂያ ብልት መሆኑን ፣ ስለዚህም ታዲያ ሐሳብን ከቁስአካል ገንጥሎ ማየት ከፍተኛ ስሕተት መሆኑን ያቀነቅናል ። በዚህ ረገድ ኤንግልስም የሚከተለውን ይላል ፤

« በማሰብና በግዝፈት ፣ በመንፈስና በተፈጥሮ መሀከል ያለው ግንኙነት በፍልስፍና ውስጥ የሚነሳ ዓይነተኛ ጥያቄ ነው ። . . . ፈላስፎችም ለዚህ ጥያቄ በሚሰነዝሩት መልስ መሠረት ከሁለት ላይ ተከፍለዋል ። መንፈስ ለቁስ አካል ቀዳማዩ ነው ያሉት በሀሳባዊነት አምባ ይጠቃለላሉ ። ተፈጥሮን ቀዳማይ ነው ያሉት ደግሞ ቁስ አካላዊነትን የሚቀበሉትን የተለያዩ የአስተሳሰብ ዝንባሌዎችን ያጠቃልላሉ ። »
(ኤንግልስ ሉድዊግ ፊወርባኽ)

ለጠቅ አድርጐም እንዲህ ይላል ፤

« በሕዋሳታችን አማካይነት የምንገነዘበውና እኛም ራሳችን አንድ አካሉ የሆንነው ቁስ አካላዊው ዓለም የመጀመሪያው የመጨረሻውም እውነት ነው ። . . . ኅሊናችንና ሐሳባችንን ምንም ያህል ከስሜታዊ ሕዋ



ሳቶቻችን ውጭ የሆኑ ቢመስሉም ፣ ቁስ አካላዊ የሆነው የሰውነት ክፍል ማለትም የአንጎል ውጤቶች ናቸው ። ቁስ አካል የልቡና ውጤት አይደለም ፤ እንዲያውም ልቡና ራሱ የቁስ አካል ከፍተኛ ውጤት ነው እንጂ ። (እንደላኛው)

ሐሳብንና ቁስ አካልን በሚመለከተው ረገድ ኤንግልስ እንዲህ ይላል፦
«ሐሳብን ፣ ከሚያስብ ቁስ አካል በምንም ዓይነት ገንጥሎ ማየት አይቻልም ። ቁስ አካል የለውጥ ሁሉ መነሻ ነው ። » (ኤንግልስ ፣ ተምኔታዊና ሳይንሳዊ ሶሻሊዝም)

ማርክሳዊውን ቁስ አካላዊ ፍልስፍና ሌኒን እንዲህ ሲል ይገልጸዋል ፤
« ባጠቃላይ ቁስአካልነት ነባራዊውን እውነት (ቁስ አካልን) የሚገነዘበው ከኅሊና ፣ ከሕዋሳታዊ ስሜት ፣ ከልማድ ውጭ የሆነ ራሱን ችሎ የቆመ ነገር አድርጎ ነው ። ኅሊና የግዝፈት ነጸብራቅ ነው ፤ ቢበዛም የዚሁ የግዝፈት ተቀራራቢ (በሐሳብ ደረጃ እሱን የሚመጥንና ትክክለኛ የሆነ) ነጸብራቅ እንጂ ሌላ አይደለም ። » (ሌኒን ፤ ቁስ አካልነትና ቤተ-ሙከራዊ ትችት)

ለጥቆም እንዲህ ይላል ፤

« ቁስ አካል በስሜት ሕዋሳቶቻችን አማካይነት በውስጣችን ስሜትን የሚፈጥር ነገር ነው ፣ ቁስ አካል በስሜታችን አማካይነት የምንገነዘበው ነባራዊ እውነታ ነው . . . ፡-ቁስ አካል ፣ ተፈጥሮ ፣ ግዝፈት ፣ አካላዊው ቀዳማይ ሲሆን መንፈስ ፣ ኅሊና ፣ ስሜት ፣ አእምሮአዊው ፣ ተከታይ ነው ። » (እንደላይኛው)

« በውስጣችን የሚቀረጸው የዓለሙ ሁላ ምስል ቁስ አካል እንዴት እንደሚንቀሳቀስና እንደምንስ አድርጐ« ቁስ አካል እንደሚያስብ » የምንመለከትበት ነው ። » (እንደላይኛው)

« አንጎል የሐሳብ ብልት ነው ። » (እንደላይኛው)

ሐ/ ዓለማችንንና የሚመራበትንም ሕግ ማወቅ አይቻልም በሚለው የእውቀታችንንም ትክክለኛነት በማይቀበለው ፣ ነባራዊ እውነትን አሌ በሚለውና ዓለም ሳይንስ ሊረዳቸውና ሊያውቃቸው በማይችሉ « ብቁዕ ነገሮች » የተሞላ ነው ሲል በሚያቀነቅነው ሐሳባዊነት አንጻር ማርክሳዊው ቁስ አካላዊ ፍልስፍና ዓለም የሚመራበትም ሕግ ሁሉ ሊታወቅ የሚችል መሆኑን ፣ እኛም ስለሕገ-ተፈጥሮ ያለን እውቀት በሙከራና በግብር በመፈተኑ መጠን ፣ ነባራዊ እውነትን የሚመጥን ትክክለኛ እውቀት መሆኑን በዓለምም ውስጥ ሊታወቅ የማይችሉ ነገሮች አለመኖራቸውን ይልቅስ በሳይንስ ጥረትና በልምድም አማካይነት ሊገለጹና ሊታወቁ የሚችሉ ገና ያልታወቁ ነገሮች ብቻ መኖራቸውን ያቀነቅናል ።

ዓለሙ ሊታወቅ አይችልም ፣ ሊታወቁ የማይችሉ « ብቁዕ ነገሮች » አሉ ሲል የሚያቀነቅነውን የካንትና የሌሎችንም ሐሳባውያን በኩረ-ሐሳ

ብ በመተቸትና እውቀታችን ትክክለኛ እውቀት ነው የሚለውን የታወቀውን የቁስ አካላዊነት ፍሬ ሐሳብ በማጥበቅ ኤንግልስ የሚከተለውን ይላል ፤

« የዚህኛውም ሆነ የሌላ ማንኛውም ፍልስፍና ፍሬ ክርስኪ. አስተሳሰብ ዋና መመላለሻችን ግብር ነው ፤ ይኸውም ሙከራና ሥራ ማለት ነው ። ስለተፈጥሮ ሂደት ያለንን ጽንሰ-ሐሳብ ትክክለኛነት እኛ ራሳችን በግብር በመሥራት ካለበት የተፈጥሮ ሁኔታ ቀስመን ለራሳችን በሚጠቅም አኳኋን ተጨባጭ በማድረግ ሕልውናውን በማጽደቅ ከፈተነው ፤ ያን ጊዜ እንግዲያው የነፃነት « ብቁዕ ነገር » ብሎ ፈሊጥ ሥፍራ አይኖረውም ። በእጽዋትና በእንስሳት አካል ውስጥ በተፈጥሮ የሚሠሩት ንጥረቅመሞች በኦርጋኒክ ኬምስትሪ አማካይነት በተከታታይ ሊቀመሙ እስከተቻለበት ጊዜ ድረስ « ብቁእ ነገሮች » ሆነው ቆይተዋል ፤ በጥበብ አማካይነት ግን እነዚህ « ብቁዕ ነገሮች » ለኛ የሚበጁ ግልጽ ነገር ሆነዋል ፤ ለምሳሌም ለማደር የተፈጥሮ ቀለም የሚሰጠውን አሊዛሪን የሚባለውን ንጥረ ነገር ለማግኘት እንደቀድሞው ማደርን ኮትኩተን ማሳደግ ሳያስፈልገን ከድንጋይ ከሰል ዝቃጭ ርካሽና ቀላል በሆነ መንገድ እንሰራዋለን። ኮፐርኒከስ ያቀነቀነውና የጸሐይና በዙሪያውም ያሉት ዓለማት ቀመር ከመቶ ፣ ከሺህ ፣ ካሥር ሺህ የሚበዛው ትክክለኛ ወደመሆኑ ቢያዘነብልም እንኳን መላ ምት ብቻ ነበር ። በኋላ ግን ሌቬሪዩ የሚባለው ሊቅ በዚህ ቀመር ከተገኘው መረጃ ላይ በመመርኮዝ ገና ያልታወቀ ዓለም መኖሩ የግድ መሆኑን ብቻ ሳይሆን ይህ ዓለም በጠፈር ውስጥ ሊገኝ የሚችልበት የተለየ ሥፍራ መኖሩንም ቀምሮ ሲያውቅ ከዚያም ጋሊሊዮ የተባለው ሊቅ ይህን የተባለውን ዓለም ሲያገኝ ያን ጊዜ ኮፐርኒከስ ያቀነቀነው ቀመር በግብር ተፈትኖ ትክክለኛ መሆኑ ተገለጸ ። »

የማችደቀ መዛሙርት የሆኑትን ቦግዳኖቭን፣ ባዛሮቭን፣ ዩሺኪቪችንና ሌሎችንም የፊዴይዝም አቀንቃኞች መሆናቸውን በመንቀፍ ስለተፈጥሮ ሕግጋት ያለን እውቀት ትክክለኛ እውቀት መሆኑን የሳይንስ ሕግጋትም ነባራዊውን እውነት የሚወክሉ መሆናቸውን የሚያቀነቅነውን ቁስአካላዊ ፍሬ ሐሳብ በማጥበቅ ሌኒን እንዲህ ይላል ፤

« የዘመናችን ፊዴይዝም ሳይንስን አሌ አይልም ፤ አሌ የሚለው የሳይንስን « የተንዛዛ እምነቱን » ማለትም ነባራዊ እውነትን መቀበሉን ብቻ ነው ። ነባራዊ እውነት ካለ (ቁስአካላዊነትን የሚቀበሉት እንደሚሉት) አፍአዊውን ዓለም በሰው ልምድ አማካይነት የሚያንጸባርቀው የተፈጥሮ ሳይንስ ብቻ ነባራዊውን እውነት የሚያስጨብጠን ከሆነ እንግዲያውስ ፊዴይዝም ስህተተኛ መሆኑ በማያዳግም አኳኋን ይገለጸል ። »

(ሌኒን ፤ ቁስ አካልነት ቤተ-ሙከራዊ ትችት)

ባጭሩ እንግዲህ የማርክሲስት ቁስአካላዊ ፍልስፍና ዋና ዋና መለዮዎቹ እነዚህ ናቸው ።



እንግዲህ ደግሞ የቁስ አካላዊ ፍልስፍና መርሆዎች ሕብረተሰብንና ታሪኩን የሕብረተሰብንም ታሪክና የወዝአደሩን ፓርቲ ተግባሮች ለማጥናትና ለመመርመር ሲውሉ የቱን ያሕል እንደሚጠቅሙና ምን ያህልስ አስፈላጊ እንደሆኑ መረዳቱ አያዳግትም ።

በተፈጥሮ ክስተቶች መሐል ያለው ግንኙነትና መደጋገፍ የተፈጥሮ እድገት ሕግጋት ከሆኑ በሕብረተሰብ ክስተቶች መሐል ያሉት ግንኙነቶችም የሕብረተሰብ እድገት የሚመራባቸው ሕግጋት እንጂ እንዲያው የአጋጣሚ ነገር አለመሆናቸው እሙን ነው ።

ስለዚህም ሕብረተሰብ ፣ የሕብረተሰብ ታሪክ « የአጋጣሚዎች » ጥርቅም መሆኑ ቀርቶ መደበኛ ሕግጋት ተከትሎ የሚጓዝ የሕብረተሰብ እድገት ታሪክ ይሆናል ፤ ታሪክም ሳይንሳዊ ለመሆን ይበቃል ።

ስለዚህም የወዝአደሩ ፓርቲ ተግባራት « በታላላቅ ግለሰቦች » መልካም ምኞት « በአእምሯዊ ዝንባሌ » « በዘላለማዊ ግብረገብነት » ወዘተ . . . መመራት የለበትም ፤ በሕብረተሰብ እድገት ሕግጋትና በነዚህም ሕግጋት ጥናት ላይ ተመሥርቶ እንጂ ።

በተጨማሪም ደግሞ ዓለም ሊታወቅ ከቻለና ስለ ተፈጥሮ እድገት ሕግጋት ያለንም እውቀት ትክክለኛ ከሆነና ነባራዊ እውቀትነት ያለው ከሆነ ሕብረተሰብን የሕብረተሰብም እድገት ሕግጋት ሊታወቁ እንደሚችሉና ሳይንስም ስለሕብረተሰብ እድገት ሕግጋት የሚያቀርባቸው መረጃዎች ትክክለኛና ነባራዊ እውነትነት ያላቸው እንደሚሆኑ ግልጽ ነው።

ስለዚህ የሕብረተሰብን ታሪክ የምናጠናበት ሳይንስ ምንም እንኳን የሕብረተሰቡ ክስተቶች የተወሳሰቡ ቢሆኑም እንደባዮሎጂ እንበል ትክክለኛ ሳይንስ ሊሆንና እነዚህንም ሕግጋት በተግባር በማዋል መጠቀሚያ ሊያደርጋቸው ይችላል ።

ስለሆነም የወዝአደሩ ፓርቲ ሥራውን ግልጽ በሆኑ ምኞታዊ ስሜቶች መምራት የለበትም ፤ በሕብረተሰብ እድገት ሕግጋትና ከነዚህም በሚፈልቁ ጠቃሚ ሐሳቦች እንጂ ።

በዚህም ዓይነት ሶሻሊዝም የሰብአዊነትን ደኅንነት የምንመኝበት ሕልም መሆኑ ይቀርና ሳይንስ ለመሆን ይበቃል ።

ስለዚህም በሳይንስና በተግባራዊ ክንውን ፣ በንድፈ-ሐሳብና በግብር መካከል ያለው መተሳሰር ፣ የነሱም አንድነት ፣ ወዝአደሩ የሚመራበት ፋና ሊሆን ይገባዋል ።

አንድም ደግሞ ተፈጥሮ ግዙፍ አካል እንደመሆኑ መጠን ቀዳማይ ከሆነ ልቡና ፣ ሐሳብ ፣ ደኃራይ ፣ ተከታይ ፣ ከሆነ ቁስ አካላዊው ዓለም ነባራዊ እውነታን የሚወክልና ከሰውም ልቡና ውጭ ራሱን ችሎ ህልው የሆነ ከሆነና

ልቡና ደግሞ የዚህ ነባራዊ እውነታ ነጸብራቅ መሆኑ ከታወቀ እንግዲያ ውስ የሕብረተ ሰብም ቁስ አካላዊ ኑሮ ሕልውናው ቀዳማዊ ሲሆን መን ፈሳዊ አቋሙ ደግሞ ደኅራይና ተከታዩ መሆኑ የሕብረተሰብ ቁስ አካ ላዊ ኑሮ ከሰዎች ፈቃድ ውጭ ራሱን ችሎ የሚገኝ ነባራዊ እውነታሲሆን የሕብረተሰብ መንፈሳዊ አቋም ግን የዚህ ነባራዊ እውነታ የሕልውና አም ሳል መሆኑ ግልጽ ይሆንልናል ።

ስለዚህም የሕብረተሰብ መንፈሳዊ ኑሮ አቋም ምንጭ የማኅበራዊ ሐሳቦች፣ የሕብረተሰብ ንድፈ ሐሳቦች ፣ የፖለቲካ አውደ ሐሳቦችና ተቋ ሞች እነዚህ ሁሉ የሚነቁበት ምንጩ ራሳቸው ሐሳቦቹ አውደ ሐሳቦቹና ተቋሞቹ ሳይሆኑ፣እነዚሁ ሐሳቦች፣ንድፈ ሐሳቦች፣ ዓውደ ሐሳቦችና ተቋ ሞቹም የሚፈልቁበት የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ ማሕበራዊ ሕልውና ነው ።

ስለሆነም ደግሞ በሕብረተሰብ ታሪክ ውስጥ በተለያዩ ወቅቶች የተ ለያዩ ሐሳቦች፣ንድፈ-ሐሳቦችና ዐውደ ሐሳቦች የፖለቲካ ተቋሞች ፣ ሲፈ ልቁ ብናይ በባርነት ሥርዓት ውስጥ አንድ ዓይነት ማኅበራዊ እምነቶች ንድፈ-ሐሳቦች ዐውደ ሐሳቦችና የፖለቲካ ተቋሞች ሲኖሩ በፊውዳሊዝም ሥርዓት ደግሞ ሌሎች ቢያጋጥሙን ፣ እንዲሁም ደግሞ በካፒታሊዝም ሥርዓት ደግሞ ሌሎች ቢያጋጥሙን፣ ይህ መሆኑን ለመረዳት የእነዚህን ሐሳቦች፣ንድፈ- ለየት ያሉ ቢያጋጥሙን፣ይህ መሆኑን ለመረዳት የእነዚህን ሐሳቦች፣ንድፈ- ሐሳቦች ፣ ዓውደ ሐሳቦችና የፖለቲካ ተቋሞች በ« ተፈጥሮአቸው » በ «ባሕርያቸው » ያለውን እንዲገልጹልን አንማጸናቸውም ፣ በሕብረተሰብ እድገት ታሪክ ውስጥ በተለያዩ ወቅቶች የሕብረተሰቡ ቁስ አካላዊ ኑሮ የሚገኝባቸውን ልዩ ልዩ ሁኔታዎች እንመረምራለን እንጂ ።

የሕብረተሰብ ሕልውና ምንም ዓይነት ይዞታ ቢኖረው የአንድ ሕብ ረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ የሚገኝበት ሁኔታ ምንም ቢሆን የዚህ ሕብረተ ሰብ ሐሳቦች ፣ ንድፈ-ሐሳቦች ፣ የፖለቲካ ዐውደ ሐሳቦችና የፖለቲካ ተቋ ሞች ሁሉ ይህንኑ ሕልውናውንና ኑሮውን መስለውና አክለው የሚፈልቁ ናቸው ።

በዚህም ረገድ ማርክስ የሚከተለውን ይለናል ፤

« የሰዎችን ሕልውና የሚወስነው ኅሊናቸው አይደለም ፤ ይልቅስ ማኅበራዊ ሕልውናቸው ኅሊናቸውን ይወስነዋል እንጂ ።»

(ማርክስ ለፖለቲካዊ ኢኮኖሚ ሐተታ አስተዋጽኦ ነገር)

ስለዚህም በመመሪያው ላይ ስህተት እንዳይሠራ በሕልመኞች ከንቱ ምኞት ከመባከን ይድን ዘንድ የወዝአደሩ ፓርቲ ማንኛውንም ተግ ባሩን ለማከናወን ረቂቅ በሆኑ በማይጨበጡ «በሰብዓዊ አእምሮ ብሂሎች» መመራት የለበትም ፣ የሕብረተሰብን እድገት የሚወስኑትን የሕብረተሰ ብን ቁስ አካላዊ ኑሮ ተጨባጭ ሁኔታዎች መመርኮዝ አለበት እንጂ በ «ታላላቅ ሰዎች» መልካም ምኞት መመራት የለበትም ፣ የሕብረተሰብ



ቁስ አካላዊ ኑሮ እድገት የሚጠይቃቸውን ሁኔታዎች ተከትሎ መሄድ እንጂ ።

ተምኔታውያኑ ናሮድኒኮችን ፣ አናርኪስቶችንና ሶሻሊስት አብዮተ ኞችንም ጨምሮ ድቀት ሊገጥማቸው የበቃው በብዙ ምክንያቶች ሲሆን፤ አንድና ዋነኛው ግን የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ በሕብረተሰብ እድ ገት ውስጥ ቀዳማዩን ሙያ የያዘ መሆኑን አለመገንዘባቸውና አለ መቀ በላቸው ነው ፣ ስለዚህም ታዲያ ወደሐሳባዊነት አዘቅት በማቆልቆል የሚያከናውኗቸውን ተግባሮች ሁሉ የሕብረተሰብ ቁስ-አካላዊ እድገት በሚጠይቃቸው ተጨባጭ ሁኔታዎች ላይ መስርተው በመምራት ፈንታ እነ ዚህን ግዴታዎች ችላ በማለት ከነሱ ነጻ በሆኑና ከሕብረተሰብ ተጨባጭ ኑሮ በተገነጠሉ ። « ሐሳባዊ እቅዶችና » « ሁሉን አቀፍ ትልሞች » ላይ ተንጠልጥለው ቀሩ ።

የማርክሲዝም — ሌኒኒዝም ኃይሉና ጸጋው በማንኛውም ተግባራዊ ክንውኑ ሁሉ የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ እድገት በሚጠይቃቸው ተጨ ባጭ ሁኔታዎች መሠረትና ከሕብረተሰብ ተጨባጭ የኑሮ ይዞታ ሳይገነ ጠል መመራቱ ላይ ነው ያለው ።

ግና ታዲያ ማርክስ እንዲህ ብሏልና በሕብረተሰብ ውስጥ የሚፈል ቁት ሐሳቦች ንድፈ-ሐሳቦች፣የፖለቲካ አውደ ሐሳቦችና የፖለቲካ ተቋ ሞች በሕብረተሰብ ሕልውና ውስጥ ከቁም ነገር የማይጣፉ ፣ ዋጋ የሌላ ቸው ነገሮች ናቸው ማለት አይደለም ፣ እነሱም በፈንታቸው የሰዎችን ማኅበራዊ ሕልውና የሕብረተሰብን ኑሮ ቁስ አካላዊ ሁኔታዎች አይጫኗ ቸውም ማለት አይደለም ። እስካሁን ድረስ ስናወራ የቆየነው የሕብረተ ሰብ ሐሳቦች፣ ንድፈ-ሐሳቦች፣ ዐውደ ሐሳቦችና የፖለቲካ ተቋሞችም ስለ ሚፈልቁበት ምንጭ ፣ ስለሚፈልቁበት አኳኋን የሕብረተሰብ መንፈሳዊ አቋም የሕብረተሰቡ ቁስ አካላዊ ኑሮ የሚገኝባቸው ሁኔታዎችን ነጸብ ራቅ ወይም ምስሉ ስለመሆኑ ነው ። የነዚህን ሐሳቦች ፣ ንድፈ-ሐሳቦች፣ ዐውደ ሐሳቦችና የፖለቲካ ተቋሞች ቁም ነገር በታሪክ ውስጥ ያላቸውን ሚና በሚመለከተው ረገድ ቢሆን ታሪካዊ ቁስ አካልነት አሌ ሊላቸው ይቅርና እንዲያውም እነዚህ ነገሮች በሕብረተሰብ ሕልውና በታሪኩም ውስጥ ያላቸውን ሙያና አስፈላጊነት ጠበቅ አድርጎ ያቀነቅናል ።

የትም ቢሆን መች ልዩ ልዩ የሕብረተሰብ አስተሳሰቦችና ንድፈ-ሐ ሳቦች ይገኛሉ ። ዘመን የተላለፋቸውና ያረጁ ያፈጁትን የሕብረተሰብ ኃ ይሎች ጥቅም ብቻ የሚደጉሙ የሚደጉሱ አሮጌ አስተሳሰቦችና ንድፈ- ሐሳቦች አሉ ። የነዚህ ሙያና ከቁም ነገርም የሚጣፉበት ምክንያት የሕ ብረተሰብን እድገት እርምጃውን የሚያደናቅፉ የሚገቱ ከመሆናቸው ላይ ነው ። በነዚህ አንጻር ደግሞ የተራመዱትን የሕብረተሰብ ኃይሎችን ጥቅም የሚንከባከቡት የሚያዳብሩ አዲስና ተራማጅ አስተሳሰቦችና ንድ

ፈ ሐሳቦች አሉ ። የነዚህ ሙያና ቁም ነገር ደግሞ የሕብረተሰብን እድገት እርምጃቸውን የሚያቀለጥፉ ከመሆናቸው ላይ ነው ፤ እነዚህንም አስተሳሰቦችና ንድፈ-ሐሳቦች የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ እድገት የሚጠይቃቸውን ሁኔታዎች የበለጠ ትክክል አድርገው ባንጸባረቁ መጠን ሙያቸውና ቁም ነገራቸውም በዚያው ልክ ከፍ ያለ ይሆናል ።

አዳዲስ ሐሳቦችና ንድፈ-ሐሳቦች የሚፈልቁት የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ በሚያደርገው እድገት በሕብረተሰብ ፊት አዳዲስ ግዳጆች ሲደቀኑበት ነው ። እነዚህ አሳቦችና ንድፈ-ሐሳቦች አንዴ ከፈለቁ በኋላ ግን ሕብረተሰቡ የገጠሙትን አዲስ ግዳጆች ለማሟላት የሚበጁና የሕብረተሰብን እርምጃ የሚያቀላጥፉ ልዩ ኃይል ይሆናሉ ። የነዚህ አዳዲስ ሐሳቦች ንድፈ ሐሳቦች የፖለቲካ አውደ ሐሳቦችና የፖለቲካ ተቋሞች የማደራጀት የማንቀሳቀስና የመለወጥ ዋጋቸው ከፍ ባለ ተጽእኖ የሚከሰተው እንዲህ ባለው ሁኔታ ጊዜ ነው ። አዲስ ሐሳቦችና ንድፈ ሐሳቦች የሚፈልቁት የግድ አስፈላጊ ሆነው በመገኘታቸው ብቻ ፣ ነው ፣ ያለነሱ የማደራጀት የማንቀሳቀስና የመለወጥ ተግባር የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ እድገት የሚደቅንብንን አጣዳፊ ግዳጆች ማሟላት በፍጹም አይቻልምና ነው ። የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ እድገት ከደቀነብን አዳዲስ ግዳጆች የሚፈልቁት እነዚህ ሐሳቦችና ንድፈ ሐሳቦች ወደፊት ገፍተው በመዝለቅ በብዙኃኑ ዘንድ በመሰራጨት ብዙኃኑ ለሕብረተሰብ ቁስአካላዊ ኑሮ እንቅፋት በሆኑት ያፈጁ ኃይሎች ላይ እንዲነሳ አደራጅና አንቀሳቃሽ ኃይል በመሆን ያፈጀውን ሥርዓት ድቀት ያፋጥናሉ ፣ ያቀላጥፋሉ ።

እንግዲህ አዳዲስ ሐሳቦች ፣ ንድፈ ሐሳቦችና የፖለቲካ ተቋሞች የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ እድገት ከሚጠይቃቸው ግዳጆች ይፈልቁና እነሱ ደግሞ በፈንታቸው በዚሁ በሕብረተሰቡ ቁስ አካላዊ ኑሮ ፣ በሕብረተሰቡ ሕልውና ላይ ተጽእኖአቸውን በማሳረፍ የሕብረተሰቡን ቁስ አካላዊ የኑሮ ግዳጆች ለማሟላትና ተጨማሪ እድገቱን ለማጐልመስ አስፈላጊ የሆኑትን ሁኔታዎች ይፈጥራሉ ።

በዚህ ረገድ ማርክስ እንዲህ ይላል ፤

« ንድፈ-ሐሳብ በብዙኃኑ ዘንድ ተሰራጭቶ ሥር ሲሰድ ራሱ አንድ ግዙፍ ኃይልይሆናል ። » (ሄግል ስለመብት ምንነት ላቀነቀነው ፍልስፍና የተጻፈ ሐተታ ፣)

ስለዚህ እንግዲህ የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ሕልውና የሚገኝባቸውን ሁኔታዎች አቅጣጫ ለመቀየስና እድገታቸውንም ለማፋጠን የወዝአደሩ ፓርቲ የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ሕልውና የሚጠይቃቸውን ነገሮች በትክክል በሚያንጸባርቅና ስለዚህም ደግሞ አድኃሪ ኃይሎችን ደምስሶ መንገዱን ለተራማጅ ኃይሎች ለመጥረግ ዝግጁ የሚሆኑትን ብዙኃኑን በመቀስቀስ ሊያደራጃቸውና ሊያንቃቃቸው በሚችል አስተሳሰብና ንድፈ ሐሳብ ላይ መመካትና በሱም መመራት ይኖርበታል ።



« ኢኮኖሚስቶቹ » ና ሜንሼቪኮቹ ሳይሆንላቸው ያቀረቡት ምክንያት እንዱ ተራማጅ ሐሳቦችና ተራማጅ ንድፈ-ሐሳብ የሕብረተሰብን ኃይሎች በማንቀሳቀስ በማደራጀትና በማነቃነቅ በኩል ያላቸውን ሚና ችላ በማለት ተራ ወደሆነ ቁስ አካልነት ዝቅ በማለት የነዚህን ነገሮች ሙያ ምንም እንዳልሆነ መቁጠራቸውና በዚህም ፓርቲውን ንቃት የሌለው ከንቱ አቋም ብቻ እንዲይዝ ለማድረግ መጣራቸው ነው ።

የማርክሲዝም-ሌኒኒዝም ዋናው ኃይሉና ጥንካሬው ያለው የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ እድገት የሚጠይቃቸውን ሁኔታዎች በሚያንጸባርቅ ተራማጅ ንድፈ-ሐሳብ ላይ መመካቱ ንድፈ ሐሳብን ከተገቢው ደረጃ ላይ ከፍ አድርጐ በማዳበሩና ይህም ንድፈ ሐሳብ ሕብረተሰቡን ለማንቀሳቀስና አደራጅቶ ለማነቃነቅ ያለውን ኃይል እስከ መጨረሻው መጠቀም አስፈላጊ መሆኑን መረዳቱ ላይ ነው ።

እነሆ እንግዲህ በሕብረተሰብ ሕልውናና በሕብረተሰብ ንቃተ ኅሊና መካከል በሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ እድገትና በመንፈሳዊ አቋሙ እድገት መካከል ስላለው ግንኙነት ታሪካዊ ቁስ አካልነት የሚሰጠው መልስ ይህ ነው ።

## 3/ ታሪካዊ ቁስ-አካልነት ፤

እንግዲህ አሁን ማብራሪያ የሚያሻው ጥያቄ የሚከተለው ነው ። ከታሪካዊ ቁስ አካልነት አንጻር ሂዶ ሂዶ በመጨረሻ ላይ የሕብረተሰብን አቋም አስተሳሰቦቹን እምነቶቹን የፖለቲካ ተቋሞቹን ይዞታ የሚወስኑት « የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ የሚገባቸው ሁኔታዎች » ሲባል ምን ማለት ነው ?

ለመሆኑስ እነዚህ « የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ ሁኔታዎች » የምንላቸው ነገሮች ምንድን ናቸው ፣ መለዮዎቻቸውስ ምን ምን ናቸው ?

« የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ ሁኔታዎች » ሲባል ከሁሉ አስቀድሞ ሕብረተሰቡ ራሱ የሚገኝበትን ተፈጥሮ ለሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ እድገት የግድ አስፈላጊና ቀዋሚ የሆነውንና የሕብረተሰብን እድገት አቅጣጫ የሚጫነውን የጂኦግራፊ ይዞታ ማለታችን እንደ ሆነ መቼም ማንም የማይጠራጠረው ነገር ነው ። ታዲያ በሕብረተሰብ እድገት ውስጥ የጂኦግራፊ ይዞታ ያለው ሙያ ምንድነው ? የጂኦግራፊ ይዞታ ወይም አቋም የሕብረተሰብን አቋም የሰዎችን ማሕበራዊ ሥርዓት ባሕርይ ከአንድ ሥርዓት ወደሌላ ሥርዓት የሚደረገው ሽግግር የሚወስነው ዋነኛው ኃይል መሆኑ ነው ወይ ?

ታሪካዊ ቁስ አካልነት ለዚህ የሚሰጠው መልስ አሉ የሚል ነው ።
ታሪካዊ ቁስ አካልነት ለዚህ የሚሰጠው መልስ እሉ የሚል ነው ።
የጂኦግራፊ ይዞታ ለሕብረተሰብ እድገት የግድ ከሚያስፈልጉትና
ቀዋሚ ከሆኑት ባሕርያት አንዱ መሆኑና በሕብረተሰብ እድገት ላይ ተጽ
እና እንዳለው ይህን እድገቱን ሊያፋጥነው ወይም ሊያጓትተው የሚችል
ሁኔታ መሆኑ አያጠያይቅም ። ነገር ግን የሕብረተሰብ ለውጥና እድገት
ከጂኦግራፊ ይዞታ ለውጥና እድገት ጋር ሲነጻጸር እጅግ ፈጣን እንደመ
ሆኑ መጠን የጂኦግራፊ ይዞታ በሕብረተሰብ እድገት ላይ ያለው ተጽእኖ
ዓይነተኛ ወይም ወሳኝ የሚያደርገው አይደለም ። በሶስት ሺህ ዓመታት
ውስጥ በአውሮፓ ሶስት የሕብረተሰብ ሥርዓቶች በቅለው አልፈዋል ፤
እነዚህም ጥንታዊ የጋርዮሽ ሥርዓት የባርነት ሥርዓት ፣ የፊውዳል ሥር
ዓት ናቸው ። በአውሮፓ ምሥራቃዊ ክፍል በሶቪየት ሶሻሊስት ሪፑብ
ሊክ አራት ሥርዓተ-ማኅበሮች በቅለው አልፈዋል ። ታዲያ በዚህ ሁሉ
ጊዜ የአውሮፓ የጂኦግራፊ ይዞታ ወይ ጨርሶ አልተለወጠም ፣ አለዚ
ያም የደረሰው ለውጥ ሲበዛ ትንሽ የረቀቀ በመሆኑ የጂኦግራፊ ጥበብ
ነገር ከቁም ነገር መዝገብ አላኖረውም ። ይህ ደግሞ የተለመደ የማንደ
ነቅበት ነገር ነው ። በጂኦግራፊ ይዞታ ላይ የሚመጣ ማንኛውም ከፍተኛ
ለውጥ በሚሊዮን የሚቆጠሩ ዓመታትን እንደሚጠይቅ በአንጻሩ ግን
በጣም ከፍተኛ የሆነ የሕብረተሰብ ሥርዓት ለውጦች ጥቂት መቶ ዓመ
ታት ወይም በሺ ፣ በሁለት ሺህ ብቻ የሚቆጠሩ ዓመታት እንደሚበቋቸው
ሁላችንም የምናውቀው ነገር ነው ።

እነሆ እንግዲህ ከዚህ የምንረዳው የጂኦግራፊ ይዞታ በሕብረተሰብ
እድገት ውስጥ ዋነኛው የለውጥ ምክንያት ወይም ወሳኙ ነገር አለመሆ
ኑን ነው ፤ ምክንያቱም በጥቂት መቶ ዓመታት ውስጥ አያሌ መሠ
ረታዊ ለውጦች ለሚካሄድበት ሁኔታ በሺህና በአሥር ሺህ በሚቆጠሩ
ዓመታት ውስጥ ምንም ያህል ሳይለወጥ የሚቆይ ነገር ራሱ የለውጥ ዋነኛ
ምክንያት ይሆን ዘንድ አይችልምና ነው ።

በተጨማሪም ደግሞ ፣ « የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ ሁኔታዎች»
ሲባል የሕዝብን ብዛት በተለያየ መጠን የሕዝብ ቁጥር በአንድ በተወሰነ
ሥፍራ መሰብሰቡን ማለታችን መሆኑ ግልጽ ነው ፤ ምክንያቱም ለሕብ
ረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ አስፈላጊ ከሆኑት ሁኔታዎች ውስጥ ሰዎች የግድ
መሠረታዊ ሲሆኑ አንድ የተወሰነ ብዛት ያላቸው ሰዎች በአንድ በተወ
ሰነ ሥፍራ ባንድ ላይ ካልኖሩ የሕብረተሰብ ቁስ አካላዊ ኑሮ ብሎ ነገር
ሊኖር አይችልምና ነው ።እንግዲያማ የሕዝብ ብዛት ማደግ የሰውን ልጅ
ሥርዓተ-ማኅበር ባሕርይ የሚወስነው ዋነኛው ኃይል መሆኑ ነዋ ?

ለዚህም ታሪካዊ ቁስ አካልነት የሚሰጠው መልስ የለም ፣ አይደ
ለም የሚል ነው ።

የሕዝብ ብዛት የሕብረተሰብን እድገት አቅጣጫ የሚቀይስና ሊያፋ
ጥነው ወይም ሊያጓትተው የሚችል መሆኑ አሌ የማይባል ነገር ነው ፣ ነገር



ግን የሕብረተሰብ እድገት ዋነኛው ኃይል ሊሆን አይችልም ፤ በሕብረተ
ሰብ እድገት ላይ ያለውን ተጽእኖ ወሳኝ የሚያደርገው ዓይነት አይደለም፤
ምክንያቱም የሕዝብ ብዛት ብቻውን አንድ ሥርዓተ-ማኅበር ሲለወጥ
ለምን በአንድ በተለየ ሥርዓተ ማኅበር ብቻ እንጂ በሌላ ዓይነት ሥርዓት
አለመተካቱ ለምን እንደሆነ ፣ ለምሳሌ ጥንታዊ የጋርዮሽ ሥርዓተ-ማኅበር
ሲለወጥ በምትኩ የመጣው የባርነት ሥርዓት እንጂ ሌላ አለመሆኑ የባር
ነት ሥርዓት በፊውዳል ሥርዓት ይህ ደግሞ በፊንታው በቡርዧው ሥር
ዓት እንጂ በሌላ አለመተካቱ ለምን እንደሆነ የሚያስረዳን ነገር የለምና
ነው ።

እውነት ፣ የሕዝብ ብዛት የሕብረተሰብን እድገት የሚወስነው ዋነ
ኛው ኃይል በሆነ ኖሮ እንግዲያው ሕዝብ በብዛት ባለበት አካባቢ ሁሉ
እሱኑ የሚመጥን በከፍተኛ ደረጃ የሚገኝ ሥርዓተ-ማኅበር ባገኘን ነበር።
ግና ደግሞ ሁኔታው ይህ አለመሆኑን እናውቃለን ። የቻይናን የሕዝብ ብ
ዛት ስንመለከት ከአሜሪካ ብዛት አራት ጊዜ እጥፍ መሆኑን እናያለን ፤
ሆኖም ግን በሕብረተሰብ እድገት በኩል ስንመለከታቸው አሜሪካ ከቻ
ይና ይልቅ በከፍተኛ ደረጃ ላይ የምትገኝ መሆኗን እናያለን ፣ ምክንያቱም
በቻይና ከፊል ፊውዳል የሆነ ሥርዓት ሰፍኖ ሲገኝ አሜሪካ ግን ገና ዱሮ
የካፒታሊዝምን ከፍተኛ የእድገት ደረጃ ተቀዳጅታ እናገኛታለንና ነው።
የቤልጅግ የሕዝብ ብዛት በአንድ በተወሰነ አካባቢ ያለውን አሰፋፈ
ሩን (ዴንሲቲ) ስንመለከት በአሜሪካ ካለው አሰፋፈር 19 ጊዜ በሶቭየት
ሕብረት ከምናየው ደግሞ 26 ጊዜ የሚበልጥ መሆኑን እናያለን ። ይሁን
እንጂ ፣ በሕብረተሰብ እድገት በኩል አሜሪካ ከቤልጅግ ይልቅ በከ
ፍተኛ ደረጃ ላይ የምትገኝ ስትሆን ቤልጂየምን ከሶቪየት ሕብረት ጋር
የምናነፃጽራት ቢሆን ደግሞ ቤልጅግ ከሶቪየት ሕብረት አንድ የታሪክ
ምእራፍ ወደ ኋላ የቀረች ሆና እናገኛታለን ፣ ምክንያቱም በቤልጅግ
የካፒታሊስት ሥርዓት እንደሰፈነ ሲሆን ፣ ሶቪየት ሕብረት ግን የካፒ
ታሊስት ሥርዓትን አፍርሳ የሶሻሊስት ሥርዓትን አቋቁማለችና ነው ።

እነሆ ከዚህ ሐተታ የምንረዳው የሕዝብ ብዛት የሕብረተሰብ እድ
ገት ዋነኛው ወሳኝ ሀይል አለመሆኑንና ሊሆንም አለመቻሉን የሕብረተ
ሰብን ስርዓት ባሕርይና የሕብረተሰብን አቋም የሚወስነው እሱ አለመ
ሆኑን ነው ።

ሀ) እሺ ታዲያ በሕብረተሰብ ቁስአካላዊ ኑሮ ውስብስብ ሁኔታዎች ው
ስጥ ዋነኛ ሀይል በመሆኑ አቋም ማሕበሩ የሥርዓተ-ማኅበሩን ባሕርይ የሕ
ብረተሰቡን ከአንድ ሥርዓት ወደ ሌላ ሥርዓት መሸጋገር ፤ ይህን ሁሉ
የሚወስነው ምን ሊሆን ነው ?

ታሪካዊ ቁስ አካልነት እንደሚያቀነቅነው ይህ ሀይል ለኑሮ አስፈ
ላጊ የሆኑትን ነገሮች የምናመርትበት ዘዴ ፣ እንደ ምግብ ፣ ልብስ ፣ ጫማ ፣

ቤት ፣ ማገዶ ፣ ማምረቻ መሣሪያዎች ወዘተ . . ያሉትን ለሕብረተሰብ ኑሮና እድገት አስፈላጊ የሆኑትን ቁሳዊ ዕሴቶችን የምናፈራበት ሥልተ ምርት ነው ።

ሰዎች ለመኖር ይችሉ ዘንድ ምግብ ፣ ልብስ ፣ ጫማ ፣ መጠለያ ፣ ማገዶ ፣ ወዘተ . . ያስፈልጋቸዋል ፣ እነዚህን ቁሳዊ ዕሴቶች ለማግኘት ደግሞ ማምረት አለባቸው ፤ እነዚህን ዕሴቶች ለማምረት ደግሞ ሰዎች ምግብን ፣ ልብስን ፣ ጫማን ፣ መጠለያን ፣ ማገዶን ፣ ወዘተ . . ለማምረት የሚያስችሉ መሣሪያዎች ያስፍልጓቸዋል ፣ አንድም ደግሞ እነዚህን ማምረቻዎች ለማምረት በነሱም ለመገልገል መቻል አለባቸው ።

እንግዲህ እነዚህ ቁሳዊ ዕሴቶች የሚመረቱባቸው የማምረቻ መሣሪያዎች የማምረት ልምድና የሥራ ጥበብ በተወሰነ ደረጃም ቢሆን ምስጋና ይግባውና እነዚህን የማምረቻ መሣሪያዎች የሚጠቀሙባቸው ሰዎች እነዚህ ሁሉ ተቀናብረው ባንድ ላይ የሕብረተሰብ የምርት ኃይሎች ይሆናሉ ።

ግን ደግሞ የምርት ኃይሎች የማምረት ተግባር የሥልተ ምርት አንደኛው ገጹ ብቻ ነው ፣ ሰዎች ቁሳዊ ዕሴቶችን ለማምረት ከሚገለገሉባቸው ቁሳቁሶችና የተፈጥሮ ኃይሎች ጋር ያላቸውን ግንኙነት ብቻ የሚያሳይ ገጽ ነው ። ሌላው የማምረት ገጽ ፣ ሌላው የሥልተ ምርት ገጽ ፣ ደግሞ ሰዎች በማምረት ሂደት ውስጥ እርስ በርሳቸው ያላቸውን ግንኙነት የሚያሳየው የምርት ግንኙነት ነው ። ሰዎች ከተፈጥሮ ጋር ትግል የሚገጥሙትና ተፈጥሮን ፣ ቁሳዊ ዕሴቶችን ለማፍራት የሚጠቀሙት ብቻቸውን በተናጠል በየግል ሆነው ሳይሆን በጋራ ፣ በቡድን ፣ በማኅበር ሆነው ነው ። ስለዚህም የማምረት ተግባር ምንጊዜም በማንኛውም ሁኔታ ቢሆን ማኅበራዊ ነው ። ቁሳዊ ዕሴቶችን በሚያመርቱበትም ሁኔታ ሰዎች በመሐላቸው አንድ ዓይነት ግንኙነት ፣ አንድ ዓይነት የምርት ግንኙነት ይመሠርታሉ ። ይህም ግንኙነት ከብዝበዛ ነጻ በሆኑ ሰዎች ዘንድ የመተባበርና የመረዳዳት ግንኙነት ሊሆን ሲችል ፣ ብዝበዛ ባለበት ደግሞ አንዱ ሌላውን የሚጫንበትና የበታች አድርጎ የሚይዝበት ግንኙነት ሊሆን ይችላል ። አንድም ደግሞ ይህ ግንኙነት በአንድ የምርት ግንኙነትና በሌላ ዓይነት የምርት ግንኙነት መሐል መሸጋገሪያ ሆኖ የቆመ ሊሆን ይችላል ። ለማንኛውም የነዚህ የምርት ግንኙነቶች መልክ እንደሆነው ቢሆን ምን ጊዜም በማንኛውም ዓይነት ሥርዓት ቢሆን የምርት ኃይሎችን ያህል መሠረታዊነት ያላቸው ነገሮች መሆናቸው መረሳት የለበትም ።

ማርክስ « በማምረት ተግባር ውስጥ ሰዎች ግንኙነታቸው ከተፈጥሮ ጋር ብቻ ሳይሆን እርስ በርሳቸው ነው ። ሊያመርቱ የሚችሉትም በአንድ ዓይነት መንገድ በመተባበርና በሚያከናውኑትም ነገር እርስ በርስ በመደ



ጋገፍ ነው ። ለማምረትም ከፈለጉ እርስ በርስ የተወሰኑ ግንኙነቶችን ይመሠርታሉ ፣ በነዚህም ማኅበራዊ ግንኙነቶች አማካይነት ብቻ ነው በተፈጥሮ ላይ የሚያከናውኑት ተግባር ፣ የማምረት ተግባር ፣ ሊኖር የሚችለው ፤ » ( ማርክስ ጉልበተ - ደመወዝና ካፒታል )

ስለሆነም እንግዲህ የማምረት ተግባር ሥልተ ምርት የሕብረተሰብን የምርት ኃይሎችና የሰዎችንም የምርት ግንኙነቶች አጠቃሎ የሚይዝ ነው ፤ ስለዚህም ደግሞ ቁሳዊ ዕሴቶችን በሚያመርቱበት ሂደት ውስጥ አንድነታቸው የሚከሰትበት ይዞታ ነው ።

ለ) የማምረት ተግባር አንደኛው መለያ ጠባዩ ምን ጊዜም ቢሆን በአንድ በተወሰነ ደረጃ ላይ ለረዥም ጊዜ እንደነበረ የሚቆይ አለመሆኑና ሁልጊዜም በመለዋወጥና በማደግ ላይ መሆኑ ፣ በተጨማሪም በሥልተ ምርቱ ላይ የሚደረጉ ለውጦች የግድ በሥርዓተ-ማኅበር መላ ቁመና በሕብረተሰብ ሐሳቦች ፣ በፖለቲካ ዓውደ ሐሳቦችና በፖለቲካ ተቋሞች ላይ ሁሉ ለውጥ የሚያስከትሉ መሆናቸውን መላው ማኅበራዊና ፖለቲካዊ ሥርዓት እንዲለወጥ ግድ የሚሉ መሆናቸው ነው ። በተለያዩ የእድገት ደረጃዎች ሰዎች በተለያዩ ሥልተ ምርቶች ወይም በዘወትር አነጋገር ለመጠቀም በተለያዩ የአኗኗር ሥልቶች ይጠቀማሉ ። በጥንታዊው የጋርዮሽ ሥርዓት አንድ ዓይነት ሥልተ ምርት ነበር ፣ በሥርዓተ ባርነት ደግሞ ሌላ ዓይነት ሥልተ ምርት ፣ በፊውዳል ሥርዓት ደግሞ እንዲሁ የተለየ ሥልተ ምርት ነበር ፤ እንዲህም እያለ ይቀጥላል ። በዚህም አኳያ የሰዎች ማኅበራዊ ሥርዓት የሰዎች መንፈሳዊ አቋም ዐውደ ሐሳቦቻቸውና የፖለቲካ ተቋሞቻቸውም የተለያየ መልክ እያየዙ ይዘልቃሉ ።

እንግዲህም ሥልተ ምርቱ ምንም ዓይነት ይሁን ምን ሕብረተሰቡም በአጠቃላይ ሐሳቦቹ ፣ ንድፈ ሐሳቦቹ ፣ የፖለቲካ ዐውደ ሐሳቦቹና ተቋሞቹ ይህንኑ ሥልተ ምርት መስለው አክለው ነው የሚወጡት ።

ነገሩን በዘወትር ፈሊጥ ለመግለጽ ያህል የሰው የአስተሳሰብ ስልት ምንም ዓይነት ይሁን ምን የኑሮ ሥልቱን መስሎና አክሎ ነው የሚወጣው ።

ይህም ማለት እንግዲህ የሕብረተሰብ እድገት ታሪክ ከሁሉም አስቀድሞ የማምረት ተግባር ታሪክ ለብዙ ዘመናት ሲፈራረቁ የኖሩት ልዩ ልዩ ሥልተ ምርቶች ታሪክ ፣ የምርት ኃይሎችና የሰዎቹ የምርት ግንኙነቶች ታሪክ ነበር ማለት ነው ።

ስለሆነም ፣ የኅብረተሰብ እድገት ታሪክ ሲባልም ቁሳዊ ዕሴቶችን ራሳቸውን የሚያመርቱት አምራቾች ታሪክ በማምረት ተግባር ውስጥ ዋነኛው ኃይል የሆኑትና ለሕብረተሰብ ሕልውና አስፈላጊ የሆኑትን ቁሳዊ ዕሴቶች የሚያመርቱት ባተሌ ብዙኃን ታሪክም ነው ማለት ነው ።

ስለዚህም ደግሞ የታሪክ ሳይንስ ደንበኛ ሳይንስ እንዲሆን ከተፈለገ ለእንግዲሁ የነገሥታትንና የጄኔራሎችን ጀብዱ መንግሥታትን « ድል አድርገው » « አስገብረው » የሚኖሩ ጦረኞችን ታሪክ ብቻ በማውሳትና በመካብ መወሰኑ ቀርቶ ከሁሉም በላይ ቁሳዊ ዕሴቶችን የሚያመርቱትን የባተሌዎቹን ብዙኃን፣የሕዝቦችን ታሪክ ለመመርመር ፣ ለማጥናትና ለማስተንተን መዋል አለበት ።

ይህም ስለሆነ ደግሞ የሕብረተሰብ ታሪክ የሚመራባቸውን ሕግጋት ለማወቅና ለመረዳት የሚያስችሉን ፍንጮች መሻት ያለብን በሰዎች ልቡና፣በሕብረተሰብ ዐውደ ሐሳቦችና እምነቶች ውስጥ ሳይሆን፣በአንድ በተወሰነ የታሪክ ዘመን ያለ ሕብረተሰብ በሚጠቀምበት ሥልተ ምርት ውስጥ ነው ፤ ፍንጩም ሆነ ምንጩ የሕብረተሰቡ የምጣኔ ሀብት ኑሮው ነው ።

ስለዚህም ደግሞ የታሪክ ሳይንስ ተቀዳሚ ግዳጅ የማምረትን ተግባር ሕግጋት የምርት ኃይሎችን እድገትና የምርት ግንኙነቶች የሚመሩባቸውን ሕግጋት የሕብረተሰብን የምጣኔ ሀብት እድገት ሕግጋት መመርመር ማጥናትና ማወቅ መሆን አለበት ማለት ነው ።

ስለዚህም የወዝአደሩ ፓርቲ ደንበኛ ፓርቲ ይሆን ዘንድ ከሁሉ አስቀድሞ የማምረት ተግባር የሕብረተሰብ የኢኮኖሚ እድገት የሚመራባቸውን ሕጐች አውቆ በዚህ እውቀት የታጠቀ መሆን ይኖርበታል ።

ስለዚህም ደግሞ በመመሪያው በኩል ከስሕተት እንዲድን የወዝአደሩ ፓርቲ ፕሮግራሙን ሲተልምም ሆነ ተግባሮቹን ሲያከናውን በቅድሚያ መነሳት ያለበት ከማምረት ተግባር ሕግጋት ከሕብረተሰብ የኢኮኖሚ እድገት ሕግጋት መሆን ይኖርበታል ማለት ነው ።

ሐ) የማምረት ተግባር ሁለተኛው መለዮ ጠባዩ የሚያደርጋቸው ለውጦችና እድገቱ ምንጊዜም ቢሆን የሚጀምሩት የምርት ኃይሎች በሚያደርጉት ለውጥና እድገት ሲሆን ከዚህም ውስጥ በመጀመሪያ ደረጃ በማምረቻ መሣሪያዎች ላይ በሚደረግ ለውጥና እድገት መሆኑ ነው ። ስለዚህም በማምረት ተግባር ውስጥ ከሁሉም ይበልጥ ተንቀሳቃሹና አብዮታዊ ባሕርይ ያለው ገጽ የምርት ኃይሎች ናቸው ። በመጀመሪያ የሕብረተሰብ የምርት ኃይሎች ይለወጣሉ ፤ ያድጋሉ ፣ ከዚያም በነዚህ ለውጦች ላይ በመመርኮዝና ከነርሱም ጋር በመስማማት የሰዎች የምርት ግንኙነቶች ማለትም የኢኮኖሚ ግንኙነቶቻቸው ይለወጣሉ ። ይህ ስለተባለ ግን የምርት ግንኙነቶች በምርት ኃይሎች እድገት ላይ ተጽእኖ የላቸውም ወይም ደግሞ የምርት ኃይሎች በምርት ግንኙነቶች ላይ አይመረኮዝም ማለት አይደለም ። እድገታቸው በምርት ኃይሎች እድገት ላይ የተመሠረተ ሆኖ ሳለ የምርት ግንኙነቶች በፈንታቸው የምርት ኃይሎችን



በመጫን ሊያራምዷቸው ወይም ሊጐትቷቸው ይችላሉ ።እዚህ ላይ ታዲያ በደንብ መገንዘብ ያለብን የምርት ግንኙነቶች ምን ቢያዘግሙ ይህን ያህል ለረዥም ጊዜ ወደ ኋላ እንደተጐተቱና ከምርት ኃይሎች ጋር እንደተቃረኑ ሊቆዩ አለመቻላቸውን ነው፤ልክ የምርት ኃይሎች ሙሉ በሙሉ ሊያድጉና ሊራመዱ የሚችሉት የምርት ግንኙነቶች ከምርት ኃይሎች ባሕርይና ይዞታ ጋር የሚገጣጠሙ በመሆን ለምርት ኃይሎች ሙሉ እድገት አስፈላጊውን መንገድ ጥርጊያ ሲያደርጉላቸው እንደሆነ ብቻ የመሆኑን ያህል ማለት ነው ። ስለዚህም የምርት ግንኙነቶች የሆነውን ያህል ከምርት ኃይሎች እድገት ወደኋላ ሲያዘግሙ ቢውሉ ውለው አድረው ከምርት ኃይሎች እድገትና ባሕርይ ጋር መገጣጠማቸው አይቀርም ፣ ደግሞም በእርግጥ ይገጥማሉ ። አለያማ የምርት ኃይሎችና የምርት ግንኙነቶች በሥርዓተ ምርት ውስጥ የሚኖራቸውን መሠረታዊ አንድነት ጨርሶ አሌ ማለት የማምረትን እንዲያው መላውን ማፋለስ ምርት ሥርዓት ላይ ቀውስ ማስከተል ፣ የምርት ኃይሎችንም ማማሰን ሊሆንብን ነው።

የምርት ግንኙነቶች ከምርት ኃይሎች ባሕርይ ጋር የማይገጣጠሙበትና የሚጋጩበት ሁኔታ አንድ ምሳሌ የሚሆነን በካፒታሊስቶች የግል ይዞታ የሚገኙት የምርት መገልገያዎች ከማምረት ሂደት ማኅበራዊ ባሕርይ ከምርት ኃይሎች ማኅበራዊ ባሕርይ ጋር የማይገጣጠሙ መሆናቸው በጉልህ አፍጦ የሚታይበት በካፒታሊስት ሀገሮች የምናየው የኢኮኖሚ ቀውስ ነው ። ይህ ሁኔታ የኢኮኖሚ ቀውሶችን በመፍጠር የምርት ኃይሎችን መማሰን ያስከትላል ። በተጨማሪ ግን ይህ አለመጣጣም ራሱ በፈንታው ያሉትን የምርት ግንኙነቶች በመደምሰስ ለምርት ኃይሎቹ ባሕርይ የሚበጁና ከሱም ጋር የሚገጥሙ የምርት ግንኙነቶችን መፍጠር ግቡ ለሆነው የሕብረተሰብ አብዮት የኢኮኖሚ መሠረቱ ወይም መንስኤው ይሆናል ።

በዚህ አንጻር ደግሞ የምርት ግንኙነቶች ከምርት ኃይሎች ባሕርይ ጋር ሙሉ በሙሉ የሚገጣጠሙበት ምሳሌ የሚሆነን የምርት መገልገያዎች ማኅበራዊ ይዞታ ከምርት ሂደት ማኅበራዊ ባሕርይ ጋር ሙሉ በሙሉ የሚገጥሙበትና ስለዚህም ታዲያ የኢኮኖሚ ቀውሶችና የምርት ኃይሎች መማሰን የማይታወቅበት የሶቪየት ሕብረት ሶሻሊስት ሪፓብሊክ ሶሻሊስት ብሔራዊ ኢኮኖሚ ነው ።

እንግዲህ የምርት ኃይሎች በማምረት ተግባር ውስጥ ከሁሉም ይልቅ ተንቀሳቃሹና አብዮታዊው ገጹ ብቻ ሳይሆኑ የማምረትን ተግባር እድገት የሚወስኑም ናቸው ማለት ነው ።

የምርት ኃይሎች አቋምና ይዞታ ምንም ዓይነት ይሁን ምን እነሆ የምርት ግንኙነቶችም እሱኑ መስለው እሱኑ አክለው ነው የሚወጡት።

የምርት ኃይሎች ይዞታ ሰዎች የሚያስፈልጓቸውን ቁሳዊ ዕሴቶች ለማምረት የሚጠቀሙባቸው የማምረቻ መሣሪያዎች ምን ዓይነት ናቸው?

ለሚለው ጥያቄ መልሱን የሚሰጠን ሲሆን የምርት ግንኙነቶች የሚገኙበት ይዞታ ደግሞ የምርት መገልገያዎችን (መሬቱን ፣ ጫካውን ፣ ውኃውን ፣ የማእድን ማውጫዎችን ፣ ጥሬ ነገሮችን ፣ የማምረቻ፡ መሣሪያዎችን የማምረቻ ሥፍራዎችን የመጓጓዣና የመገናኛ መገልገያዎችን ወዘተ . . .) በንብረትነት የያዛቸው የሚያዝባቸው ማን ነው መላው ሕብረተሰብ ባንድነት ነው ፣ ወይስ ሌሎች ግለሰቦችን ፣ ቡድኖችን ወይም መደቦችን ለመበዝበዝ የሚጠቀሙባቸው ግለሰቦች ቡድኖች ወይም መደቦች ናቸው? ለሚለው ጥያቄ መልሱን የምናገኝበት ነው ።

እስቲ ከጥንት ጀምሮ እስካሁን እስካለንበት ዘመን ሲለዋወጥ የመጣውን የምርት ኃይሎችን እድገት ባጠቃላይ እንቃኘው ። ጥሬ ከሆኑት የድንጊያ መሣሪያዎች ጀምረን በቀስትና በፍላጻ ወደመጠቀም ስንሻገር ከዚሁ ጋር ተያይዞ ከአደን ኑሮ እንስሳትን አልምዶ ጥንታዊውን የከብት ርቢ ማካሄድ እንለምዳለን ፤ ከዚያ በድንጊያ መሣሪያዎች ከመገልገል እንወጣና በብረታ ብረት መሣሪያዎች (የብረት መጥረቢያ ከእንጨት ተሠርቶ ከብረት ወገል ጋር የተዋደደ ማረሻ ወዘተ . . .) ወደመገልገል ስንሻገር ከዚሁ ጋር ተያይዞ ከቁፋር ወደ እርሻ ሙያ እንገባለን ፤ ከዚያ የብረታ ብረት መሣሪያዎች እያደር ተሻሽለው ልዩ ልዩ ቁሳቁሶችን መሥራት ይለመዳል ፣ የአንጥረኛው ወናፍ ብቅ ይላል ፣ የሸክላ ሥራ ይጀመራል ፣ አብሮትም እደጥበብ ይዳብርና የእደ ጥበብ ሙያ ከእርሻ ሙያ ተለይቶ ራሱን የቻለ ሥምሪት ይሆናል ፤ ይህም እየገፋ ይመጣና የእጅ ጥበብ ወይም ባለእጅነት በሰፊው ተዘርግቶ ይቆማል ፣ ከዚያም ፣ ከእጅ መሣሪያዎች በመኪና መሣሪያዎች ወደመጠቀም ስንሻገር የእጅ ጥበብም ወደፋብሪካ ጥበብ ይለወጣል ፤ በመጨረሻም የፋብሪካ ጥበብ ዘመናዊውን የታላላቅ ኢንዱስትሪ ሙያ ይወልዳል ፤ እንግዲህ በደፈናው ስንመለከተው በሰው ልጅ ታሪክ ውስጥ የምርት ኃይሎች እድገት የተጓዘበት ጉዳና ይህን የመሰለ ነው ፣ ዝርዝሩ ግን ከዚህ የጠለቀ ለመሆኑ ማስረጃ አንጠቅስበትም ። ከዚህ እንደምናየው የምርት መሣሪያዎች ሊዳብሩና ሊሻሻሉ የበቁት ከማምረት ተግባር ጋር ግንኙነት ባላቸው ሰዎች ክንውን እንጂ ከነሱ ተነጥለው ራሳቸውን ችለው የሆኑ ነገሮች አይደሉም ፣ እንዲሁም ደግሞ ከነዚህ የማምረቻ መሣሪያዎች ለውጥና እድገት ጋር ጐን ለጐን የምርት ኃይሎች ዋነኛው ክፍል የሆኑትም ሰዎች በማምረት ልምዳቸው መለወጥና ፣ መዳበር በሥራ ጥበባቸው በማምረቻ መሣሪያዎች በመጠቀም ችሎታቸው አማካይነት እንደተለወጡና እንደዳበሩ እናያለን ።

በዚህ የታሪክ ጉዞ ውስጥ ከምርት ኃይሎች ለውጥና እድገት ጋር ጐን ለጐን በመጓዝ የሰዎች የምርት ግንኙነቶች የኢኮኖሚ ግንኙነቶቻቸው እንዲሁ ተመሳሳይ ለውጥና እድገት አድርገዋል ።

በታሪክ ውስጥ የምናውቃቸው የምርት ግንኙነቶች ዋና ዋናዎቹ አምስት ዓይነት ናቸው ፤ እነሱም ጥንታዊ የጋርዮሽ ፣ የባርነት ፣ የፊውዳል ፣ ካፒታሊስትና ሶሻሊስት የምንላቸው ናቸው ።



በጥንታዊው የጋርዮሽ ሥርዓተ ማኅበር የምርት ግንኙነቶች መሠረት የምርት መገልገያዎች በሕብረተሰቡ ባለቤትነት ሥር የዋሉ መሆናቸውን ነው ። ይህ በመሠረቱ በጊዜው ከነበሩት የምርት ኃይሎች ባሕርይ ጋር የሚስማር ነበር ። ሰዎች በዚያን ጊዜ ይጠቀሙ የነበረው መጀመሪያ በድንጊያ መሣሪያዎች ወደኋላ ሲልም በቀስትና በፍላጻ መሆኑ ማንም ቢሆን ብቻውን በግል የተፈጥሮ ኃይሎችንና አራዊትን ለመቋቋምም ሆነ ለማደን እንዲችል የሚያበቃው አልነበረም ። በረሀብ ከመሞት ወይም ደግሞ የአራዊት እራት ከመሆን በጐረቤት በሕብረተሰቦች ከመጠቃት ለመዳን ከፈለጉ ከየዱሩ ፍራፍሬ ሲለቅሙም ሆነ ደግሞ ዓሣ ሲያጠምዱ አንድ የሆነ ዓይነት መጠለያ ሲሠሩም ሰዎች የግድ አንድ ላይ ሆነው በማኅበር መሥራት ነበረባቸው ። እንዲህ ዓይነቱ የሕብረት ሥራ ደግሞ የግድ የምርት መገልገያዎችም ሆኑ የምርት ፍሬዎች የማኅበሩ የጋራ ይዞታ እንዲሆኑ አደረገ ። በዚህ ሥርዓት ውስጥ የምርት መገልገያዎች ባጠቃላይ የግል ንብረት የመሆናቸው ነገር ሐሳቡም እንኳን አልነበረም ፤ እርግጥ አንዳንድ የምርት መሣሪያዎች በግለሰቦች ይዞታ ነበሩ ፤ እነዚህ ግን ከአራዊት ጥቃት መከላከያ ወይም መጠበቂያም ጭምር ሆነው የሚያገለግሉ በመሆናቸው ነው ። በተቀረ በዚህ ሥርዓት ውስጥ ብዝበዛ አልነበረም ፣ መደቦች አልነበሩም ።

በባርነት ሥርዓት ውስጥ ደግሞ የምርት ግንኙነቶች መሠረት ባለባርያው የምርት መገልገያዎችን በግል ንብረትነት የያዘበት ሁኔታ ነበር። ባለባርያው በንብረትነት የያዘው አምራቹንም — ባርያውንም ሲሆን— ይህንን ባርያ እንደ እንስሳ ሁላ ሊገዛው ፣ ሊሸጠው ወይም ሊገድለው ይችል ነበር ። ባጠቃላይም እንዲህ ያሉት የምርት ግንኙነቶች በጊዜው ከነበሩት የምርት ኃይሎች ባሕርይ ጋር የሚስምሩ ነበሩ ። በዚህ ወቅት በድንጊያ መሣሪያዎች ፈንታ ሰዎች በብረታ ብረት መሣሪያዎች ላይ ሰልጥነው ነበር ፤ ከብት ርቢንም ሆነ ቁፋሮን የማያውቀው አዳኝ በነበረበት ጐስቋላ የኑሮ ይዞታ ከብት ማርባት ቁፋሮ እደ ጥበብ ለምልመው ያብባሉ ። በነዚህ ልዩ ልዩ የማምረት መስኮችም መሀል የሥራ ክፍፍል ወይም ስምሪት ይፈጠራል ። በዚህ ወቅት በግለሰቦችና በሕብረተሰቦች መካከል የምርት ልውውጥ ሊኖርና ሀብትም በጥቂቶች እጅ ሊካበት የሚችልበት ሁኔታ ይፈጠራል ፤ በእርግጥም ደግሞ የምርት መገልገያዎች በጥቂቶች ወይም በንኡሳን እጅ ይከማቻሉ ፤ ብሎም ታዲያ ብዙኃኑ ለንዑሳን የሚገብሩበትና ወደባርነት የሚለወጡበት ሁኔታ ይፈጠራል ። ስለዚህም በዚህ ሥርዓት ውስጥ በፊተኛው ሥርዓት ውስጥ እናየው የነበረው መላው የሕብረተሰብ አባሎች ይካፈሉበት የነበረው ነጻና የጋራ ወይም የሕብረት ሥራ ይቀርና በሱ እግር ምንም የማይባትሉት የባሪያ ጌቶች የሚበዘብዙዋቸው ባሮች የሚሠማሩበት የግዴታ ሥራ በማምረት ተግባር ውስጥ ዓይነተኛው ሥምሪት ሆኖ ብቅ ይላል ፤ ይስፋፋል ። ስለሆነም ደግሞ በዚህ ሥርዓት ውስጥ በምርት መገልገያዎችም ሆነ በምርት ፍሬዎች ላይ የጋራ

ይዞታ የለም ። በሱ እግር የግል ይዞታ ይተካል ። ባለባርያውም በማያሻማ
አኳኋን ዋናውና ተቀዳሚው የንብረት ባለቤት በመሆን በታሪክ መድ
ረክ ላይ ብቅ ይላል ።

ሀብታምና ድሀ ፤ በዝባዥና ተበዝባዥ ባለሙሉ መብት አልባ የሆኑ ፤
ከዚህም ጋር በሁለቱ መሐል የመረረ የመደብ ትግል እነሆ የባርነት ሥር
ዓት ይህን የመሰለ መልክ ይዞ ነው የተፈጠረው ።

ወደ ፊውዳል ሥርዓተ ማኅበር ደግሞ ስንገባ የምርት ግንኙነቶች
መሠረታቸውን የጣሉት የፊውዳል መኳንንት የምርት መገልገያዎቹን
በንብረትነት ሲይዙ አምራቹን ፣ ገባሩን ግን ሙሉ በሙሉ በንብረትነት
ባልያዙበት ሁኔታ ላይ ነው ፤ ማለትም የፊውዳል መኳንንቱ ገባሩን ሊገ
ዙና ሊሸጡ ቢችሉም እንዳሰኛቸው ይገድሉት ዘንድ ግን አይቻላቸውም።
አንድም ደግሞ ከፊውዳል መኳንንቱ የንብረት ይዞታ ጋር ጐን ለጐን ገበ
ሬውና ባለእጁ የራሱን ማምረቻ ቁሳቁሶች ይዞ በራሱ ጉልበት እየተጠ
ቀመ ሙያውን የሚገፋበት የንብረት ይዞታ በቅሎ ነበር ። ታዲያም እነ
ዚህ የምርት ግንኙነቶች ባጠቃላይ በጊዜው ከነበሩት የምርት ኃይሎች
ይዞታ ጋር የሚስማሩ ነበሩ ። ብረት ማቅለጥና ማንጠር መሻሻሉ የብረት
ማረሻና የሸማ መሥሪያ መስፋፋቱ የእርሻ የአትክልትና የፍራፍሬ የወ
ይን ተክል የወተት ከብት የማርባት ሙያ እያደር መዳበሩ ከአ ንጥረኛው
ከባለእጁ ዛኒጋባ ጐን ለጐን የፋብሪካ ጥበብ መለስተኛ አቋም ይዞ መብ
ቀሉ እነሆ በዚህ ጊዜ የነበረው የምርት ኃይሎች ይዞታ መለያ ጠባዩ
ይህን የመሰለ ነበር ።

እነዚህ አዲስ የምርት ኃይሎች የነበሩበት ይዞታ አምራቹ በማም
ረት ተግባር ላይ የግል ጥረት እንዲያደርግ ለሥራ ዝንባሌ እንዲኖረው
የሥራ ፍላጐት እንዲያሳይ የግድ የሚለው ዓይነት ነበር ። ይህም በመሆኑ
ባለመሬቱ መኳንንት ለሥራ ምንም ፍላጐት የሌለውንና የግል ጥረትየሚ
ያደርገውን ባሪያ የሚይዝበት ምክንያት ስለሌለው በሱ ፈንታ የራሴ የሚ
ለው ትዳር የራሱ የሆኑ የምርት ቁሳቁሶች ያለውንና መሬቱን ለማልማ
ትና ከምርቱም ከፍሎ ለመሬቱ መኳንንት መገበር ይችል ዘንድ የሚያስ
ፈልገው የሥራ ዝንባሌ ያለውን ገባር መያዙን ይመርጣል ።

በዚህ ሥርዓት ውስጥ የግል ንብረት ይዞታ ይስፋፋል ። ብዝበዛም
ቢሆን ትንሽ ለዘብ ማለቱ እንደሆነ እንጂ በባርነት ሥርዓት ከነበረው ጋር
የሚመጣጠን ጥብቅ የሆነ ነበር ። በበዝባዦችና በተበዝባዦች መሀል
የሚካሄድ የመደብ ትግል የፊውዳል ሥርዓት ዓይነተኛው መለዮው ነበር።

በካፒታሊስት ሥርዓት ውስጥ የምናያቸው የምርት ግንኙነቶች ደ
ግሞ ያረፉበት መሠረት ካፒታሊስቱ የምርት መገልገያዎችን በግል ንብ



ረትነት የያዘበት ሁኔታ ነው ፣ ብቻ እዚህ ላይ ካፒታሊስቱ የግል ነጻነታ
ቸው የተጠበቀ በመሆኑ ሊገድላቸውም ሆነ ሊሸጣቸው የማይቻለውን
ነገር ግን ደግሞ ከማንኛውም ዓይነት የምርት መገልገያ ባለቤትነት ነጻቸ
ውን በመውጣታቸው በረሀብ እንዳይሞቱ ሲሉ የጉልበት ኃይላቸውን
ለካፒታሊስቱ ለመሸጥና ስለሆነም የብዝበዛን ቀንበር ለመሸከም የተገ
ደዱትን ሠራተኞች በንብረትነት አይዛቸውም ። ከካፒታሊስት የንብረት
ይዞታ ጋር ጐን ለጐን በመጀመሪያ ላይ ሰፋ ባለ ሁኔታ ገበሬውና ባለእጁ
የምርት መገልገያዎች በግል ንብረትነት የያዘበት ሁኔታ እናያለን ። ባለእ
ጁም ሆነ ገበሬው ከገባርነት ነጻ የሆኑበት በራሳቸው ጉልበት የሚጠቀ
ሙበት ይዞታ ነው ። ታዲያ ፤ በአንጥረኛውና በባለእጁ ዛኒጋባዎችና መለ
ስተኛ የፋብሪካ አቋሞች ፈንታ በመኪና ኃይል የሚጠቀሙ ትላልቅ ፋብ
ሪካዎች እናገኛለን ። ጥንታዊነት ባላቸው የእርሶ አደሩ የማምረቻ ቁሳ
ቁሶች ይታረሱ በነበሩት ሁዳዶች ምትክ በሳይንሳዊ ስልት የሚመሩና
በእርሻ መኪናዎች የሚታረሱ ትልልቅ የካፒታሊስት እርሻዎች በየቦ
ታው ይፈልቃሉ ።

በዚህ ሥርዓት ውስጥ ያሉት አዲስ የምርት ኃይሎች ሠራተኞች
ከተገፋውና ማይም ሆኖ ከቆየው ገባር የበለጠ የሠለጠኑና እስተዋይ
ይሆኑ ዘንድ የመኪና መሣሪያዎቹን አሠራር የተረዱና በደንብ ሊጠቀ
ሙባቸው የሚችሉ እንዲሆኑ የግድ የሚሉ ዓይነት ናቸው ። ይህ በመ
ሆኑም ካፒታሊስቶቹ ከገባርነት ቁራኛ ነጻ ከሆኑት የመኪና መሣሪያ
ዎችንም ለማንቀሳቀስ የሚያስችል እውቀት ካላቸው ደመወዝተኛ ሠራ
ተኞች ጋር መዋዋሉን ይመርጣሉ ።

ግን ደግሞ ካፒታሊዝም የምርት ኃይሎችን ይህን ያህል የላቀ ደረጃ
ካቀዳጃቸው በኋላ ተመልሶ ራሱ ሊፈታቸው በማይቻለው ቅራኔዎች ውስጥ
ተተብትቦ እናየዋለን ። የሚያመርታቸውም ሸቀጦች ቁጥር ከቀን ወደቀን
እየጨመረ በመሄድና ዋጋቸውን ዝቅ በማድረግ ፉክክርን ወይም ጨረ
ታን ያፋፍማል ፣ በዚህም ዝቅተኛና መለስተኛ ከሆኑት የግል ባለንብረ
ቶች ብዙኃኑን እንዲከስሩ ወደ ወዝአደርነት ደረጃ ዝቅ እንዲሉ የመሸ
መት ኃይላቸውም እንዲቀንስ ያደርጋል ፣ የዚህም ውጤቱ ያመረታቸውን
ሸቀጦች ለመሸጥ ለማጣራት አለመቻሉ ይሆናል ። በሌላ በኩል ደግሞ
የማምረትን ተግባር በማሳደግና በሚሊዮን የሚቆጠሩ ሠራተኞችን በት
ላልቅ ፋብሪካዎች ባንድ ላይ ሰብስቦ በማሠራት ካፒታሊዝም የምርትን
ሂደት ማኅበራዊ ጠባይ ያላብሰዋል ፣ በዚህም ደግሞ የምርት ሂደት ማኅ
በራዊ ጠባይ በመላበሱ መጠን የምርት መገልገያዎችም ማኅበራዊ ይዞታ
እንዲኖራቸው የግድ ይላልና ካፒታሊዝም የገዛ ራሱን መሠረት የሚያ
ናጋ ይሆናል ፤ ግን ታዲያ የምርት መገልገያዎች የካፒታሊስት የግል ንብ
ረት ይዞታ እንደያዙ ናቸውና ከምርት ሂደት ማኅበራዊ ባሕርይ ጋር የማ
ይስምር ሆነው እናገኛቸዋለን ።

ታዲያ እነዚህ በምርት ኃይሎች ባሕርይና በምርት ግንኙነቶች መሀል ያሉት የማይታረቁ ቅራኔዎች የሚያስከትሉት አበሳ የሚከሰተው በየወቅቱ በሚመላለሱ— የብዙ—ምርት ቀውሶች አማካይነት ነው ፣ እንደነዚህ ባሉት ቀውሶች ጊዜ ካፒታሊስቶቹ ራሳቸው ባመጡት የብዙኃኑ መገፋትና ማጣት ምክንያት ሸቀጦቻቸው ገዥ ስለሚያጡ በቂ የምርት ውጤቶች ሳይኖሩ ቀርተው ሳይሆን ብዙ—ምርት በመኖሩ ብቻ በሚሊዮን የሚቆጠሩ ሰዎች በሥራ እጦትና በረሀብ በሚሰቃዩበት ጊዜ እነሱ ምርትን ያቃጥላሉ ፤ የፋብሪካ ውጤቶችን ያወድማሉ ፤ የምርት ኃይሎች እንዲማስኑ ያደርጋሉ ።

እነሆ እንግዲህ ፤ የካፒታሊስት የምርት ግንኙነቶች ከምርት ሀይሎች ባሕርይ ጋር የሚስማሩ መሆናቸው እዚህ ላይ ያበቃና ሁለቱ ጨርሶ በማይታረቅ ቅራኔ ተጠምደዋል ማለት ነው ።

እነሆም ደግሞ ፣ ካፒታሊዝም ፣ ተልእኮው አሁን ያለውን የምርት መገልገያዎችን የካፒታሊስት የግል ይዞታ ደምስሶ በሶሻሊስት የሕብረት ይዞታ መተካት የሆነውን አብዮት አርግዞአል ማለት ነው ።

አንድም ፤ የካፒታሊስት ሥርዓት መለዮ ጠባይ በበዝባዦችና በተበዝባዦች መሀል የሚደረግ እጅጉን የተባ የጦፈ የመደብ ትግል መሆኑ ነው ።

እስካሁን በሶቪየት ሕብረት ሶሻሊስት ሬፓብሊክ ብቻ ተቋቁሞ በምናገኘው ሶሻሊስት ሥርዓት ውስጥ ደግሞ የምርት ግንኙነቶች መሠረታቸውን የጣሉት በምርት መገልገያዎች ማሕበራዊ ይዞታ ላይ ነው ። በዚህ ሥርዓት ውስጥ በዝባዥና ተበዝባዥ የለም ። የሚመረቱም ነገሮች ለሁሉም እንደ የስራው ይከፋፈላሉ ፤ ዋናው መርሕም ፤« የማይሠራ ሰው ይበላ ዘንድ አይቻለውም ፣ » የሚል ነው ። በዚህም ሥርዓት ውስጥ ሰዎች በምርት ሂደት ውስጥ ያሏቸው ግንኙነቶች ከብዝበዛ ነጻ የሆኑ ሠራተኞች በሚያደርጉት ጓዳዊ መተባበርና ሶሻሊስት በሆነ የእርስ በርስ መደጋገፍ መንፈስ የተከተቡ ናቸው ። አንድም በዚህ ሥርዓት ውስጥ የምርት ግንኙነቶች የምርት ሀይሎች ካሉበት ይዞታ ጋር ሙሉ በሙሉ የሚገጣጠሙ ናቸው ፤ ምክንያቱም የምርት ሂደት ማሕበራዊ ባሕርይ በምርት መገልገያዎች ማሕበራዊ ይዞታ አማካይነት የሚጠናከር ነውና ነው ።

በዚህም ምክንያት ታዲያ በሶቪየት ሕብረት ውስጥ ያለው ሶሻሊስት ሥርዓት ምርት ምንም ዓይነት ተመላላሽ የብዙ—ምርት ቀውስና የሚያስከትለውም ቅጥ—የለሽ ሁኔታ አይገጥመውም ።

ስለሆነም የምርት ሀይሎች በተፋጠነ እርምጃ ይዳብራሉ ፣ ምክንያቱም እነዚህን የምርት ሀይሎች የሚመጥኑት የምርት ግንኙነቶች እንዲህ ላለው የተፋጠነ እድገት ጥርጊያውን የሚያዘጋጁ በመሆናቸው ነው ።

እነሆ እንግዲህ በሰው ልጅ ታሪክ ውስጥ የታወቁት የሰዎች ግንኙነቶች እድገት የተጓዘበት አኳኋን ይህን የመሰለ ነው ።



አንድም ደግሞ የምርት ግንኙነቶች እድገት በምርት ሀይሎች እድገት ላይ በቅድሚያ ደግሞ በማምረቻው መሣሪያዎች እድገት ላይ የመመርኮዙ ነገር የምርት ሀይሎች ለውጥና እድገት ማምራቱ የማይቀርበት አስፈላጊ ምርኩዝ ይህን የመሰለ ነው ።

« ማምረቻ መሣሪያዎችን መጠቀምና እነሱንም የመሥራት ችሎታ ምንም እንኳን ዘሩ ባንዳንድ የእንስሳት ዝርያዎች ዘንድ ያለ ቢሆንም በተለይ ለሰው ልጅ የሥራ ሂደት ባሕርይ የሆነ ነገር ነው ፤ ስለዚህም ነው ፍራንክሊን ሰው መሣሪያ የሚሠራ እንስሳ ነው የሚለው ። ጥንታዊ ዓጽሞች ከምድር ገጽ የጠፉትን እንስሳት ዝርያዎች ምንነት ለማወቅ የሚረዱትን ያህል ፤ እንዲሁም ከዘመናት በፊት የነበሩ ማምረቻ መሣሪያዎች ቅሪቶች የጠፉት የኢኮኖሚ ሥርዓቶች መልክ ለመመርመር የሚረዱ ከፍተኛ ዋጋ ያላቸው ናቸው ። የተለያዩትን የኢኮኖሚ ደረጃዎች ለመለየት የሚረዱን ቁሳቁሶች ራሳቸው ሳይሆኑ እንዴትና በምንስ ዓይነት መሣሪያ እንደተሰሩ ማወቁ ነው ፣ . . . ። የማምረቻ መሣሪያዎች የሰው ልጅ የሥራ ይዞታ የደረሰበትን የእድገት ደረጃ ብቻ ሳይሆን ሥራው ይካሄድ የነበረበትን ማህበራዊ ሁኔታም ጭምር የሚጠቁሙን ናቸው ፤ » ይላል ማርክስ ። ( ማርክስ ካፒታል ቅጽ 1)

በተጨማሪም ደግሞ የሚከተለውን ይላል ፤

ሀ/ « ማሕበራዊ ግንኙነቶች ከምርት ሀይሎች ጋር በቅርብ የተሣሠሩ ናቸው አዲስ የምርት ሀይሎች ሲፈልቁ ሰዎች በዚያው መጠን ሥልተ ምርታቸውን ይቀይራሉ ፤ ሥልተ ምርታቸውንም ሲቀይሩ ማለትም ኑሮዋቸውን የሚመሩበትን ሥልት ሲቀይሩ በዚያው ልክ መላ ማሕበራዊ ይዞታቸውን ይቀይራሉ ። በእጅ የሚንቀሳቀስ መዘውር( መሣሪያ ተርጓሚ) የፊውዳል መኳንንቱ የሰፈነበትን ሕብረተሰብ ሲያመለክተን በእንፋሎት ሀይል የሚንቀሳቀሰው መኪና ደግሞ ባለ ኢንዱስትሪው ካፒታሊስት የሰፈነበትን ሕብረተሰብ ያመለክተናል ። » ( ማርክስ የፍልስፍና ድህነት)

ለ/« የምርት ሀይሎች የሚያድጉበት ማሕበራዊ ግንኙነቶች የሚፈራርሱበት ልዩ ልዩ ሀሳቦች የሚፈጠሩበት የማያቋርጥ እንቅስቃሴ አለ ፤ የማይለወጥ አንድ ነገር ቢኖር የእንቅስቃሴ ዘይቤ ብቻ ነው ። » ( ይህም እንደላኛው )

ኤንግልስ ስለታሪካዊ ቁስ አካልነት በኮሚኒስት ማኒፌስቶ ውስጥ እንደተቀመረው ሲናገር የሚከተለውን ይላል ፦

« በማንኛውም የታሪክ ዘመን ላይ የሚገኝ የኢኮኖሚ ሥርዓትና ከዚህም ሥርዓት የግድ የሚመነጨው አቋም ማሕበር በተወሰነው ዘመን ለሚፈልቀው የፖለቲካና የአስተሳሰብ ታሪክ ሁሉ መሠረቱ ናቸው . . .

በዚህም መሠረት ጥንታዊ የጋርዮሽ የመሬት ንብረት ሥርዓት ከጠፋ ጀምሮ ያለው ታሪክ በሙሉ በተለያዩ የሕብረተሰብ የእድገት ደረጃዎች ላይ በበዝባዥና በተበዝባዥ በጨቋኝና በተጨቋኝ መደቦች መካከል ሲካሄዱ የኖሩ የመደብ ትግሎች ታሪክ ነው ፤ . . . ይሁንናም ታዲያ ይህ የመደብ ትግል በአሁኑ ወቅት ፣ ተበዝባዥና ተጨቋኝ መደብ (ወዝአደሩ) መላውን ሕብረተሰብ ከእንግዲህ ከብዝበዛ ከጭቆናና ከመደብ ትግሎች እንዳያዳግም አድርጎ ነጻ ካላወጣ ከሚበዘብዘውና ከሚጨቁነው መደብ (ከቡርዧው) ራሱን ነጻ ያወጣ ዘንድ አይሆንለትም ።» ( ለኮሚኒስት ማንፌስቶ የጀርመንኛ እትም ከተጻፈው መቅድም ላይ የተጠቀሰ)

የማምረት ተግባር ሶስተኛው መለያ ጠባዩ አዲሶቹ የምርት ሀይሎችና እነሱንም የሚመጥኑት የምርት ግንኙነቶች የሚፈልቁት ከአሮጌው ሥርዓት ተነጥለው አሮጌው ሥርዓት ጨርሶ ከወደመ በኋላ ሳይሆን በዚያው በአሮጌው ሥርዓት ማህፀን ውስጥ መሆኑ ነው ፤ ይህም የሚሆነው ሰዎች ይሆነኝ ብለው አውቀው በሚያካሂዱት ክንውን ሳይሆን ግብታዊ በሆነ አኳኋን ከሰዎች ልቡናና ፈቃድ ውጭ ነው ። ግብታዊ በሆነ መንገድና ከሰዎችም ፈቃድ ውጭ የሚሆነውም በሁለት ምክንያት ነው ።

አንደኛ ፡- ሰዎች አንዱን ሥልተ ምርት ከሌላው ይልቅ ለመምረጥ ነጻነት ስለሌላቸው እያንዳንዱም አዲስ ትውልድ በኑሮ መስክ በሚሰማራበት ወቅት ከዚያም በፊት ኖረው ያለፉ ትውልዶች ሲያከናውኗቸው በነበሩት ድርጊቶች አማካይነት የተፈጠሩ የምርት ኃይሎችና የምርት ግንኙነቶች ስለሚጠብቁት ፤ ስለዚህም ታዲያ ቁሳዊ ዕሴቶችን ለማምረት ይችል ዘንድ በማምረት መስክ ጥንቱኑ ተዘጋጅቶ የሚጠብቀውን ነገር እስከጊዜው ድረስ ለመቀበልና ራሱንም ከዚሁ ሁኔታ ጋር ለማዋደድ ግድ ስለሚሆንበት ነው ።

ሁለተኛ ፤ አንድ ዓይነት የማምረቻ መሣሪያን ወይም ከምርት ኃይሎች ውስጥ አንዱን ክፍል በሚያሻሽሉበትና በሚያዳብሩበት ጊዜ ሰዎች ይህ ድርጊታቸው የሚያስከትላቸው ማኅበራዊ ለውጦች ምን እንደሚሆኑ በቅድሚያ አይገነዘቡም ወይም ምን ሊሆኑ እንደሚችሉ ቆም ብለው አያጤኑም ። የእለት ችግራቸውን ፣ ሥራቸው መቃለሉንና ጉዳያቸውን መተኮሳቸውን ብቻ ነው የሚመለከቱት ።

በዚህም መሠረት በጥንታዊው ሥርዓተ-ጋርዮሽ ዘመን የነበሩ አንዳንድ አባሎች ቀስ በቀስ ከደንጊያ መሣሪያዎች በብረታ ብረት መሣሪያዎች ወደመጠቀም ሲሻገሩ ፣ ይህ አድራጎታቸው ምን ማኅበራዊ ለውጥ እንደሚያስከትል አያውቁም ነበር ፤ ይህንንም ቆም ብሎ ለማጤን አልሞከሩም ፤ ወደ ብረታ ብረት መሣሪያዎች መሻገር በምርት ሂደት ውስጥ አብዮታዊ ለውጥ ማምጣቱንና በመጨረሻም ወደ ሥርዓተ ባርነት የሚያመራ መሆኑን አያውቁትም ፣ አልተገነዘቡትም ነበር ። በዚያን ጊዜ ዓላማቸው ሁሉ የሥራ ሸክማቸውን ማቃለልና ጉዳያቸውን



የመተኮስ ብቻ ነበር ፤ ይሁነኝ ብለው የሠሩትም ነገር ቢኖር ይህንኑ የእለት ችግራቸውንና የግል ጉዳያቸውንም በማሟላት ክበብ ብቻ የተወሰነ ነበር ።

እንዲሁም የፊውዳል ሥርዓት በሰፈነበት ጊዜ ጨቅላው ቡርዧ ከትንንሾቹ የሙያ ሱቆች ጐን ለጐን የበቀሉትን የፋብሪካ አቋሞች በማቋቋም የሕብረተሰቡን የምርት ኃይሎች ይዞታ ሲያራምድ ይህ ድርጊት የሚያስከትለውን ማኅበራዊ ለውጥ ይሁነኝ ብሎ አላጤነውም ። ይህ « ትንሽ » ለውጥ የቡርዧው ተቀዳሚ አባላት ያደገድጉላቸው የነበሩትን ነገሥታት ኃይል ሆነ ይመኙትም የነበረውን የመኳንንቱን ይዞታና ደረጃ ለፍጻሜ ያበቃውን የሕብረተሰብ ኃይሎች አሰላለፍ በአዲስ መልክ የምታደላድል ትሆናለች ብሎ አልገመተም ነበር ። በዚያን ጊዜ ይታየው የነበረው የሸቀጦችን የምርት ወጭ መቀነስና እነዚህን ሸቀጦች በብዛት አምርቶ በእስያና በቅርቡ በተገኘችው የአሜሪካ ምድር በገበያ ላይ በማሰራጨት ከፍተኛ ትርፍ ለመሰብሰብ ነበር ። ይሁነኝ ብሎ የሚያደርገው ነገር ቢኖር ያው ኑሮውን ለማዳበር የዘወትር ተግባሩን በትጋት የሚያከናውን ማንም ሰው በሚያደርገው ክበብ ብቻ የተወሰነ ነበር ።

እንዲሁም ደግሞ የሩስያ ካፒታሊስቶች ከውጭ ካፒታሊስቶች ጋር በመተባበር የዛሩን አገዛዝ እንዳለ ትተው አርሶ አደሮቹን ለመሬት ከበርቴዎች ግፍ አሳልፈው በመስጠት ዘመናዊ ታላላቅ ኢንዱስትሪዎች ሲከተሉ ፣ የምርት ኃይሎች እድገት ምን ዓይነት ማኅበራዊ ለውጥ እንደሚያስከትል ቆም ብለው ለማጤን አልቻሉም ፣ ይህ በምርት ኃይሎች በኩል የተደረገው ታላቅ እመርታ ወዝአደሩ ከአርሶ አደሩ ጋር አንድነትን በመፍጠር ድል የተቀዳጀውን ሶሻሊስት አብዮት የሚያስከትለውን የሕብረተሰብ ኃይሎችን አሰላለፍ ባዲስ መልክ ይፈጥራል ብለው አልገመቱም ነበር ። እነሱስ ይታያቸው የነበረው የኢንዱስትሪን የምርት ይዞታ እስከ መጨረሻው በመግፋት የሀገሪቱን ገበያ በቁጥጥራቸው ሥር አድርገው ሞኖፖሊስቶች በመሆን ከብሔራዊ ኢኮኖሚ የተቻላቸውን ያህል ትርፍ ለማካበት ነበር ። ይሁነኝ ብለው አውቀው የሠሩት ነገር ቢኖር ይህንኑ የዘወትር ተግባር ከማሟላት ውጭ የሆነ አልነበረም ። በዚህም እንጻር ታዲያ ማርክስ የሚከተለውን ይነግረናል ።

« ሰዎች በሚያከናውኑት ማኅበራዊ የማምረት ተግባር( ማለትም ለሰዎች ኑሮ አስፈላጊ የሆኑትን ቁሳዊ ዕሴቶች ለማምረት በሚያከናውኑት ተግባር የአዘጋጁ ማከያ ) የግድ አስፈላጊና ከነሱም ፈቃድ ነጻ የሆኑ ግንኙነቶችን በመሐላቸው ይመሠርታሉ ፤ እነዚህ የምርት ግንኙነቶችም ቁስ አካላዊ የምርት ኃይሎቻቸው ከደረሱበት የተወሰነ የእድገት ደረጃ ጋር የሚመጣጠኑ ይሆናሉ ። » (ማርክስ ምርጥ ጽሑፎች ቅጽ 1)

ይህ ስለተባለ ግን በምርት ግንኙነቶች ላይ የሚደረገው ለውጥ ማለትም ከአሮጌዎቹ የምርት ግንኙነቶች ወደ አዲሶቹ የምርት ግንኙነቶች

ለውጥ ሲደረግ እንዲያውም ስተት ብሎ ያለምንም እንቅፋት ያለምንም ውጣ ውረድ ይሳካል ፣ ይስምራል ማለት አይደለም ። እንዲያውም እንዲህ ያለው ለውጥ ሊካሄድ የሚችለው አሮጌዎቹን የምርት ግንኙነቶች ይዞታ በአብዮታዊ መንገድ ገልብጠ አዲስ የምርት ግንኙነቶችን በመተካት ነው ። አንድ የተወሰነ ደረጃ እስኪደርስ ድረስ የምርት ኃይሎች እድገትና በምርት ግንኙነቶች በኩል የሚደረገው ለውጥ አካሄድ ግብታዊና ከሰዎች ፈቃድ ነጻ የሆነ ነው ። ይህ የሚሆነው ታዲያ እስከተወሰነ ደረጃ ብቻ አዲሶቹ የምርት ኃይሎች እየዳበሩ እያደጉ ከተገቢው የብስለት ደረጃ እስኪደርሱ ድረስ ብቻ ነው ። አዲሶቹ ኃይሎች ከበሰሉ በኋላ ግን ነባሮቹ የምርት ግንኙነቶችና የሚንከባከቡላቸው ክፍሎች የገዥው መደቦች አዲሶቹ መደቦች ይሁነኝ ብለው በሚወስዱት እርምጃ በነዚህ አዲስ መደቦች የኃይል እርምጃ ማለትም በአብዮት ብቻ እንጂ እንዲሁም በጥሞና ሊወገድ የማይችል « የማይበገር» እንቅፋት ይሆናሉ ። እዚህ ላይ ታዲያ ተልእኳቸው ፣ ሙያቸው ፣ አሮጌዎቹን የምርት ግንኙነቶች በኃይል መደምሰስ የሚሆነው አዲስ ማኅበራዊ ሐሳቦች ፣ አዲስ የፖለቲካ ተቋሞች ፣ አዲስ የፖለቲካ ኃይል የሚጫወቱት ከፍተኛ ሚና ጉልህ ሆኖ ይከስታል ። በአዲሶቹ ኃይሎችና በአሮጌዎቹ የምርት ግንኙነቶች መሀል ከሚነሳው ግጭት ከሕብረተሰቡ አዲስ የኢኮኖሚ ጥያቄዎች አዲስ ማኅበራዊ ሐሳቦች ይወለዳሉ ፤ እነዚህ አዲስ ሀሳቦች ብዙኃኑን ሕዝብ አደራጅተው ያንቀሳቅሱታል ፤ ብዙኃኑ ሕዝብ በነዚህ አዲስ ሐሳቦች ነጥሮ አዲስ የፖለቲካ ሠራዊት ሆኖ ይቀረጻል ፤ አዲስ አብዮታዊ ኃይልን ይፈጥራል ፣ በዚህም አሮጌዎቹን የምርት ግንኙነቶች ሥርዓት በኃይል ደምስሶ በምትኩ አዲሱን ሥርዓት ይመሠርታል ። ግብታዊው የእድገት ሂደት በሰዎች ንቁ ድርጊት ይተካል ፣ ሰላማዊው እድገት በኃይል ፣ ግብ ግብ ዝግመት በአብዮት ይተካሉ ።

« ወዝአደሩ » ይላል ማርክስ «ከቡርዧው ጋር ግብግብ በሚገጥምበት ጊዜ ራሱን በመደባዊ አቋም ያደራጅ ዘንድ ሁኔታዎች ያስገድዱታል . . . በአብዮታዊ መንገድም ራሱ የገዥ መደብ በመሆን በኃይል እየተጠቀመ አሮጌዎቹን የምርት ሁኔታዎች ጠራርጎ ያጠፋቸዋል ።» (ማርክስ ኮሚኒስት ማኒፌስቶ)

እንደገና ደግሞ የሚከተለውን ይለናል ፤

ሀ/ « ወዝአደሩ የፖለቲካ የበላይነቱን ቀስ በቀስ እያለ ካፒታልን በሙሉ ከቡርዧው እጅ ፈልቅቆ በማውጣት የማምረቻ መሣሪያዎችን በሙሉ ጠቅልሎ በመንግሥት እጅ ማለትም ወዝአደሩ በመደባዊ አቋሙ ተደራጅቶ ገዥ መደብ ሆኖ በሰፈነበት መንግሥት እጅ ለማማከልና የምርት ኃይሎችንም አጠቃላይ መጠን በተቻለ ፍጥነት ለማሳደግ ይጠቀምበታል ። » (የኮሚኒስት ማኒፌስቶ)

ለ/ « ኃይል አዲስ ሕብረተሰብን ያረገዘ ማንኛውንም አሮጌ ሕብረተሰብ የምታገላግል አዋላጅ ናት ። » (ማርክስ ካፒታል ቅጽ 2)



ማርክስ በ1859 ዓ. ም ለፖለቲካዊ የኢኮኖሚ ሐተታ አስተዋጽአ ነገር ለሚውለው ዝነኛ መጽሐፉ በጻፈው ታሪካዊ የሆነ መቅድም የታሪካዊ ቁስአካልነትን ምንነት አጢቃሎ የቀመረበት አስተዋይነት የተመላበት ምንባብ እነሆ ፤

ሰዎች በሚያከናውኑት ማኅበራዊ የማምረት ተግባር የግድ አስፈላጊና ከነሱም ፈቃድ ነጻ የሆኑ የተወሰኑ ግንኙነቶችን በመሀላቸው ይመሠርታሉ ፤ እነዚህ የምርት ግንኙነቶችም ቁስ አካላዊ የምርት ኃይሎቻቸው ከደረሱበት የተወሰነ የእድገት ደረጃ ጋር የሚመጣጠኑ ይሆናሉ ። እነዚህም የምርት ግንኙነቶች ተጠቃለው የሕብረተሰብ የኢኮኖሚ መዋቅር ማለትም ሕጋዊና ፖለቲካዊ የሆነ ላእላይ መዋቅር ከሱም ጋር የሚስምር ማኅበራዊ ንቃተ-ሕሊና ባንድ ተጣምረው የሚበቅሉበትን መሠረት ይቀምራሉ ። ቁስ አካላዊው ኑሮ የሚመራበት ሥልተ ምርት የሕብረተሰቡን ማኅበራዊ ፣ ፖለቲካዊና አእምሮአዊ የኑሮ ሂደት ይወስናል ። የሰዎችን ሕልውና የሚወስነው ሕሊናቸው አይደለም ፤ ይልቅስ ማኅበራዊ ሕልውናቸው ኅሊናቸውን ይወስነዋል እንጂ ። የሕብረተሰብ የምርት ኃይሎች በአንድ በተወሰነ የእድገት ደረጃ ላይ ሲደርሱ ፣ ነባር ከሆኑ የምርት ግንኙነቶች ጋር ወይም ደግሞ የሕጉ መስከ በሰጣቸው ስያሜ እንጠቀምና ቀደም ሲል ሲንቀሳቀሱባቸው ከኖሩባቸው የንብረት ይዞታ ግንኙነቶች ጋር ግጭት ይፈጥራሉ ። እነዚህ የምርት ግንኙነቶች የምርት ኃይሎች እድገት የሚገለጽባቸውአንዱ መልኩ መሆናቸው ይቀርና እነሱኑ መልሰው የሚቀራኙ ሰንሰለት ይሆናሉ ። ያን ጊዜ ታዲያ የሕብረተሰብ አብዮት ዘመን ይጀምራል ። የኢኮኖሚ መሠረት ሲለወጥ ግዙፍ የሆነው መላ ላእላይ መዋቅርም ከሞላ ጎደል በተፋጠነ አኳኋን ይለወጣል ። ታዲያም እንዲህ ያሉትን ለውጦች በምናጤንበት ጊዜ መቸም ቢሆን የት በተፈጥሮ ሳይንስ ውስጥ የምናደርገውን ያህል ትክክለኛ በሆነ መንገድ ልንጠቁማቸውና ልንወስናቸው በምንችለው በምርት ተግባር የኢኮኖሚ ሁኔታዎች ላይ በሚደረገው ቁስ አካላዊ ለውጥና ሰዎች ይህንን ግጭት ተገንዝበውና አውቀው በሚታገሉባቸው ሕጋዊ ፣ ሃይማኖታዊ ፣ ኪነታዊ ፣ ወይም ፍልስፍናዊ ፣ ባጭሩ ርእዮተ-ዓለማዊ አቋሞች መሐል ልዩነት መኖሩን መገንዘብ ይኖርብናል ። ስለአንድ ግለሰብ ያለን አስተያየት መሠረቱ ራሱ ስለራሱ የሚያስበው እንደማይሆነው ሁሉ እንዲሁም እንዲህ ባለ ወቅት የሚካሄዱትን ለውጦች በዚያው በዘመኑ ንቃተ ኅሊና ክበብ ልንገመግማቸው ፣ ልንዳኛቸው አንችልም ። በዚህ አንጻር ማድረግ ያለብን እንዲያውም የዘመኑን ንቃተ ኅሊና በቁስ አካላዊው ኑሮ ውስጥ በሚገኙት ቅራኔዎች መሠረት በወቅቱ ባሉት የሕብረተሰብ የምርት ኃይሎችና የምርት ግንኙነቶች መሀል በሚነሱት ነባር ግጭቶች ምክንያት ተመርኩዘን ማስተንተንና መግ

ለጽ ነው ። ማንኛውም ማኅበራዊ ሥርዓት ቢሆን ለማደግና ለመዳበር የሚችሉት በውስጡ ያሉት የምርት ኃይሎች በሙሉ እስኪዳብሩ ድረስ ሊጠፉ አይችልም ፤ እንድም ደግሞ የአቋማቸው ሁሉ መሠረት የሚሆነው ቁስ አካላዊ ሁኔታ በዚያው በአሮጌው ሕብረተሰብ ማኅጸን ውስጥ አካል እስኪገዛ ድረስ በከፍተኛ ደረጃ የሚገኙት አዲስ የምርት ግንኙነቶች በፍጹም ሊፈጠሩ አይችሉም ። እና ታዲያም የሰው ልጅ ምንጊዜም ቢሆን የሚተልመው ማሰሪያ ሊያበጅላቸው የሚቻለውን ግዳጆች ብቻ መሆኑን እንገነዘባለን ፤ ምክንያቱም ነገሩን መልሰን በመልኩ፣ በጥሞና ብንመለከተው ምንጊዜም ቢሆን ሰውን የሚገጥሙት ግዳጆች ራሳቸው የሚበቅሉት፣ የሚደቀኑበት እነዚህን ግዳጆች ለማሟላት ማሰሪያ ለመስጠት አስፈላጊ የሆኑት ቁስ አካላዊ ሁኔታዎች መጀመሪያውኑ ሲኖሩ ብቻ፣ አልያም ደግሞ ቢያንስ ቢያንስ በመፈጠር ላይ ሲሆኑ እንደሆነ ሲታይ የኖረ ነገር ነውና ነው ። (ማርክስ፣ ምርጥ ጽሑፎች፣ ቅጽ 1)

እነሆ ማርክሲስት ቁስአካላዊ ፍልስፍና በሕብረተሰብ ኑሮ በሕብረተሰብ ታሪክ እንፃር ሲተረጎም ይህንን የመሰለ ነው ።

እነሆም ደግሞ የዲያሌክቲካዊና የታሪካዊ ቁስ አካልነት ዋና ዋና መለዮዎች እነዚህ ናቸው ።

## 3. ቦልሼቪኮችና ሜንሼቪኮች በስቶልፒን የአድሀሮት እንቅስቃሴ ወቅት ቦልሼቪኮች ከበታኞችና ከኢትዞቪስቶች ጋር ያደረጉት ትግል :-

ከቀድሞው የአብዮቱ የእድገት ወቅት ይልቅ የአድሀሮት ሀይል በያለበት በዚያ ወቅት ውስጥ የፓርቲ ድርጅታዊ ተግባሮችን ማከናወን እጅግ ከባድና አስቸጋሪ ነበር ። የፓርቲው አባሎች ቁጥር ፈጽሞ አቆለቆለ ። በፓርቲው ውስጥ የነበሩ አያሌ የንዑስ ከበርቴ ተጓዥ መንገደኞች በተለይም ምሁራን የዛሩን አገዛዝ የሚያደርሰውን ስቃይ በመፍራት እየከዱ ሄዱ ።

ሌኒን ይህንን ወቅት ሲገልጽ እንዲህ ባለው ወቅት ፓርቲዎች ትምህርታቸውን ማጠናቀቅ አለባቸው ። አብዮቱ መነሳሳት ባለበት ወቅት እንዴት ማጥቃት እንዳለባቸው ተምረዋል ። አድሀሮት ሀይል በያለበትና አብዮቱ አደጋ በገጠመው ወቅት ደግሞ በተገቢው መንገድ እንዴት ማፈግፈግ እንደሚገባው፣ ሚስጢራዊ በሆነ መንገድ ተግባርን እንዴት ማከናወን እንደሚቻል፣ በሕቡእ የገባው ፓርቲ እንዴት መጠበቅና ማጠናከር እንደሚያስፈልግ፣ ህጋዊ መድረክ ለመጠቀም የሚያስችሉት ማናቸውንም አጋጣሚዎች — በተለይም ከሠፊው ሕዝብ ጋር ያላቸውን ግንኙነት ለማጠናከር የሚያስችላቸውን ብዙሀን ድርጅቶች — እንዴት መጠቀም እንደሚገባቸው ጠንቅቀው መማር አለባቸው ።



ሜንሼቪኮች አብዮቱ ደክሞ በንጥረ አመጿ እድገቱ ላያንሰራራ ያከተመ መስሏቸው በመሸበር አፈገፈጉ ። በሕቡእ የገባውን የወዝአደሩን ፓርቲ ለመበተንና ለማስቀረት ይፈልጉ ነበርና በመርሀግብሩ ላይ የተጠቀሱትን አብዮታዊ ዓላማዎችንና የፓርቲውን መፈክሮች በሚያሳፍር ሁኔታ ሽምጥጥ አድርገው ካዱ ። በዚህም የተነሳ ሜንሼቪኮች በታኞች ተብለው ይታወቃሉ ።

እንደ ሜንሼቪኮች ሳይሆን ቦልሼቪኮች በሚቀጥሉት ጥቂት አመታት ውስጥ አብዮቱ በታላቅ ግርማ እንደሚነሳ እርግጠኞች በመሆን ለዚህ አዲስ አመጽ ሠፊውን ሕዝብ የማዘጋጀቱ ተግባር የፓርቲው መሆኑን አስገነዘቡ ። የአብዮቱ መሰረታዊ ጥያቄዎች ገና መልስ አላገኙም ፤ የመሬት ከበርቴዎች መሬት ለገበሬዎች አልተሰጠም ፣ የሰራተኞች በቀን 8 የሥራ ሰዓት ገና በተግባር አልዋለም ፣ ሕዝቡ እጅግ የሚጠላው የዛሩ ፈላጭ ቆራጭ መንግስት ገና ተገርስሶ አልወደቀም ፣ ለ1905ቱ አብዮት ሕዝቡ አጥጋቢም ባይሆን በትግሉ ያገኛቸው ፖለቲካዊ መብቶች እንደገና ታፍነዋል ። ስለሆነም ለ1905ቱ አብዮት መንስኤ የነበሩት ምክንያቶች አንዳችም መፍትሔ ሳያገኙ አሁንም በሀይል ታፍነው ይገኛሉ ፤ ለዚህም ነበር ቦልሼቪኮች አዲስ አብዮታዊ አመጽ እንደሚኖር እርግጠኞች በመሆን ለመጪው አብዮት የሚዘጋጁትና የሠራተኛውን መደብ ሀይሎች የሚያሰባስቡት ።

አዲስ አብዮታዊ አመጽ በማይቀር ሁኔታ የመነሳቱን እርግጠኛነት ቦልሼቪኮች ያረጋገጡት የ1905ቱ ዓ፡ ም፡ አብዮት የሠራተኛው መደብ ለመብቶች ለሚያደርገው ተጋድሎ ሰፊ አብዮታዊ ትግል ማድረግ እንዳለበት ካስተማረው ሐቅ ነበር ። ካፒታሊስቶች በአጠቁበት በዚያ በአድሀሮት ወቅት ሠራተኞች በ1905ቱ ዓ.ም የቀሰሙትን ትምህርት ፍጹም አይረሱትም ። ሌኒን የፋብሪካ ባለቤቶች እንዴት አድርገው እንደገና እንደሚጨቁኗቸውና እንደሚያዋርዷቸው እንዲሁም « ጠብቁ ሌላ 1905 ዓ. ም ይመጣል ! » ያሉበትን የሠራተኞች ደብዳቤ ጠቅሷል ።

የቦልሼቪኮች መሠረታዊ የፖለቲካ ዓላማ በ1905 ዓ. ም ከነበሩት ዓላማዎች አልወጣም ። እነዚህም አላማዎች የዛሩን አገዛዝ መገርሰስ ፣ የቡርዧውን ዲሞክራሲያዊ አብዮት ማጠናቀቅና ወደ ሶሻሊስት አብዮት መሸጋገር ናቸው ። ለአንዲትም ደቂቃ እንኳ ቢሆን ቦልሼቪኮች ይህንን ዓላማ ዘንግተው አያውቁምና ዋነኞቹን አብዮታዊ መፈክሮች ከሰፊው ሕዝብ ፊት ለፊት ማንገባቸውን ቀጠሉ ። እነሱም ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ፣ የሰፋፊ ባለመሬቶች መሬት መወረስ ፣ በቀን 8 የሥራ ሰዓት ፣ ናቸው ።

ነገር ግን የፓርቲው ታክቲኮች አብዮቱ በመነሳሳት ላይ በነበረበት በ1905 ዓ. ም አይነት በመሆን ሊቆዩ አልቻሉም ። ለምሳሌ በመጪው ቅርብ

ጊዜዎች ውስጥ አብዮታዊ ንቅናቄው በማቆልቆል ላይ ባለበት፣ሠራተኛው መደብ በከፍተኛ ደረጃ በተዳከመበትና የጸረ-አብዮት ሀይላት ከመቼውም ጊዜ ይልቅ በተጠናከሩበት ወቅት ሠፊውን ሠራተኛ ሕዝብ ለአጠቃላይ ፖለቲካዊ የሥራ ማቆም አድማ ወይም ለትጥቃዊ አመጽ ጥሪ ማድረግ ፍጹም የሚታሰብ አይሆንም፣ፓርቲው ከመጪው አዲስ ሁኔታ ጋር ራሱን ማጣጣም አለበት። የማጥቃት ታክቲኮች በመከላከል ታክቲኮች መተካት ይኖርባቸዋል ። ሀይል የማሰባሰቡ ታክቲክ፣ካድሬዎችን ወደ ህቡእ የማስገባትና በህቡእ የፓርቲውን ተግባር የማከናወን ታክቲኮች፣ የሠራተኛውን መደብ ሕጋዊ ስራዎችን ከሚስጢራዊ ተግባሮች ጋር የማዋሀድ ታክቲኮች እናም ይህን ማከናወን መቻላቸውን ቦልሼቪኮች አረጋግጠዋል ።

« አብዮቱ ከመቀጣጠሉ ቀደም ብሎ ላሉት ረዘም ያሉ ዓመታት ውስጥ እንዴት መስራት እንዳለብን አውቀናል ። እኛ እንደአለት ጠንካራ ነን ሲሉ ያለምንም አይደለም ። ሶሻል ዲሞክራቶች የመጀመሪያው ትጥቃዊ አመጽ በመከሸፉ ተስፋ የማይቆርጥ የወዝአደር ፓርቲ ገንብተዋል» ሲል ሌኒን ጽፏል ። (የሌኒን ምርጥ ሥራዎች እንግሊዝኛ እትም መስኮ 1947 ቅጽ 1 ገጽ 467)

ቦልሼቪኮች ሕቡእ የፓርቲ ድርጅቶቻቸውን ለመጠበቅና ለማጠናከር ታላቅ ጥረት ያደርጋሉ ። ይሁን እንጂ ከዚሁ ጋር ማናቸውንም ሕጋዊ አጋጣሚዎች መጠቀም እጅግ አስፈላጊ መሆኑን በጽኑ ያምናሉ ። የሕጋዊ መድረክ ማናቸውም ቀዳዳዎች ፓርቲው ከሠፊው ሕዝብ ጋር ያለውን ግንኙነት በመጠበቅና በመንከባከብ ፓርቲውን ያጠነክራሉ ።

« በዚህ ወቅት ነበር ፓርቲያችን የዛሩን አገዛዝ በመቃወም ከሚያደርገው ግልጽ ትግል ወደ ሕቡእ( ዘወርዋራ) የትግል ዘዴ የተለወጠው ። ሕጋዊውን መድረክ ለመጠቀም የሚያስችሉ እያንዳንዱንና መላውን አጋጣሚዎች ሁሉ — ከጋራ የመረዳጃ ማኅበር እስከ ዱማው መድረክ ድረስ የተጠቀመው ከ1905ቱ የአብዮት ሽንፈት ወዲህ ወቅቱ የምናፈገፍግበት ወቅት ሆኗል ። ይህ ለውጥ( አብዮቱ የደረሰበት ደረጃ—ተርጓሚው) ሀይላችንን ለማከማቸትና የዛሩን አገዛዝ ለመቃወም የሚደረገው ትግል ከቆመበት እንደገና እንዲቀጥል ለማድረግ እንድንችል አዲስ ዓይነት የትግል ዘዴ እንድንከተል ያስገድደናል ። » (ጆሴፍ ስታሊን ፤ የአምስተኛው የፓርቲ ኩንግሬስ የጽሑፍ ዘገባ ።)

የተረፉት ሕጋዊ ድርጅቶች ለፓርቲው ሕቡእ ድርጅቶች ከለላ ከመሆናቸውም ሌላ ፓርቲው ከሰፊው ሕዝብ ጋር ያለውን ግንኙነት መጠበቂያ መንገድ በመሆን ያገለግላሉ ። ቦልሼቪኮች የህሙማን በጐ አድራጐት ማኅበር ፣ የሠራተኞች አንድነት ማኅበር ክለቦች ፣ ትምህርታዊ ማኅበሮችና ሕዝባዊ ቤቶች የመሰሉትን የሙያ ማህበራትንና ሕጋዊ ሕልውና ያላቸው ሕዝባዊ ድርጅቶች በሚገባ ተጠቅመውባቸዋል ። ቦልሼቪኮች የዛ



ሩን መንግሥትና የሕገ መንግሥታዊ ዲሞክራቶችን መመሪያ ለማጋለጥና ወዝአደሩ የገበሬውን ድጋፍ እንዲያሸንፍ ለማድረግ ሲሉ በመንግሥታዊው ዱማ ውስጥ በመሳተፍ ተጠቅመውበታል ። ሕቡዑን የፓርቲ ድርጅቶች በመጠበቃቸውና በዚህ ድርጅት ሥር ያከናወኑት ማናቸውም የፖለቲካዊ ተግባርና መልክ አቅጣጫ ፓርቲው ሀቀኛውን መሥመር እንዲያራምድና መፈንዳቱ ለማይቀረው ለአዲስ አብዮታዊ አመጽ ዝግጅት አያሌ ሀይሎች በዙሪያው ለማሰባሰብ አስችለውታል ።

ቦልሼቪኮች አብዮታዊ መስመራቸውን ሲያራምዱ በሁለት ግንባሮች እየተፋለሙ ነበር ። በፓርቲው ውስጥ ከተከሰቱት ሁለት የተለያዩ አድርባይነት—ቀንደኛ የፓርቲው ጠላቶች ከነበሩት ከበታኞችና የፓርቲውን ጠላቶች ከሸፋፈኑት ከኦትዞቪስቶች ጋር በመታገል ነበር ።

ሌኒንና ቦልሼቪኮች ይህን የበታኝነት አድርባይ ዝንባሌ በመቃወም ከቀድሞውኑ በእንጭጩ ሳለ በጽኑ ታግለውታል ።እንዲያውም ሌኒን በታኞች በፓርቲው ውስጥ ያሉ የለዘብተኛ ቡርዧ ተጠሪዎች ናቸው ይላል ።

በታህሳስ ወር 1908 ዓ. ም. የሩ. ሶ. ዲ. ሠ. ፓ አምስተኛ ጉባኤ በፓሪስ ተደረገ ። በፓርቲው ውስጥ ያለ አንድ የምሁራን ክፍል (ሜንሼቪኮች) « የሩ. ሶ. ዲ. ሠ. ፓ. ን ሕልውና ለመበተንና መርሀ ግብሩን ፣ ታክቲኰቹንና የፓርቲውን ልምድ ሽምጥጥ አድርጐ እስከ መካድ ድረስ መስዋእት በመክፈል ሕጋዊ በሆነ ቅርጸቢስ ማህበር ለመተካት በታኞች የሚያደርጉትን አሳፋሪ ተግባር በሌኒን አሳሳቢነት ጉባኤው አወገዘ ። » (የሶቪየት ሕብረት ኰሚኒስት ፓርቲ (ቦልሼቪክ) ውሳኔ ሩስያ እትም ክፍል 1 ገጽ 128)

ጉባኤው ማንኛውንም ዓይነት የበታኞች ዝንባሌ በመቃወም ጠንካራ ትግል እንዲደረግ ለመላው የፓርቲ ድርጅቶች ጥሪ አደረገ ።

ይሁን እንጂ ሜንሼቪኮች በጉባኤው ውሳኔ አልጸኑምና ከቀድሞው ይልቅ በበታኝነታቸው ፣ አብዮቱን በመክዳት ተግባራቸው ከሕገ መንግሥታዊ ዲሞክራቶች ጋር መተባበራቸውን ገፉበት ። ለዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ፣ ለ8 የሥራ ሰዓት ፣ ለትላልቅ መሬቶች መወረስ የሚታገለውን አብዮታዊ መርሀ ግብር በመክዳት ይበልጥ የአብዮቱ ጠላት መሆናቸው እየጐላና ግልጽ እየሆነ ሄደ ። የፓርቲውን መርሐ ግብርና ታክቲኮች በመክዳት ግልጽና ሕጋዊ « የሠራተኞች » ፓርቲ ሕልውና ለማግኘት የዛሩን አገዛዝ መልካም ፍቃድ የሚፈልጉ ፣ ከነርሱ ጋር እርቅ ለማድረግና ከስቶልፒን አገዛዝ ጋር ራሳቸውን ለማመሳሰል የተዘጋጁ ነበሩ ። ለዚህም ነው እነዚህ በታኞች « የስቶልፒን ሠራተኞች ፓርቲ » በመባል የሚጠሩት ።

ከአብዮቱ ግልጽ ጠላቶች ጋር ከመዋደቁ ጐን ለጐን ቦልሼቪኮች
ከአብዮቱ ግልጽ ጠላቶች ሚንሼቪኮች የሚረዱትን በዳን ፣ በኤ
በማርቶቭ ፣ በትሮትስኪና በሌሎች ሚንሼቪኮች የሚረዱትን በዳን ፣ በኤ
ክሲልሮድና በፖትሬስቭ የሚመሩ በታኞችንና አድርባይነታቸውን « በግ
ራ ለበስ » ሐረጐች የሚሸፋፍኑትን አትዞቪስቶች በጽኑ ታግለዋቸዋል ።
አትዞቪስቶች የተሰኘው ስም የሠራተኞች ተወካዮች ከመንግሥታዊው
ዱማ ወጥተው እንዲመለሱ የጠየቁና ሕጋዊ ሕልውና ባላቸው ድርጅቶች
ሁሉ መሥራታቸውን ያቋረጡ ለቀድሞ ቦልሼቪኮች የተሰጠ የመጠሪያ
ስም ነበር ። (አትዞቪ ማለት መመለስ ማለት ነው)

በ1908 ዓ. ም. የሶሻል-ዲሞክራቲክ ተወካዮች ከመንግሥታዊው
ዱማ ለቀው እንዲመለሱ ሲሉ አያሌ የቦልሼቪክ አባሎች ጥያቄ
አቀረቡ ። ስለሆነም አትዞቪስት ተብለው ተጠሩ ። አትዞቪስቶች
የራሳቸው የሆነ ቡድን (ቦግዳኖቭ ፤ ሉናቻርስኪይ ፣ አሌክሲንስኪይ
ፓክሮቪስኪይ ፣ ቡብኖቭና ሌሎችም) በመመስረት ሌኒንንና የሌኒንን
መሥመር መውጋት ጀመሩ ። አትዞቪስቶች በሠራተኞች የሙያ ማህበ
ርና በሌሎችም ሕጋዊ ሕልውና ባላቸው ማህበሮች ውስጥ መስራት
እያስፈልግም ሲሉ በግትርነት ተቃወሙ ። ይህንን በማድረጋቸው በሠራ
ተኛው ዓላማ ላይ ታላቅ ጥፋት ፈጸሙ ። አትዞቪስቶች በፓርቲውና
በሠራተኛው መደብ መሀከል ሽብልቅ በመክተት የፓርቲው አባል
ነት ከሌላቸው ከሠፊው ሕዝብ ጋር ያለውን ግንኙነት ለማስቀረት ራሳ
ቸውን በህቡእ ድርጅቶች ውስጥ መመሸግን አጥብቀው ይመርጣሉ ። አብ
ሮም ማናቸውንም ሕጋዊ ሽፋን መጠቀሙ አስፈላጊ አለመሆኑን በመና
ገር እንዲያውም ይህን ማድረጉ የሚያሰጋ ሁኔታ ነው በማለት ሽምጥጥ
አድርገው ካዱ ። አትዞቪስቶች በመንግሥታዊው ዱማ ውስጥና በዱ
ማው ምክንያት ቦልሼቪኮች የሕገ መንግሥታዊ ዲሞክራቶችንና የዛሩን
አገዛዝ እርቃኑን እንደሚያስቀሩ ፣ የገበሬዎችን ድጋፍ ለማትረፍ እንደ
ሚችሉ አልተረዱም ። አትዞቪስቶች መጪውን አዲስ አብዮት ለማካ
ሄድ የሚደረገውን የሀይል ክምችት አደናቀፉ ። ስለሆነም አትዞቪስቶች
« የውስጥ በታኞች » መሆናቸው ሕጋዊ ሕልውና ባላቸው ድርጅቶች
በሚገባ መጠቀም እንዳይቻል ከፍተኛ ጥረት አደረጉ ። በርግጥ የፓር
ቲው አባል ባልሆኑ ሰፊው ሕዝብ ላይ የወዝአደሩን መሪነት ሽምጥጥ
አድርገው በመካድ ፣ አብዮታዊ ሥራውን እርግፍ አድርገው ተውት ።

የተስፋፋው የቦልሼቪኮች ጋዜጣ ፕሮሌታሪይ የሥነ-ጽሁፍ መም
ሪያ ጉባኤ በ1909 ዓ. ም. ተጠርቶ በአትዞቪስቶች ተግባር ላይ ከተወያየ
በኋላ በጽኑ አወገዛቸው ። ቦልሼቪኮች ከአትዞቪስቶች ጋር እንዳችም
የሚያገናኛቸው ነገር አለመኖሩን በይፋ በማሳወቅ እነዚህ በታኞች ከቦ
ልሼቪክ ድርጅት ውስጥ እንዲባረሩ ተደረገ ።

መላው በታኞችና አትዞቪስቶች በወዝአደሩና በፓርቲው ውስጥ
ያሉ የንዑስ ከበርቴ ተጓዥ መንገዶኞች እንጂ ሌላ አይደሉም ። ወቅቱ ለወ



ዝአደሩ እጅግ አስቸጋሪና ከባድ በሆነበት ጊዜ የበታኞችና የአትዞቪስ
ቶች ሀቀኛ ባህርይ በተለየ መልኩ እየተገለፀ መጣ ።

## 4. ቦልሼቪኮች ከትሮትስኪዝም ጋር ያደረጉት ትግል ፣ የነሐሴው ጸረ-ፓርቲ ሕብረት

ቦልሼቪኮች የወዝአደሩን ፓርቲ ሀቀኛ መስመር ለመጠበቅ በሁለት ግንባር—ከበታኞችና ከአትዞቪስቶች—ጣምራ ትግል ሲያካሂድ ትሮትስኪ የሚንሼቪክ ደምሳሾችን በጽኑ ይደግፍ ነበር ። በዚህም ወቅት ነበር ሌኒን « ይሁዳው ትሮትስኪ » በማለት ትሮትስኪን የጠራው ። ትሮትስኪ በቬይና (አውስትሪያ) ውስጥ የጸሐፊዎች ቡድን በማዘጋጀት ወገናዊ ያልሆነ መሰል ጽሁፍ ማውጣት ጀመረ ። ይሁን እንጂ እንደ እውነቱ ከሆነ የሚንሼቪኮች ጋዜጣ እንጂ ሌላ ምንም ሊሆን አይችልም ነበር ። «ትሮትስኪይ እጅግ ከሚነገረው በላይ ራስ ወዳድና አንጃኛ በመሆን ይሰራል . . . ለፓርቲው የከንፈር ድርጐ ያበረክታል ። ነገር ግን ከማናቸውም ዓይነት አንጃኛ ይልቅ የከፋ ተግባር ይፈጽማል ።» ሲል ሌኒን በወቅቱ ጽፎ ነበር ።

በኋላም ትሮትስኪ በ1912 ዓ. ም. የነሐሴውን ሕብረት አደራጀ ። ይህ ሕብረት ማናቸውንም ጸረ-ቦልሼቪክ ቡድኖች በሌኒንና በቦልሼቪክ ፓርቲ ላይ ያተኰሩ ቀጥተኛ ዝንባሌዎች ያቀፈ ነበር ። በታኞችና አትዞቪስቶች በዚህ ጸረ-ቦልሼቪክ ህብረት ውስጥ በመሳተፍ ሕብረት ፈጠሩ ። ይህ ህብረት ያላቸውን ዝምድና በጉልህ የሚያሳይ ሲሆን ፣ ትሮትስኪና ትሮትስካይቶች( ደቀመዝሙሮቹ—ተርጓሚው) በማናቸውም መሠረታዊ ጥያቄዎች ላይ በታኝ አቋም ወሰዱ ። ይሁን እንጂ ትሮትስኪ የበታኝነት ሀቀኛ መልኩን በመሀል ሰፋሪነት ሥር በመሸፈን መሸሽግ ፈለገ ። ታዲያ ምን ይሆናል መሀል ሰፋሪነት እራሱ ታራቂነት ማለት ነውና ከቦልሼቪኮች ወይም ከሚንሼቪኮች አለመሆኑን በይፋ አሳወቀና ሁለቱን ለማስታረቅ ከፍተኛ ጥረት አደረገ ። ከዚህ ሁኔታ ጋር በማያያዝ ሌኒን ሲናገር ትሮትስኪ ከግልጽ በታኞች ይልቅ ባለጌና ጠንቀኛ ነበር። ምክንያቱም እርሱ « ከአንጃዎቹ » በላይ መሆኑን ለሠራተኛ በመስበክ ለማሳመን ይጥር ነበርና ነው ። እንደ እውነቱ ከሆነ ግን ትሮትስኪ ሚንሼቪኮች በታኞችን በጽኑ ይደግፍ ነበር ። ትሮትስካይቶች መሀል ሰፋሪነትን ያስፋፉ አይነተኛ ቡድኖኛ ነበሩ ።

« መሀል ሰፋሪነት » ይላል ጓድ ጆሴፍ ስታሊን በጽሁፉ « ፖለቲካዊ ጽንሰ ሀሳብ ነው ። ርእዮተ-ዓለሙ በአንድ ፓርቲ ውስጥ የወዛደሩን ጥቅምና ፍላጐት ለንዑስ ከበርቴው ዓላማ ጥገኛ የሚያደርግ ሲሆን ፣ ይህ ርእዮተ ዓለም ለሌኒናዊነት ባእድና አሳፋሪ ነው ። »
(ጆሴፍ ስታሊን የሌኒኒዝም ችግሮች ሩሲያ እትም ገጽ 379)

ሀ ወቅት ካሜኔቭ ፣ ዜኔቪየቭና ራይኮቭ ሌኒንን በመቃወም ትሮ
በዚህ ወቅት ካሜኔቭ ፣ ዜኔቪየቭና ራይኮቭ ሌኒንን በመቃወም ትሮ
ትስኪ ለሚያደርገው ትግል ረዳት ወኪሎች ወደመሆን ተለወጡ ።
በዜኖቪየብ ፣ በካሜኔቭ ፣ በራይኮቭና ሌሎችም ግልጽ የትሮትስኪ ተባባ
ሪዎች በሚያደርጉት እርዳታ የማእከላዊ ኰሚቴው ጠቅላላ ስብሰባ የሌ
ኒንን ዓላማ በመጻረር በጥር ወር 1910 ዓ. ም እንዲሰበሰብ ጥሪ ተደረገ ።
በዚያን ጊዜ ቦልሼቪኮች በብዛት በመታሰራቸው የተነሳ የማእከላዊ ኰ
ሚቴ አባሎች ተለዋውጠው ነበርና ዋዣቂው ክፍል ጸረ-ሌኒኒስት ውሳኔ
ለማሳለፍ በቃ።ስለሆነም በዚህ አጠቃላይ ስብሰባ ላይ የቦልሼቪኮች ጋዜጣ
የሆነው ፕሮሊታሪ (ወዝአደር) እንዲታገድና ትሮትስኪ በቬይና ለሚያት
መው ፕራቭዳ ጋዜጣ የገንዘብ ድጋፍ እንዲደረግ ተወሰነ ። ካሜኔቭ በዚ
ሀ ትሮትስኪ በሚያትመው የፕራቭዳ ጋዜጣ የሥነ ጽሑፍ መምሪያ ውስጥ
በመቀላቀልና ከዜኖቪየቭ ጋር በመሆን ጋዜጣው የማእከላዊ ኰሚቴ
ልሳን እንዲሆን ለማድረግ እጅግ ከፍተኛ ጥረት አደረጉ ።

በጥር ወር በተደረገው የማእከላዊ ኰሚቴ አጠቃላይ ስብሰባ ላይ
በታኞችና ኦትዞቪዝም እንዲወገዝ ሌኒን ብቻውን ሀሳብ በማቅረብ እነ
ዚህ በታኞች በጉባኤው ሊወገዙ በቁ ። ይሁን እንጂ ዚኖቪየቭና ካሜኔቭ
በበታኞች ላይ ይህን ያህል ትኩረት የምናደርግባቸው አይደሉም የሚለ
ውን የትሮትስኪ አባባል አነሳስተው ነበር ።

ልክ ቀደም ብሎ ሌኒን በማየት እንደተናገረው ጐሎስ ሶትቪያል-
ዲሞክራት ( የሶሻል— ዲሞክራቱ ድምጽ) የተሰኘውን የሚንሼቪኮች
አንጃ በታኝ ጋዜጣቸውን ሲያትሙ ቦልሼቪኮች ግን ማእከላዊ ኰሚቴ
በአጠቃላይ ስብሰባው ያሳለፈውን ውሳኔ በማህበር ፕሮሌታርያን ልሳን
ማውጣት አቆሙ ።

የሌኒን አቋም በሶሺያሊስት ዲሞክራት ቁጥር 11 ላይ ምርጥ ጽሁ
ፉን ባሰፈረው በጓድ ስታሊን ሙሉ ለሙሉ የተደገፈ ነበር ። የትሮትስ
ስኪን ግብረ አበሮች ባህርይ በጽኑ ባወገዘበትና በካሜኔቭ በዜኖቪየቭና
በራይኮቭ ከሀዲ ባህርይ ምክንያት በቦልሼቪክ ቡድን ውስጥ የተከሰተ
ውን ጤናማ ያልሆነ ሁኔታ መደምደሚያ መስጠት አስፈላጊ መሆኑን ባሳ
ሰበበት ጽሁፍ በፕራግ ለሚደረገው የፓርቲ ጉባኤ መደረግ ያለባቸውን
አፋጣኝ ተግባሮች ጠቆመ ። እነዚህ — አጠቃላዩን የፓርቲ ስብ
ሰባ መጥራት ሕጋዊ በሆነ መንገድ የፓርቲውን ጋዜጣ ማተምና በሩስያ
ውስጥ በሕቡእ የሚሠራ በተግባር የሚውል የፓርቲ ማእከል መመሥ
ረት ሲሆኑ ፣ የጓድ ስታሊን ጽሁፍ የተመሠረተው ሙሉ ለሙሉ ሌኒንን
በሚደግፈው በባኩ ኰሚቴ ውሳኔ ላይ ነበር ።

ከደምሳሾችና ትሮትስካይቶች እስከ ኦትዞቪስቶችና ጣኦት አማኞች
ያሉትን ጸረ-ፓርቲ ክፍሎች ብቻ አጣምሮ የያዘውን የትሮትስኪን ጸረ-
ፓርቲ የነሐሴ ሕብረት ለመቃወም ሕቡዑን የወዝአደር ፓርቲ ለመጠ
በቅና ለማጠናከር የሚፈልጉ ወገኖችን ያቀፈ የፓርቲ ሕብረት ተመስርቶ



ነበር ። ይህ ሕብረት በሌኒን የሚመራውን ቦልሼቪኮችና በፕሌክሀኖቭ
የሚመሩትን የፓርቲ ደጋፊዎች የሆኑ ጥቂት ሜንሼቪኮች የያዘ ነበር ።
በአያሌ ጥያቄዎች ላይ የሜንሼቪኮችን አቋም የሚያራምድ ራሳቸውን
ከነሐሴው ሕብረትና ከበታኞች በጥብቅ የገነጠሉ ፣ የፓርቲው ደጋፊዎች
የሆኑ ሜንሼቪኮችና ፕሌክሀኖቭን እንዲሁም ከቦልሼቪኮች ጋር እርቅ
ለማድረግ ጥረዋል ። ሌኒን የነፕሌክሀኖቭን አስተሳሰብ በመቀበልና
ጸረ-ፓርቲ ሀይላትን ለመታገል ጊዜያዊ ህብረት ፈጠረ ። እንዲህ ዓይ
ነቱ ሕብረት ለፓርቲው ታላቅ ጠቀሜታ ከመስጠቱም በላይ ለበታኞች
መቅሰፍት በመሆን አገልግሏል ።

ጓድ ስታሊን ይህንን ሕብረት በሚገባ ደግፎታል ። በዚያን ወቅት
ምንም እንኳ በግዞት ላይ ቢሆንም ለሌኒን የሚከተለውን ደብዳቤ ጽፎ
ነበር ።

« በኔ አስተሳሰብ የሕብረቱ መስመር (የሌኒንና የፕሌክሀኖቭ) አንድ
ብቸኛ የሆነ እውነት ነው ፡- 1 ይህ መስመርና ራሱ ብቻ የእውነተኛ
ፓርቲ ክፍሎችን በአንድነት እንዲሰባሰቡ ለሚሻው የሩስያ አብዮታዊ
ተግባር ፍላጐት እርኪ መልስ ይሰጣል ፤2/ ይህ መስመርና እርሱ ብቻ ፣
በሜንሼቪክ ሠራተኞችና በታኞች መሀከል ከፍተኛ ልዩነት በመፍጠር
በስተመጨረሻው የተጠቀሰውን በመነጣጠልና በማክሸፍ ሕጋዊ ድር
ጅቶችን ከበታኞች ቀንበር ሥር ነጻ የማውጣቱን ሂደት ያፋጥናል ። »
(ሌኒንና ስታሊን ሩሲያ እትም ቅጽ 1 ገጽ 529—30)

ጥበብ ለተጐናጸፈው የሚስጥራዊና የሕጋዊ ሥራዎች ቅንጅት ምስ
ጋና ይግባውና በሕጋዊ የሠራተኞች ማህበር ውስጥ ቦልሼቪኮች ጠንካራ
ሀይል ለመሆን በቁ ። ይህ የታየው በዚያን ወቅት ቦልሼቪኮች ሠራተኞች
ላይ ያሳለፉት ተጽእኖ በሕጋዊ መንገድ በተመራው የሠራተኞች ቡድ
ኖች አራት ኮንግረሶች ላይ በድንገት በተገለጸው የቦልሼቪኮች ተደማጭነት
ሲሆን ፤እነዚህ ሕዝባዊ የዩኒቨርስቲ ኮንግሬስ የሴቶች ኮንግረስ ፣ የፋብሪካ
ሀኪሞች ኮንግረስና የመጣኞች ኮንግረስ ነበሩ ። በነዚህ ኮንግረሶች
ላይ ቦልሼቪኮች ያደረጉአቸው ንግግሮች ከፍተኛ ፖለቲካዊ ጠቀሜታ
ነበሩና በመላው ሀገሪቷ አስተጋቡ ። ለምሳሌ ያህል በሕዝባዊ ዩኒቨር
ስቲ ኮንግረስ ላይ የቦልሼቪክ ተወካይ ቡድን ማናቸውንም ባሕላዊ እን
ቅስቃሴ አፍኖ የያዘውን የዛሩን መርሆ በማጋለጥና የዛሩ አገዛዝ ከስሩ
ተመንግሎ እስካልወደቀ ድረስ በሀገሪቷ ውስጥ ማናቸውም እውነተኛ
ባህላዊ እርምጃዎች እንደማይኖሩ ተከራከረ ። በፋብሪካ ሐኪሞች ኮንግ
ረስላይ የተወከሉት የሠራተኞች ተወካዮች ሠራተኛው የሚኖርበትና የሚ
ሠራበትን ለጤና ጠንቅ የሆኑ ሁኔታዎች በማንሳት የዛሩ አገዛዝ እስካ
ልተገረሰሰ ድረስ በፋብሪካ ውስጥ ጤንነት ሊጠበቅ እንደማይቻል ማጠ
ቃለያ ሰጡ ።

ቦልሼቪኮች ቀስ በቀስ ከተለያዩ ሕጋዊ ድርጅቶች ውስጥ በታኞችን
ቦልሼቪኮች ቀስ በቀስ ከተለያዩ ሕጋዊ ድርጅቶች ጋር ያደረጉት ይህ አስወጡአቸው ከፕሌክሀኖቭ የፓርቲው ደጋፊዎች ጋር ያደረጉት ይህ የተለያየ የሕብረት ግንባር ቦልሼቪኮች በእያሌ የሜንሼቪክ ሰራተኞች ድርጅቶች ውስጥ ድልን እንዲጐናጸፉ አስቻላቸው ። (በቫይቦርግ አው ራጃ ውስጥ ፤ በኢካቴሪኖስላቭ ፤ ወዘተ . . )

በዚህ እጅግ አስቸጋሪ ወቅት ሕጋዊ ሥራዎች ከሕቡእ ሥራዎች ጋር እንዴት እንደሚቀናጁ ቦልሼቪኮች መልካም ምሳሌ አኑረዋል ።

## 5. የ1912 ዓ. ም. የፕራግ የፓርቲ ጉባኤ ። ቦልሼቪኮች ራሳቸውን ነጻ ማርክሲስት ፓርቲ ስለማድረጋቸው ።

በታኞችን ፣ አትዞቪስቶችንና ትሮትስካይቶችን በመቃወም የተደረገው ፍልሚያ ፣ መላውን ቦልሼቪኮችን የማዋሀዱና ነጻ የቦልሼቪክ ፓርቲ የመ መስረቱ አፋጣኝ ግዴታ ከቦልሼቪኮች ፊት ለፊት ተጋረደ ። የዚህ ተግ ባር አስፈላጊነቱ በፓርቲው ውስጥ ሆነው ሠራተኛውን መደብ የሚከ ፋፍሉ አድርባይ ዝንባሌዎችን ድባቅ ለመምታት ብቻ ሳይሆን ፣ ሀይልን የማከማቸቱን ተግባር ለማጠናቀቅና ለአዲሱ የአብዮት ፍንዳታ ዝግጅት ለማድረግ ጭምር ነበር ።

ነገር ግን ይህ ተግባር ከመጠናቀቁ ቀደም ሲል ፓርቲው ከአድርባ ዮች ሜንሼቪኮች ራሱን ማጽዳትና ነጻ ማውጣት ነበረበት ።

ከሜንሼቪኮች ጋር በአንድ ፓርቲ ሥር እንቆያለን ማለቱ ለቦልሼ ቪኮች የሚታሰብ አለመሆኑን እንዳችም የሚጠራጠር ቦልሼቪክ አሁን አይኖርም ። በስቶልፒን የአድህሮት ወቅት ውስጥ የሜንሼቪኮች ከሀዲ ባህርይ የወዝአደሩን ፓርቲ ለመበተን አዲስ ጠጋኝ ፓርቲ ለማደራጀት ያደረጉት ከፍተኛ ጥረት ከነርሱ ጋር አቆራርጦናል ። ከሜንሼቪኮች ጋር በአንድ ፓርቲ ውስጥ በመሆን ቦልሼቪኮች በአንድም ሆነ በሌላ መንገድ ለሜንሼቪኮች ባህርይ ሞራል ሀላፊነት ተቀብለዋል ። ይሁን እንጂ እነ ርሱ ራሳቸው የፓርቲውና የሠራተኛው መደብ ከዳተኞች መሆን ካልፈ ለጉ በቀር ይህንን ጉልቶ የሚታየውን የሜንሼቪኮች ክዳት ሞራላዊ ሀላ ፊነት መቀበሉ ፍጹም የሚታሰብ አይሆንም ። በአንድ ፓርቲ ውስጥ ከሚ ንሼቪኮች ጋር አንድ መሆን የሠራተኛውን መደብና ፓርቲውን መክዳት ይሆናል ። በመቀጠልም ከሜንሼቪኮች ጋር ያለው እርግጠኛ መቆራረጥ እስከ መጨረሻው መቀጠል አለበት — መደበኛ ድርጅታዊ መነጣጠ ልና ከፓርቲው ውስጥ ሜንሼቪኮች ተለይተው መወገድ ይኖርባቸዋል።

በእንዲህ ዓይነት መንገድ ብቻ ነበር የወዝአደሩን ግንባር ቀደም ፓርቲ በአንድ መርሀ-ግብር ፣ በአንድ ታክቲኮችና በአንድ መደባዊ ድር ጅት ማደስ የሚቻለው ።



በዚህ ዓይነት መንገድ ብቻ ነበር ሜንሼቪኮች ደምስሰውት የነበረ ው እርግጠኛውን አንድነት (ቅርጻዊ ያልሆነ) እንደገና ለማስፈን የሚቻ ለው ።

ይህ ተግባር ቦልሼቪኮች ከፍተኛ ዝግጅት በሚያደርጉለት በስድስ ተኛው የፓርቲ አጠቃላይ ጉባኤ የሚከናወን መሆን ነበረበት ።

ነገር ግን ይህ የነገሩ አንድ ገጽታ ብቻ ነበር ። ከሜንሼቪኮች ጋር ግልፅ የሆነ ልዩነት በማድረግ የተለየ የቦልሼቪክ ፓርቲ መመስረቱ በእርግጥ ጠቃሚ ፖለቲካዊ ተግባር ነበር ። ይሁን እንጂ ቦልሼቪኮች ከዚህ ሌላና እጅግ ጠቃሚ የሆነ ተግባር ከፊት ለፊታቸው ተደቀነ ። የቦልሼቪኮች አይነተኛ ተግባር እንዲያው ዝም ብሎ ከሜንሼቪኮች ጋር መለያየትና ቅርጻዊ በሆነ መንገድ ራሳቸውን የተለየ ፓርቲ ማድረግ አል ነበረም ። ነገር ግን ከሁሉም በላይ ከቦልሼቪኮች ሲገነጠሉ ከምእራቡ ሶሻል ዲሞክራሲ የቀድሞ ፓርቲዎች የተለየ ፣ ከማናቸውም አድርባይ ክፍሎች የጸዳ ወዝአደሩን መርቶ ለሥልጣን ማብቃት የሚችል ፣ አዲስ ዓይነት ፓርቲ መፍጠር ነበር ።

ቦልሼቪኮችን በመታገሉ ላይ ከአክሲልሮድና ከማርቲይኖቭ እስከ ማርቶቭና ትሮትስኪ ድረስበያይነቱ ያሉ ሜንሼቪኮች ከምእራብ አውሮፓ ሶሻል ዲሞክራቶች የተዋሱትን ዘዴ በአልተለየ መንገድ ተጠቅመውበታ ል ። በሩሲያ ውስጥ እንበል እንደ ጀርመኑ ወይም እንደ ፈረንሳዩ ሶሻል ዲሞ ክራቲክ ፓርቲ የመሰለ እንዲኖር ሲሹ ቦልሼቪኮችንም ይዋጉ የነበረበት ምክንያት ከምዕራቡ ሶሻል ዲሞክራቶች የተለየና አዲስ ነገር ስለተ መለ ከቱ ነበር ። ግን እዚህ ላይ በዚያን ጊዜ የምዕራብ የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲዎች ይወክሉ የነበሩት ማንን ነበር ? ከዚህም ከዚያም የተጠራቀመን የማርክሲስትና የአድርባይ ክፍሎችን የአብዮቱ ወዳጆችና ጠላቶች የፓር ቲውን መርህ ደጋፊዎችና ተቃዋሚዎችን ሲሆን ፣ የመጀመሪያዎቹ ማለ ትም ደጋፊ የነበሩት ከኋለኞቹ ጋር በርዕዮተ አለሙ መንገድ እርቅ በመ ፈለግ ቀስ በቀስ የእነሱ ጥገኞች ለመሆን በቅተዋል ። ቦልሼቪኮች የምዕ ራብ አውሮፓን ሶሻል ዲሞክራቶችን ሲጠይቁ ከአድር ባዮች ከአብዮቱ ከዳተኞች ጋር ዕርቅ ማድረግ ለምን ሲባል ? «በፓርቲው ውስጥ ሰላምን ለማስፈን» «ለአንድነት» ሲባል ነው በማለት እነዚያ የምዕራብ ሶሻል ዲሞክራቶች ይመልሳሉ ፤ አንድነት ከማን ጋር ከአድርባዮች ጋር ? አዎ ከአድርባዮች ጋር በማለት አሁንም ለዚህ መልስ ይሰጣሉ ። በግልጽ እንደ ሚታየው እንደ እነዚህ ዓይነት ፓርቲዎች አብዮታዊ ፓርቲዎች ሊሆኑ አይችሉም ።

ከኤንግልስ ሞት በኋላ የምእራብ አውሮፓ ሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ከሶሻል አብዮት ፓርቲዎች ወደ « ሶሻል ጠጋኞች » ፓርቲዎች ሲዘቅጥ እያዩ ቦልሼቪኮች አንዳችም እርዳታ ሊያደርጉ አልቻሉምና እነዚህ እያ

ንዳንዱ ፓርቲዎች እንደ አንድ ድርጅት ከሚመራ ሀይል ወደ የራሱ ፓር
ላማዊ ቡድኖች ተቀጥላነት ከተለወጠ ቆይቷል ።

እንዲህ ያለው የፓርቲ ዝንባሌ ለወዝአደሩ መልካም አለመሆኑን
በማወታቸው ማለትም እንዲህ ዓይነቱ ፓርቲ የሠራተኛውን መደብ ወደ
አብዮት መምራት አይችልምና ቦልሼቪኮች ለመርዳት አልቻሉም ።

ቦልሼቪኮች ወዝአደሩ እንዲህ ዓይነቱ ፓርቲ አለመሻቱን ነገር ግን
የተለየ ዓይነት ፓርቲ ፣ አዲስና ሀቀኛ ማርክሲስት ፓርቲ ፣ ከአድርባዮች
ጋር የማይታረቅና በቡርዧው ላይ አብዮታዊ የሆነ ፣ በጥንካሬ የሚሠራና
አንድ ወጥ የሆነ ፣ የሶሻል አብዮት የሚያካሂድ ፣ የወዝአደሩ አምባገነ
ንነት ፓርቲን ሊሆን የሚችል እንደሚፈልግ ቢያውቁም አሁንም ይህንን
ሁኔታ ሊረዱ አልቻሉም ።

እንዲህ ዓይነቱን አዲስ ፓርቲ ነው ቦልሼቪኮች የሚፈልጉት ። እ
ናም ቦልሼቪኮች እንዲህ ዓይነቱን ፓርቲ ለመገንባት ሌት ተቀን ይጥራሉ
«ኤኮኖሚዝምን» ፣ ሚንሼቪኮችን ፣ ትሮትስካይቶችን ፣ አትዞቪስቶችንና
አያሌ ዓይነት ሀሳባውያንን እስከ ተግባራዊ ተቺዎች ድረስ በመቃወም
የተደረገው መላው የትግልታሪክ እንዲህ ዓይነቱን ፓርቲ ለመመሥረት
የተደረገ የትግል ታሪክ ነው ። ቦልሼቪኮች ለማናቸውም እውነተኛ አብዮ
ታዊ ማርክሲስት ፓርቲ እንዲኖራቸው ለሚሹ እንደ ምሳሌነት የሚያገ
ለግል አዲስ ዓይነት ፓርቲ — ቦልሼቪኮች ፓርቲ — ለመፍጠር ፈለጉ ።
ቦልሼቪኮች እንዲህ ዓይነቱን ፓርቲ ለመመስረት በቀድሞው ኢስክራ
ጊዜም እንኳ ይጥሩ ነበር ። ለዚህ ዓላማ ከማንኛውም ነገር ይልቅ በጥንካሬ
ነትና ፣ በጽኑነት ሠርተዋል ። ለዚህ ተግባር መሰረታዊውንና ወሳኙን ሚና
የተጫወቱት የሌኒን ጽሁፎች — ምን መደረግ አለበት ? ፣ ሁለት ታክቲኮች
ወዘተ . . . ነበሩ ። የሌኒን ምን መደረግ አለበት ? የሚለው መጽሀፉ
እንደዚህ ላለው ፓርቲ ርእዮተ - ዓለማዊ ዝግጅት ነበር ። የሌኒን
አንድ እርምጃ ወደፊት ፣ ሁለት እርምጃ ወደኋላ የሚለው መጽሀፉ ለእን
ዲህ ዓይነቱ ፓርቲ ድርጅታዊ ዝግጅት ነበር ። የሌኒን በዲሞክራሲያዊ
አብዮት ውስጥ የሶሻል ዲሞክራሲ ሁለት ታክቲኮች የተሰኘው መጽሀፉ
እንዲህ ላለው ፓርቲ ፖለቲካዊ ዝግጅት ነበር ። እናም በመጨረሻ የሌ
ኒን ቁስ አካላዊነትና ተግባራዊ ትችት እንዲህ ላለው ፓርቲ ንድፈ-ሀሳ
ባዊ ዝግጅት ነበር ።

በታሪክ ውስጥ ምንም ዓይነት የፖለቲካ ቡድን እንዲህ ባለ አስተ
ሳሰብ ራሱን ፓርቲ ሊያደርግ የተዘጋጀ ከቦልሼቪክ ሌላ አልነበረም ብሎ
በሙሉ ልብ መናገር ይቻላል ።

ስለሆነም ሁኔታዎቹ በሚገባ የተዘጋጁና ቦልሼቪኮች ራሳቸውን
ፓርቲ ሊያደርጉ የሚያስችላቸው የሰባ መስከ ተፈጥሮ ነበር ።



ሜንሼቪኮችን በማስወጣትና በአወቃቀሩ የተለየ አዲስ ፓርቲ ፣
(የቦልሼቪክ ፓርቲን) ለማደራጀት የተጠናቀቀውን ተግባር የሚያረጋ
ግጠው ስድስተኛው የፓርቲ ጉባኤ ነበር ።

ስድስተኛው የመላው ሩስያ ፓርቲ ጉባኤ በጥር ወር 1912 ዓ. ም.
በፕራግ ተደረገ ። ከ20 የሚበልጡ የፓርቲ ድርጅቶች ተወካዮች ተገኝ
ተው ነበር ። ጉባኤውም ጠቀሜታ የነበረው መደበኛ የፓርቲ ኮንግረስ
ሆነ ።

ተደምስሶ የነበረው የፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ መዋቅር መመለሱ
ንና ማእከላዊ ኮሚቴ መቋቋሙን ባበሰረው የጉባኤው መግለጫ ላይ የሩ
ስያ ሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ ከተመሠረተ ጊዜ ጀምሮ ካሳለፈው ትግ
ሎቹ ይልቅ የአድሀሮት ጽልመት የረበበበት የአሁኑ ወቅት እጅግ አስቸጋሪ
መሆኑን አሳሰበ ። አያሌ ስቃዮችን ቢቀበልም ፣ ከውጪና ከውስጥ ከሀ
ዲዎች ከሚዋዥቁ አድርባዮች ጠንካራ ጉዳት ቢደርስበትም እንኳ የወዝ
አደሩ ፓርቲ አንዴም ለጠላቶቹ ሳይንበረከክ ያነገበውን ሰንደቅና
ድርጅቱን ጠብቆ ቆይቷል ።

« የሶሻል ዲሞክራቲክ ፓርቲ እርማው ፣ መርሀ ግብሩና አብዮ
ታዊ ልምዱ ብቻ አይደለም የተንሰራራው ። ስቃይ ያመነመነውና ያዳ
ከመው ነገር ግን ፈጽሞ ያልወደመው ድርጅቱም ጭምር ነው ። » ሲል
የጉባኤው መግለጫ አሳወቀ ።

ጉባኤው በሩስያ ውስጥ የሠራተኛው መደብ አዲስ አመጽ የመጀመ
ሩን ምልክቶችና የፓርቲው ተግባሮች ማንሠራራቱን መዘገበ ።

ከአካባቢ ድርጅቶች የቀረበውን ዘገባ ካዳመጠ በኋላ « በሶሻል
ዲሞክራቲክ ሠራተኞች መሀከል የሕቡእ ሶሻል ዲሞክራቲክ ድርጅቶ
ችና ቡድኖች ለማጠናከር ከፍተኛ እንቅስቃሴ በማናቸውም ሥፍራ መካ
ሄድ አለበት » ሲል ባሳለፈው ውሳኔ አስገነዘበ ።

በማፈግፈግ ወቅት በስራ ላይ መዋል የሚገባቸው የቦልሼቪክ
ጠቃሚ ታክቲኮች ማለትም ሕጋዊና ሕገወጥ ሥራን በተለያዩ ሕጋዊ
የሰራተኞች ውስጥ የማዋሃዱ ተግባር በሁሉም አካባቢዎች መታየት
እንዳለበት ጉባኤው አመለከተ ።

የፕራጉ ጉባኤ ሌኒንን፣ ስታሊንን፣ አርጀኔኪድዝን፣ ስቨርድሎቭን፣ ስፓ
ዳርያንና ሌሎችንም የያዘ ቦልሼቪክ የሆነ የፓርቲ ማእከላዊ ኮሚቴ መረ
ጠ ። ጓድ ስታሊንና ስቨርድሎቭ በእስር ላይ ነበሩና ባልነበሩበት ነበር
ለማእከላዊ ኮሚቴው አባልነት የተመረጡት ። ጓድ ሌኒን የማእከላዊ
ኮሚቴ ተለዋጭ አባሎች ሆነው ከተመረጡት መሀል አንዱ ነበር ።

በሩስያ ውስጥ ለሚሠራው አብዮታዊ ተግባር መመሪያ የሚሰጥ
በጓድ ስታሊን የሚመራ ጓድ ዋይ ስቨርድሎቭ ፣ ኤስ. ስፓንዳርያን ፣ ኤስ

አርጀኒኪድዝ ፣ ኤም ፣ ካሊኒን የሚይዝ ተግባራዊ ማእከል (የሩስያ ማእ ከላዊ ኰሚቴ ቢሮ) ተቋቋመ ።

የፕራጉ ጉባኤ አድርባዮችን በመቃወም ቦልሼቪኮች ያካሄዱትን ትግል ሁሉ በመገምገም ሜንሼቪኮችን ከፓርቲው ውስጥ ለማባረር ወሰነ ።

የፕራጉ ጉባኤ ሜንሼቪኮችን ከፓርቲው ውስጥ በማስወገድ ነጻ የቦልሼቪክ ፓርቲ ሕልውናን አረጋገጠ ።

በርእዮተ-ዓለምና በድርጅት ድል በመምታትና ከፓርቲው ውስጥ በማስወገድ ቦልሼቪኮች የፓርቲው (የሩ. ሶ. ዴ. ሠ. ፓ) ቀደምት ሰንደቅ አውለበለቡ ። ስለዚህ ነው ቦልሼቪክ ፓርቲ እስከ 1918 ዓ. ም. ድረስ ራሱን የሩስያ ሶሺያል ዴሞክራቲክ የሠራተኞች ፓርቲ በማለት « ቦልሼቪክስ » የሚለውን በቅንፍ አስቀምጦ የሚጠራው ።

በ1912 ዓ. ም. መጀመሪያ ላይ የፕራጉን ጉባኤ ውጤት አስመልክቶ ሌኒን ለጐርኪ ሲጽፍ እንዲህ ብሏል ፦

« ፓርቲውንና ማእከላዊ ኰሚቴውን ለመከለስ በታች ልክስክስ ሰዎች ቢኖሩም እንኳ በመጨረሻው ለማሸነፍ በቅተናል ። እንተም ከእኛ ጋር እንደምትደሰት ተስፋ አደርጋለሁ ። (ሌኒን ስብስብ ሥራዎች ሩስያ እትም ቅጽ 29 ገጽ 9)

የፕራጉን ጉባኤ ዓይነተኛነት አስመልክቶ ጓድ ስታሊን ሲናገር ፦ « ይህ ጉባኤ በፓርቲያችን ታሪክ ውስጥ በቦልሼቪኮችና በሜንሼቪኮች መሀከል የመለያ መስመር የከለለና በመላው ሀገሪቷ ላይ ያሉትን የቦልሼቪክ ድርጅቶች በአንድ ቦልሼቪክ ፓርቲ ያዋሀደ ታላቅ ጉባኤ ነበር » (ሶ. ሕ. ኮ. ፓ. (ቦ) የአሥራ አምስተኛው ጉባኤ ላይ ሽርባንቲየም ካቀረበው ሪፖርት ሩስያ እትም ገጽ 361-62)

ሜንሼቪኮች ከተወገዱና ነጻ ቦልሼቪክ ፓርቲ ከተመሠረተ በኋላ የቦልሼቪክ ፓርቲ እጅግ ጽኑና ጠንካራ ሆነ ። ፓርቲው በውስጡ ያሉትን አድርባይ ክፍሎች በማጽዳት ተጠናከረ ። አዲሱ ዓይነት ፓርቲ ከሁለተኛው አለም አቀፍ ሶሺያል ዴሞክራቲክ ፓርቲዎች በመሠረቱ የተለየ ለአዲስ ዓይነት ፓርቲ ቦልሼቪክ አንድ ምሳሌ ሆነ ። ምንም እንኳ የሁለተኛው አለም አቀፍ ፓርቲዎች ራሳቸውን ማርክሲስት ፓርቲ ብለው ይጥሩ እንጂ እንደ እውነቱ ከሆነ በግልጽ የታወቁ አድርባዮችን ያቀፉና ሁለተኛውን ዓለም አቀፍ እንዲበክሉና እንዲንዱ የፈቀዱ ለማርክሲዝም ያልተኙ ጠላቶች ነበሩ ። በተቃራኒው ቦልሼቪኮች አድርባይነትን በመቃወም ጽኑ ትግል ያካሄዱና የወዝአደሩን ፓርቲ አድርባይ በካዮችን ያስወገዱ ብሎም አዲሱን አይነት ፓርቲ ፣ ሌኒናዊውን ፓርቲ ፣



የወዝአደሩን አምባገነንነት ለመመሥረት የበቃውን ፓርቲ የመሠረቱ ናቸው ።

በወዝአደሩ ፓርቲ ውስጥ አድርባዮች ሳይወገዱ ቀርተው ቢሆን ኖሮ ቦልሼቪክ ፓርቲ በሰፊው አውራ ጐዳና ላይ መራመድና ወዝአደሩን መምራት ፍጹም አይችልም ነበር ። ስልጣን ለመንጠቅና የወዝአደሩን አምባገነንነት ለመመስረት አይቻልም ነበር ። ከእርስ በርሱ ጦርነት በድል አድራጊነት በመውጣት ሶሻሊዝምን መገንባት ከቶም አይችልም ነበር ።

የፕራጉ ጉባኤ በመለስተኛው መርሀ-ግብር ላይ የተጠቀሱትን ዓላማዎች የፓርቲው ዋና ወቅታዊ መፈክሮች በማድረግ ወደፊት ለማራመድ ወሰነ ፣ እነዚህም ዴሞክራሲያዊ ሪፓብሊክ ፣ በቀን ስምንት የሥራ ሰዓትና ሁዳዳዊ ባለቤትነትን መውረስ ነበሩ ።

በዚህ አብዮታዊ መፈክሮች ሥር ነበር ቦልሼቪኮች ዘመቻቸውን ለአራተኛው መንግሥታዊ ዱማ ከሚደረገው ምርጫ ጋር እያይዘው ያራመዱት ።

በ1912 — 14 ዓ. ም. የተነሳውን የሰራተኛውን መደብ እንቅስቃሴ የመራው ይህ መፈክር ነበር ።

## አጭር ድርሞ ።

ከ1908—12 ዓ. ም. ድረስ ያሉት ዓመታት ለአብዮታዊው ተግባር እጅግ አስቸጋሪ የሆኑ ወቅቶች ነበሩ ። አብዮታዊው እንቅስቃሴ በማቆልቆል ላይ በነበረበትና ሰፊው ሕዝብ ድካም በተሰማበት ወቅት ቦልሼቪኮች ታክቲኰቻቸውን በመለወጥ የዛሩን አገዛዝ በመቃወም ከሚያደርጉት ቀጥተኛ ፍልሚያ ወደ ዘወርዋራ ትግል ተሸጋገሩ ። የስቶልፒን አድሀሮት በሰፈነበት እጅግ አስቸጋሪ ወቅት ቦልሼቪኮች ከሰፊው ሕዝብ ጋር ያላቸውን ግንኙነት ለመጠበቅ በጣም ትንሽ የሆኑ ሕጋዊ አጋጣሚዎችን (ከመረዳጃ ማኅበርና የሙያ ማኅበራት አንስቶ እስከ ዱማው መድረክ) ተጠቅመውበታል ። ቦልሼቪኮች ለአዲሱ አብዮታዊ እንቅስቃሴ መነሳሳት ሀይል ለማሰባሰብ ሳይታክቱ ሠርተዋል ።

የአብዮቱ ሽንፈት ባስከተለው እጅግ ከባድ የሆኑ ሁኔታዎች ማለትም የተቃዋሚ ዝንባሌዎች መነጣጠል ፣ ከአብዮቱ ጋር አለመጣጣምና ፓርቲውን የካዱ ምሁራን (በግዳኖቭ ፣ በዛሮቭና ሌሎችም) ንድፈ-ሀሳባዊ መሰረቶቹን ለመከለስ የሚያደርጉት ጥረቶች ጨመሩ ። ቦልሼቪኮች በፓርቲው ውስጥ የፓርቲውን ሰንደቅ ያልጣሉ ፣ በፓርቲው መርሀግብር ላይ ጽኑ እምነት ይዘው የቆዩና በማርክሲስት ንድፈ-ሀሳብ ላይ የተሰነዘሩትን «ትችቶች» የተከላከሉ፣(የሌኒን ቁስ አካላዊነትና ተግባራዊነት ትችት) በፓርቲው ውስጥ ያሉ አንድ ብቸኛ ሀይል ቦልሼቪኮች ብቻ ነበሩ ። በሌ

ኒን ዙሪያ የተመአከለውን የቦልሼቪኮች የአመራሩ እንብርት (Core) ፓርቲውንና አብዮታዊ መመሪያውን ለመጠበቅ እንዲችል የረዳው የአመራሩ እንብርት በማርክሲስት ሌኒንስት ርእዮተ-ዓለም የተኰተኰተና የአብዮቱን አስተሳሰብ ጠንቅቆ የተረዳ በመሆኑ ነበር ። « እኛ ከአለት ይልቅ ጠንካሮች ነን ሲሉ ለምንም ነገር አልነበረም» በማለት ቦልሼቪኮችን አስመልክቶ ሌኒን ተናግሯል ፡—

በዚያን ወቅት ሜንሼቪኮች ከአብዮቱ እጅግና በጣም ርቀው ነበር ። የወዝአደሩን ሚስጥራዊ አብዮታዊ ፓርቲ ለመበተን በማለም በታኞች ሆኑ ። እጅግ ግልጽና በማያሻማ ሁኔታ የፓርቲውን መርሀ ግብር ፣ አብዮታዊውን ግብርና የፓርቲውን መፈክሮች በመክዳት የራሳቸውን ሠራተኞች «የስቶልፒን ሠራተኞች ፓርቲ» ብለው የቀጸሉትን የራሳቸውን የጠጋኞች ፓርቲ ለማደራጀት ታላቅ ጥረት አደረጉ ። ትሮትስኪይ ለሽፋን የ« ፓርቲው አንድነት » የሚለውን መፈክር በማንሳት በታኞችን ደገፈ። ነገር ግን እንደ እውነቱ ከሆነ ግን ይህ ማለት ከበታኞች ጋር ህብረት መፍጠር ነበር ።

በሌላ በኩል ደግሞ የዛሩን አገዛዝ በአዲስና በዘወርዋራ መንገድ የመታገሉን አስፈላጊነት በቅጡ ያልተገነዘቡ አንዳንድ ቦልሼቪኮች የተገኙትን ሕጋዊ መድረኰች መጠቀም እያስፈልግምና በመንግሥታዊ ዱማ ውስጥ እንዲሳተፉ የተላኩት የሠራተኞች ተወካዮች እንዲመለሱ ሲሉ ጠየቁ ። እነዚህ አትዘቪስቶች ፓርቲው ከሰፊው ሕዝብ ጋር ያለውን ግንኙነት ወደ ማቋረጡ እያመሩና ለአዲሱ አብዮታዊ አመጽ የሚደረገውን የሀይል ክምችት እያደናቀፉ ነበር ። « ግራ » ለበስ ሀረጐችን በመሰንዘር አትዘቪስቶችም እንደ በታኞች ሁሉ የአብዮታዊውን ትግል ይዘት በፅኑ ተቃውመዋል ።

በታኞችና አትዘቪስቶች ሌኒንን በመቃወም በጋራ ሕብረት መሰረቱ ። ይህም ሕብረት የነሐሴው ሕብረት በመባል ይታወቃል ። ይህ ህብረት የተመሰረተው በትሮትስኪ ነበር ።

በታኞችንና አትዘቪስቶችን በመቃወም ባደረጉት ትግልና ከነሐሴው ሕብረት ጋር ባደረጉት ትግል ቦልሼቪኮች ሕቡዑን የወዝአደር ፓርቲ ለማጠናከርና ለመጠበቅ ችለዋል ።

የዚህ ወቅት የማይዘነጋው ቁም ነገር ( በጥር ወር 1912 ዓ. ም) በፕራግ ላይ የተደረገው የሩ. ሶ. ሠ. ፓ. ጉባኤ ነበር ። በዚህ ጉባኤ ላይ ሜንሼቪኮች ከፓርቲው እንዲወገዱ ተደረጉና በአንድ ፓርቲ ውስጥ የሜንሼቪክና የቦልሼቪክ ቅርጻዊ አንድነት ለመጨረሻው አከተመ ። ከአንድ ፖለቲካዊ ቡድን ተነስተው ቦልሼቪኮች ራሳቸውን አንድ ነጻ ፓርቲ ማለትም የሩስያ ሶሺያል ዲሞክራቲክ ፓርቲ (ቦልሼቪክ) ለማድረግ በቁ ። የፕራጉ ጉባኤ አዲሱን አይነት ፓርቲው ፣ ሌኒናዊውን ፓርቲ ፣ ቦልሼቪክ ፓርቲን አበሰረ ።



የወዝአደሩን ፓርቲ ቀንደኛ አድርባዮች ፣ ሜንሼቪኮችን የማስወገዱ ተግባር በፕራጉ ጉባኤ ላይ ውጤት ማግኘት ለፓርቲውና ለአብዮቱ ተከታይ እድገት እጅግ ጠቃሚና ወሳኝ ተጽእኖ አሳድሯል ። ቦልሼቪኮች ከሜንሼቪኮች ጋር እርቅ በመፍጠር ሠራተኛውን የካዱትን ከሀዲዎች ከፓርቲው ውስጥ ባያስወግድ ኖሮ የወዝአደሩ ፓርቲ በ1917 ዓ. ም ሰፊውን ሕዝብ ለወዝአደሩ አምባገነንነት እንዲታገሉ ለማንቀሳቀስ ባልቻለም ነበር ።

## ምእራፍ አምስት

# የቦልሼቪክ ፓርቲ—ከመጀመሪያው የኢምፔሪያሊስት ጦርነት በፊት የሠርቶ አደሩ መደብ አዲስ እንቅስቃሴ ባደረገበት ወቅት ።

(1912—1914)

### 1 ከ1912—14 ባለው ጊዜ የአብዮታዊ እንቅስቃሴ መነሳት ።

የስቶሊፒን አድሀሪ ድል በአጭሩ ተቀጨ ።ለሕዝቡ ከግርፋትና ስቅላት በስተቀር ሌላ መስጠት የማይችል መንግሥት ለረጅም ጊዜ መቆየት አይችልም ። የጭቆና እርምጃዎች በጣም የተለመዱ በመሆናቸው ሕዝቡ መፍራቱን ተወ ። አብዮቱ ከተመታ በኋላ ወዛደሩ ተሰምቶት ከነበረው ድካም አገገመ ። ሠርቶ አደሮች ትግሉን ቀጠሉ ። ቦልሼቪኮች አዲስ የአብዮት ማእበል መነሳቱ አይቀርም ሲሉ የተነበዩት እውነት መሆኑ ተረጋገጠ ። ከ1911 በፊት ሥራ ያቆሙ ሠራተኞችን ብዛት በእያንዳንዱ ዓመት ከ50,000 እስከ 60,000 የማይበልጥ ሲሆን አሁን ግን ከ100,000 በላይ ሆነ ። በጥር 1912 ፕራግ ላይ የተደረገው የፓርቲ ስብሰባ የሠርቶ አደሩ መደብ እንቅስቃሴ መጀመሩን መዘገበ ። ነገር ግን እውነተኛው አብዮታዊ እንቅስቃሴ የተጀመረው በሌና የወርቅ ማእድን ሠራተኞች በመገደላቸው የተነሳ ሰፊ ፖለቲካዊ የሥራ ማቆም አድማ በተደረገበት በሚያዚያና በግንባት 1912 ነበር ።

ሚያዚያ 4/ 1912 ፣ በሳይቤሪያ በሚገኘው የሌና ወርቅ ማእድን በተደረገው የሥራ ማቆም አድማ ወቅት በዛሩ ጸጥታ ጠባቂዎች አዛዥ ትእዛዝ ከ500 በላይ ሠርቶ አደሮች ተገደሉ ወይም ቆሰሉ ። ከአስተዳደሩ ጋር በሰላም መነጋገር የጀመሩት ያልታጠቁ የሌና ማእድን ሠራተኞች መገደል ሀገሪቱን በሞላ አነሳሳ ። ይህ የዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ አስቀያሚ አድራጐት የተፈጸመው የማእድን ሠራተኞችን አድማ አክሽፎ የሌናን ወርቅ ማእድን ባለቤቶችን ፣ የኢንግሊዝ ካፒታሊስቶችን ለማስደሰት ነበር ። የእንግሊዝ ካፒታሊስቶችና የሩሲያ ባልደረቦቻቸው ሠርቶ አደሩን በአስከፊ ሁኔታ በመበዝበዝ ከሌና የወርቅ ማእድን ከፍተኛ ትርፍ ከ7,000,000 ሩብሎች በላይ በዓመት—ያገኙ ነበር ። ለሠርቶ አደሮች የሚከፍሉት ምንዳእ አሰቃቂ ከመሆኑም በላይ የሚሰጧቸው ምግብ የበሰበሰና ለምግብነት የማያገለግል ነበር ። ጭቆናውንና ኢ-ሰብአዊነቱን መቋቋም ስላቃታቸው ስድስት ሺ የሌና ወርቅ ማእድን ሠራተኞች ሥራ አቆሙ ።

የቅዱስ ፒተርስበርግ ፣ የሞስኮና የሌሎችም የኢንዱስትሪ ማእከሎችና አካባቢዎች ወዛደሮች ለሌናው ግድያ በብዛት ሥራ በማቆም ፣ ሰላማዊ ሰልፍ በማድረግና ስብሰባዎችን በማካሄድ ተቃውሞአቸውን ገለጹ።



« በጣም ከመደንገጣችንና ከመደንዘዛችን የተነሳ ስሚታችንን ለመግለጽ አሁን ቃላት የለንም ። ምንም ዓይነት ተቃውሞ ብናደርግ ይህ በሁላችን ልብ ያለውን ቁጣ መግለጽ የሚችለው በደበዘዘ አኳኋን ብቻ ነው ። የመደብ ትግል እንጂ ፣ ሌላ የሚረዳን ነገር የለም ። እንባም ሆነ ቁጣ አይጠቅመንም ። » ሲሉ የፋብሪካዎች አንድ ቡድን ሠራተኞች በውሣኔያቸው ገለጹ ።

የዛሩ ሚኒስቴር ማካሮቭ ፣ በመንግሥቱ ሸንጎ ውስጥ ያሉ ሶሻል ዲሞክራቶች ስለ ሌናው እልቂት እንዲያስረዳ በጠየቁበት ጊዜ « እንደዚያ ነበር ፤ እንዲያም ይሆናል ! » ብሎ መልስ በመስጠቱ የሠራተኛው ቁጣ ተካረረ ። በሌና ሠራተኞች ላይ የደረሰውን አሰቃቂ እልቂት በመቃወም ሥራ ያቆሙ ሠራተኞች ቁጥር 300,000 ደረሰ ።

የሌና ድርጊቶች በስቶሊፒን አገዛዝ የተፈጠረውን « ሰላም » እንደ ማእበል አናጉት ።

ጓድ ስታሊን ይህን አስመልክቶ ፣ በ1912 አዝቤዝዳ (ኮከብ) በተባለው የቅዱስ ፒተርስበርግ የቦልሼቪክ ጋዜጣ የሚከተለውን ጽፏል ።

«የሌናው ግድያ የዝምታውን በረዶ ስለሰበረው የሕዝቡ እንቅስቃሴ ጅረት መፍሰስ ጀመረ ። በረዶው ተሰብሯል! . . . የአሁኑ አገዛዝ ወንጀሎችና ጉዳቶች በሞላ ፣ የሩስያ ከባድ መከራና ስቃይ በሞላ በአንድ ሐቅ ፣ በሌና ድርጊት ተተኮረበት ። በመሆኑም ነው ፤ የሌናው ግድያ ለሥራ ማቆምና ለሰላማዊ ሰልፍ የጥሪ ደወል ሆኖ ያገለገለው ። »

ገዳዮችና ትሮትስካይቶች አብዮቱን ለመቅበር ያደረጉት ጥረት በከንቱ ቀረ ። የሌናው ድርጊት የአብዮቱ ኃይላት ሕያው እንደሆኑ ፣ ከፍተኛ የአብዮት ኃይል በሠርቶ አደሩ መደብ ውስጥ ተከማችቶ እንዳለ አሳየ ። በ1912 ሜይ ዴይ (May Day) የሥራ ማቆም አድማ 400,000 ሠራተኞች ተሳተፉበት ። እነዚህ የሥራ ማቆም አድማዎች ከፍተኛ የፖለቲካ ጠባይ ከማዘላቸውም በላይ ዲሞክራቲክ ሪፑብሊክ ፣ 8 የሥራ ሰዓት ፣ የመሬትን መወረስ በሚጠይቅ በቦልሼቪክ መፈክር ስር የተደረጉ ነበሩ ። እነዚህ መፈክሮች ሰፊውን ሠርቶ አደር ለማስተባበር ብቻ ሳይሆን ፣ አርሶ አደሮችንና ወታደሮችንም ጭምር በፈላጭ ቆራጩ አገዛዝ ላይ ለማስነሳት የታቀዱ ነበሩ ።

« የሞላው ሩስያ ወዛደሮች በሜይ ዴይ ያደረጉት ከፍተኛ የሥራ ማቆም አድማና ከዚሁ ጋር ተያይዘው የተደረጉ ሰላማዊ ሰልፎች ፣ አብዮታዊ መግለጫዎች ፣ አብዮታዊ ንግግሮች ሩስያ በአብዮታዊ እንቅስቃሴ ወቅት ውስጥ እንደገባች በግልጽ ያሳዩ ነበር።» ሲል ሌኒን «አብዮታዊው መነሳሳት » በሚል አርእስት ጽፏል ። ( ሌኒን ስብስብ ሥራዎች የሩስያ እትም ቅጽ 15 ገጽ 533)

በሠራተኞች አብዮታዊ ወኔ በመደናገጥ በሥራ ማቆሙ እንቅስቃሴ ላይ በታኞች ብቅ አሉ ፣ የተደረገውንም እንቅስቃሴ « የሥራ ማቆም

ተስቦ » ብለው ጠሩት ። በታኞችና ግብረ አበራቸው ትሮትስኪ ፣ የወዛ
ደሩን አብዮታዊ እንቅስቃሴ « በአቢቱታ ዘመቻ » ለመተካት ሞከሩ ።
ለመንግሥቱ ዱማ የሚላክ « መብቶች » እንዲሰጡ (ማህበር የማቋቋ
ምን መብት የሚከለክለው ደንብ እንዲነሳ ፣ ሥራ የማቆም አድማ እን
ዲፈቀድ ወዘተ . . .) በሚጠይቅ ብጣሽ ማመልከቻ ላይ እንዲፈርሙ
ሠራተኞችን ጋበዙ ። በመቶ ሺ የሚቆጠሩ ሠራተኞች የቦልሼቪኮችን
አብዮታዊ መፈክር በደገፉበት ወቅት በታኞች 3100 ፊርማ ብቻ መሰ
ብሰብ ቻሉ ።

የሠርቶ አደሩ መደብ ቦልሼቪኮች ያሳዩአቸውን መንገድ ተከተሉ ።

በዚያን ወቅት፣የሀገሪቱ የምጣኔ-ሀብት ሁኔታ እንደሚከተለው
ነበር ።

ከ1910 ዓ. ም. ከዚያ በፊት ጸጥ ብሎ የነበረው የኢንዱስትሪ ቅር
ንጫፍ በሞላ ማንሰራራት ጀመረ ። በ1910 ፣ ዓ. ም. 186,000,000 ፑዶች
የነበረው የጥሬ ብረት በ1912፣256,000,000 ፑዶች በ1913፣283,000,
000 ፑዶች ደረሰ ። በ1910 ፣ 1,522,000,000 ፑዶች የነበረው የከሰል
ምርት በ1913 ፣ 2,214,000,000 ፑዶች ሆነ ።

የካፒታሊስት ኢንዱስትሪ መስፋፋት የወዛደሩ ቁጥር በፍጥነት እን
ዲያድግ አደረገ ። የኢንዱስትሪ እድገት ልዩ ገጽታው ምርት በትላልቅ ድር
ጅቶች እንዲሰባሰብ ማድረጉ ሲሆን፤በ1901 ፣ ዓ ም 500ና ከዚያ በላይ በሚ
ቆጠሩ ትላልቅ ድርጅቶች የነበረው የሠራተኛ ቁጥር ከመላው ሠራተኛ ጋር
ሲነጻጸር 46.7 በመቶ በመሆን፤በ1910 ፣ ዓ ም 54 በመቶ ወይም ከግማሽ
በላይ ሆነ ። እንዲህ ዓይነት የኢንዱስትሪ መሰባሰብ ከዚህ በፊት ያልታየ
ሲሆን ፤ በኢንዱስትሪ በጣም በበለጸጉ እንደ አሜሪካ ባሉ ካፒታሊስት
ሀገሮች እንኳን በዚያ ወቅት በትላልቅ ኢንዱስትሪዎች የተቀጠረው ሠራ
ተኛ ቁጥር አንድ ሶስተኛ ብቻ ነበር ።

የወዛደሩ ቁጥር መጨመርና በትላልቅ ድርጅቶች መሰባሰብ ፣ እንደ
የወዛደሩ ቁጥር መጨመርና በትላልቅ ድርጅቶች መሰባሰብ ፣ እንደ
ቦልሼቪክ ፓርቲ ያለ የአብዮታዊ ፓርቲ መኖር ተጨምሮበት ፣ የሩስያን
የሠርቶ አደር መደብ በሀገሪቱ የፖለቲካ ኑሮ እጅግ ከፍተኛ ኃይል እያደረ
ጉት ናቸው ። በፋብሪካዎች ይደረግ የነበረው አረመኔያዊ ብዝበዛ ፣ ከባድ
ሸክም ከሆነው ከዛሩ ወኪሎች የፖሊስ አገዛዝ ጋር ተጣምሮ ፣ ማንኛው
ንም ትልቅ የሥራ ማቆም አድማ የፖለቲካ ባሕሪይ ሰጠው ። በተጨማ
ሪም ፣ የምጣኔ-ሀብቱና የፖለቲካው ትግል መጣመር ለሰፊው ሕዝብ የሥ
ራ ማቆም አድማዎች ልዩ አብዮታዊ ኃይል ሆነ ።

በግንባር ቀደሙ አብዮታዊ የሠርቶ አደር መደብ እንቅስቃሴ ውስጥ
የቅዱስ ፒተርስበርግ ጀግና ወዛደሮች ተሰለፉ ። የባልቲክ አውራጃዎች ፣
የሞስኮና የሞስኮ አውራጃዎች ፣ የቮልጋ አካባቢና ደቡብ ሩስያ የቅዱስ
ፒተርስበርግን ምሳሌነት ተከተሉ ። በ1913 እንቅስቃሴው ወደ ምእራብ
ግዛቶች ፣ ፖላንድና ካውካሶስ ተዛመተ ። በ1912 በተደረገው የሥራ ማቆም
አድማ በመንግሥታዊ መግለጫ መሠረት 725,000 ሠራተኞች በትክክል



ግን ከአንድ ሚሊዮን በላይ ሠራተኞች ሲሳተፉ ፣ በ1913 ደግሞ በመንግ
ሥታዊ መግለጫ መሠረት 861,000 ሠራተኞች በትክክል ግን 1,272,
000 ሠራተኞች ተሳትፈዋል ። በ1914 የመጀመሪያው አጋማሽ ላይ የሥራ
ማቆም አድማ ያደረጉ ሠራተኞች ቁጥር አንድ ሚሊዮን ተኩል ደረሰ ።

በእንዲህ ዓይነት ሁኔታ በ1912—14 ያለው አብዮታዊ መነሳሳት ፣
የሥራ ማቆም አድማው እንቅስቃሴ ፣ በሀገሪቱ ውስጥ ከ1905 አብዮት
በፊት የነበረውን ዓይነት ሁኔታ ፈጠረ ።

አብዮታዊው የብዙሀን ወዛደሮች የሥራ ማቆም አድማ ለጠቅላላው
ሕዝብ አንድ ታሪካዊ ወቅት ነበር ። እነዚህ የተደረጉት በፈላጭ ቆራጩ
አገዛዝ ላይ በመሆኑ በአብዛኛው ሠራተኛ ሕዝብ ዘንድ የተደገፈ ነበር።
ባለ ፋብሪካዎች ሠራተኞችን ከሥራ በማስወጣት ተበቀሉ ። በ1913 ፣
ካፒታሊስቶች በሞስኮ ክፍለ ሀገር 50,000 የጨርቃ ጨርቅ ሠራተኞችን
በመንገድ ላይ አፈሰሱ ። በመጋቢት 1914 ዓ. ም በቅዱስ ፒተርስበርግ
ውስጥ በአንድ ቀን 70,000 ሠራተኞች ከሥራ ተባረሩ ። የሌሎች ፋብሪካ
ዎችና የቅርንጫፍ ኢንዱስትሪ ሠራተኞች የሥራ ማቆም አድማ ያደረጉ
ጓዶችን ገንዘብ በማዋጣትና የድጋፍ ሥራ ማቆም አድማ በማድረግ ረዱ
ቸው ።

በመነሳሳት ላይ ያለው የሠርቶ አደር መደብ እንቅስቃሴ ሰፊ የሥራ
ማቆም አድማ አርሶ አደሮችንም በመቀስቀስ ወደ ትግሉ ሳባቸው ። አርሶ
አደሮች እንደገና በመሬት ከበርቴዎች ላይ ተነሱ ። የመሬት ከበርቴዎችን
ንብረትና የሀብታም ገበሬዎች የእርሻ ይዞታዎች ደመሰሱ ። በ1910—
14 ባሉ ዓመታት ከ13,000 በላይ የገበሬ ተቃውሞ መነሳሳቶች ነበሩ ።

በጦር ኃይሎችም ውስጥ አብዮታዊ አመጾች በመነሣሣት ፤ በ1912
በቱርክስታን የሚገኙ ወታደሮች የትጥቅ አመጽ አደረጉ ። በባልቲክ
የጦር መርከብና በሴቫስቶፓልም አመጽ እየተጠነሰሰ ነበር ።

በቦልሼቪክ ፓርቲ የተመራው ፣ አብዮታዊ የሥራ ማቆም እንቅስ
ቃሴና ሰላማዊ ሰልፎች ፣ የሠርቶ አደሩ መደብ የሚዋጋው ለከፊል ፍላ
ጐት ፣ «ለጥገናዎች » ሳይሆን ሕዝቡ ከዛሩ አገዛዝ ነጻ እንዲወጣ መሆኑን
አሳዩ ። ሀገሪቱ ወደ አዲስ አብዮት እያመራች ሄደች ።

በ1912 ክረምት ፣ ሌኒን ወደ ሩስያ ለመቃረብ ከፋሪስ ወደ ጋሊሲያ
(ቀድሞ አውስትሪያ) ተጓዘ ። በዚህም አንድ በ1912 ዓ.ም. መጨረሻ በክራ
ኮው ውስጥ የተደረገውንና ሌለው በ1913 ዓ.ም ደግሞ በክራኮው አጠገብ
በምትገኘዋ ፓሮኒኖ በምትባለዋ ትንሽ ከተማ የተደረጉትን ሁለት የማእ
ከላዊ ኮሚቴ አባላትና የፓርቲ መሪ ሠራተኞችን ስብሰባ በሊቀመንበ
ርነት መራ ። እነዚህ ስብሰባዎች በሠርቶ አደሩ መደብ እንቅስቃሴ ዋና ዋና
ጥያቄዎች ላይ ማለትም የአብዮታዊ እንቅስቃሴ መነሳት ፣ የሥራ ማቆም
አድማዎች ፤ የፓርቲው ተግባሮች ፣ የሕቡእ ድርጅቶችን በሚለከት ረገድ
ውሳኔ አስተላለፉ ።

## 2. የቦልሼቪክ ጋዜጣ «ፕራቭዳ»፤ የቦልሼቪክ ቡድን በአራተኛው መንግሥታዊ ዱማ ።

የቦልሼቪክ ፓርቲ ድርጅቶቹን ለማጠናከርና ተጽእኖውን በሰፊው ሕዝብ ዘንድ ለማስራጨት የተጠቀመበት ኃይለኛ መሣሪያ ፕራቭዳ (እውነት) የሚባለው በቅዱስ ፒተርስበርግ እየታተመ የሚወጣው ዕለታዊ ጋዜጣ ነበር ። የዚህ ስራ ከሌኒን በተሰጠው መመሪያ መሠረት በስታሊን አልሚንስኪና ፓሌታዮቭ ተጀመረ ። ፕራቭዳ ከአዲሱ አብዮታዊ እንቅስቃሴ ጋር በአንድነት የተጀመረ የሰፊው ሠርቶ አደር መደብ ጋዜጣ ነበር። የመጀመሪያው እትም ሚያዝያ 22(ግንቦት 5 በአዲሱ አቆጣጠር)፣1912 ወጣ፣ይህ ቀን በሠርቶ አደሮች ዘንድ የተከበረ ቀን ነበር ። ለፕራቭዳ መታተም ክብር ሲባል ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ግንቦት 5 የሠርቶ አደሮች ፕሬስ (Press) ቀን ተብሎ እንዲከበር ተወሰነ ።

ከፕራቭዳ ቀደም ሲል፣ቦልሼቪኮች እዝቬዝዳ የሚባል ለነቁ ሠርቶ አደሮች የታቀደ ጋዜጣ ነበር ። በሌና ድርጊቶች ወቅት እዝቬዝዳ ከፍተኛ ሚና ተጫውቷል ። ይህ ጋዜጣ በሌኒንና በስታሊን የተጻፈና የሠርቶ አደሩን መደብ ያነቃነቁ ጥልቀት ያላቸው በርካታ የፖለቲካ ሥነ ጽሑፎች አወጣ ። ነገር ግን በመነሳት ላይ ባለው አብዮታዊ ማእበል አንጻር፣ ሳምንታዊ ጋዜጣ የቦልሼቪክ ፓርቲን ፍላጐቶች ማሟላት አይችልም ነበር። ለሰፊው ሠራተኛ ክፍል የሚያገለግል እለታዊ ሰፊ የፖለቲካ ጋዜጣ አስፈለገ ። ፕራቭዳ እንዲህ ዓይነቱ ጋዜጣ ነበር ።

ፕራቭዳ በዚህ ወቅት ከፍተኛ ግምት የሚሰጠው ልዩ ሚና ተጫውቷል።በሰፊው ሠርቶ አደር መደብ ዘንድ ለቦልሼቪዝም ድጋፍ አስገኝቷል ። ሴንሰር የማይፈቅዳቸው ጽሑፎችንና ደብዳቤዎችን በማሳተሙ የተነሳ በሚደረስበት ተከታታይ ጥቃት፣ ቅጣትና ውርስ አንጻር ፕራቭዳ መኖር የሚችለው በሺ ከሚቆጠሩ ሰርቶ አደሮች ከፍተኛ ድጋፍ ሲያገኝ ብቻ ነበር ። ፕራቭዳ የሚወድቅበትን ከፍተኛ መቀጫ መክፈል የቻለው ከሠራተኛው ከፍተኛ መዋጮ ሊያገኝ ስለቻለ ብቻ ነበር ። ንቁ ሠርቶ አደሮች ማታ ወደ ማተሚያው ቤት እየመጡ ጋዜጦችን በብዛት ይወስዱ ስለነበር ብዙውን ጊዜ የተወረሱ ጋዜጦችም ለአንባቢያን ይደርሱ ነበር ።

በሁለት ዓመት ተኩል ጊዜ ውስጥ የዛሩ መንግሥት ፕራቭዳን ስምንት ጊዜ አፍኗል ። ነገር ግን በእያንዳንዱ ጊዜ በሠርቶ አደሮች ድጋፍ ለምሣሌ፣ ዛ ፕራቭዳ (ለእውነት) ፑትፕራቭዳ ( የእውነት መንገድ)፣ ትሩዳቫያ ፕራቭዳ (የሥራ እውነት) በተሰኙ አዲስ ግን ተመሳሳይ ስሞች ወጥቷል ።

በየእለቱ በሕዝቡ ዘንድ የሚሠራጨው የፕራቭዳ ቁጥር 40,000 ሆኖ ሳለ ፤ ላች (ጮራ) የተሰኘው የሜንሼቪኮች የእለት ጋዜጣ ግን ከ15.000 እስከ 16,000 አያልፍም ነበር ።



ሠርቶ አደሮች ፕራቭዳን የራሳቸው ጋዜጣ አድርገው ይቆጥሩት፣ ይመኩበትና ጥሪውንም በደንብ ይቀበሉ ነበር ። እያንዳንዱ እትም ከአንዱ ወደ አንዱ እየተላለፈ በርካታ አንባቢያንን ያዳርስ ነበር ። የመደብ ንቃታቸውን ይቀርጽ፣ ያስተምራቸው፣ ያደራጃቸውና ለትግል ይጠራቸውም ነበር ።

ፕራቭዳ ስለምን ነበር የሚጽፈው ?

እያንዳንዱ እትም ከሠራተኞች የተላኩ ስለኑሮአቸው፣ በካፒታሊስቶች፤በአስተዳዳሪዎቻቸውና በካቦዎቻቸው ስለሚደርስባቸው አረመኔአዊ ብዝበዛና የተለያየ የጭቆናና ኢ-ሰብአዊ ድርጊት የሚያስረዱ በርካታ ደብዳቤዎችን ይዞ የሚወጣና እነዚህም ጥልቀት ያላቸውና ስለካፒታሊስት ሁኔታዎች የሚያስረዱ ነበሩ።ፕራቭዳ ብዙውን ጊዜ ሁለተኛ የሥራ የማግኘት ተስፋ በመቁረጣቸው የተነሳ ራሳቸውን ስለገደሉ ሥራ አጦችና የተራቡ ሠራተኞች ዘገባ ያቀርብ ነበር ።

ፕራቭዳ በተለያዩ ፋብሪካዎችና የኢንዱስትሪ ቅርንጫፎች ውስጥ ያሉ ሠራተኞችን ፍላጐትና ጥያቄ ይጽፋል፣ ሠራተኞቹ ለጥያቄአቸው እንዴት እንደሚዋጉም ይናገራል ። በአጠቃላይ ማንኛውም እትም በተለያዩ ፋብሪካዎች ስለተደረጉ የሥራ ማቆም አድማዎች ዘገባ ያቀርባል ። ትልልቅና የተራዘሙ የሥራ ማቆም አድማዎች ሲደረጉ ጋዜጣው የሌሎች ፋብሪካዎች ሠራተኞች የሥራ ማቆም አድማ ላደረጉት መዋጮ እንዲደረግ ለማደራጀት ይረዳል ። አንዳንድ ጊዜ በአሥር ሺ ሩብሎች የሚቆጠሩ መዋጮ ይሰበሰብ ነበር፣ ይህም አብዛኛው ሠራተኛ በቀን 70 ወይም 80 ኩፔኮች በሚያገኝበት በዚያን ጊዜ ከፍተኛ ገንዘብ ነበር ። ይህ አድራጐት በሠርቶ አደሮች መካከል ወዛደራዊ አንድነት ከመመሥረቱም በላይ ሁሉም ሠራተኞች የፍላጐት አንድነት እንዲኖራቸው አድርጓል ።

ሠራተኞች ለእያንዳንዱ የፖለቲካ ድርጊት፣ ለእያንዳንዱ ድልና ሽንፈት ደብዳቤዎችን፣ ሰላምታዎችን፣ ተቃውሞዎችን ወዘተ . . . ለፕራቭዳ በመላክ ስሜታቸውን ገልጸዋል ። ፕራቭዳ በጽሑፎቹ ስለ ሠራተኞች እንቅስቃሴ ተግባሮች ይገልጽ የነበረው ከጸና የቦልሼቪክ አቋም በመነሳት ነበር ። ሕጋዊ መድረክን የሚጠቅም ጋዜጣ በይፋ የዛሩን አገዛዝ መገርሰስ መጠየቅ አይችልም ። ሆኖም የመደብ ንቃት ያላቸው ሠርቶ አደሮች በደንብ ተረድተው ለሰፊው ሕዝብ ማስረዳት እንዲችሉ ጥቆማዎችን ያካሂድ ነበር ። ለምሣሌ ፕራቭዳ « ሙሉና ያልተሸፋፈኑ የአምስተኛ ዓመት ጥያቄዎች» ብሎ ሲጽፍ ሠርቶ አደሮች የዛሩን አገዛዝ መደምሰስ፣ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ፣የመሬት መወሰንና በቀን 8 የስራ ሰዓት የሚለው የቦልሼቪኮች መፈክር እንደሆነ ያውቁ ነበር ።

ፕራቭዳ የነቁ ሠርቶ አደሮችን በአራተኛው ሸንጐ ዋዜማ አደራጃቸው ። ከለዘቦተኛው ቡርዧ ጋር ስምምነት እንዲደረግ የሚደግፉ ፡ « የስቶሊፒን ሠራተኞች ፓርቲ» የሜንሺቪኮችን ደጋፊዎች አደገኛ አቋም አጋልጧል ። ፕራቭዳ ሠራተኞች « ሙሉና ያልተሸፋፈነ የአምስተኛውን ዓመት ጥያቄዎች « ማለትም ቦልሼቪዝምን የሚደግፉትን እንዲመርጡ ጥሪ አደርጓል ። ምርጫዎቹ ቀጥተኛ ሳይሆኑ በተለያየ ደረጃ የሚደረጉ ነበሩ ። መጀመሪያ የሠራተኞች ስብሰባዎች ተወካዮችን ይመርጣል ። እነዚህ ተወካዮች መራጮችን ይመርጡና እነዚህ መራጮች ነበሩ ለዱማው የሠርቶ አደሮችን ተወካዮች የሚመርጡት ። መራጮች በሚመረጡበት ቀን ፕራቭዳ የቦልሼቪክ እጩዎችን ስም ዝርዝር አውጥቶ ሠራተኞች እነዚህን እንዲመርጡ አሳሰበ ። የተዘረዘሩትን ሰዎች ለእሥራት አደጋ ሳያጋልጡ ቀደም ብሎ የእጩዎችን ዝርዝር ማውጣት አይቻልም ነበር ።

ፕራቭዳ የወዛደሩን ሰፊ ድርጊት ለማደራጀት ረድቷል ። በቅዱስ ፒተርስበርግ በ1914 ጸደይ ፋብሪካዎች በተዘጉበት ጊዜ የሥራ ማቆም አድማ ማድረግ የሚደገፍ ስላልነበር ፡ ፕራቭዳ ሰራተኞች በፋብሪካዎች ውስጥ ስብሰባዎችን መጥራትና በጐዳናዎች ሰላማዊ ሰልፎችን እንደማድረግ ያሉ ሌላ የትግል መልኮችን እንዲጠቀሙ ጥሪ አደረገ ። ይህ በጋዜጣው ላይ በይፋ መገለጽ አይችልም ነበር ። ግን በተወሰነ ወቅት የሥራ ማቆም አድማዎችን ፡ የተደራጁ ስብሰባዎችንና ሰላማዊ ሰልፎችን በማድረግ መተካት አለባቸው ሲል ሌኒን «የሠርቶ አደሩ እንቅስቃሴ መልኮች» በሚል ርእስ የጻፈውን የመደብ ንቃት ያላቸው ሠራተኞች ሊረዱት ችለዋል ።

በዚህ መንገድ የቦልሼቪኮች ሕቡእ አብዮታዊ ድርጊቶች በፕራቭዳ አማካይነት ሰፊውን ሠርቶ አደሮች በሕጋዊ መንገድ ከመቀስቀስና ከማደራጀት ጋር ተዋሀዱ ።

ፕራቭዳ የጻፈው ስለ ሠርቶ አደሮች አኗኗር ፡ የሥራ ማቆም አድማቸው ሰላማዊ ሰልፋቸው ብቻ ሳይሆን ስለ አርሶ አደሮች ኑሮ ሁኔታ ያሰቃያቸው ስለነበረው ረሀብ ፡ ከመሬት ከበርቴዎች ስለሚደርስባቸው ብዝበዛ ሳያሰልስ አብራርቷል ። በስቶሊፒን « ጥገናዊ ለውጥ » የተነሳ ሀብታም ገበሬዎች ከአርሶ አደሩ ጥሩውን መሬት እንዴት እንደዘረፉ አብራርቷል ። ፕራቭዳ በገጠሩ ያለውን የተስፋፋና እንገብጋቢ ብሶት የመደብ ንቃት ያላቸው ሠርቶ አደሮች እንዲረዱት አድርጓል ። የ1905 አብዮት ዓላማዎች ግባቸውን እንዳስመቱና አዲስ አብዮት በመነሳት ላይ እንደነበረ ወዛደሩን አስተምሯል ። በሁለተኛው አብዮት ወዛደሩ እርግጠኛ መሪ ሆኖ መምራት እንዳለበትና በዚህም አብዮት አብዮታዊ አርሶ አደሩን የመሰለ ኃይለኛ አጋር እንደሚኖረው አስተማረ ።



ሜንሼቪኮች ወዛደሩ ለአብዮት ኦ.ሮ.ማቲ ትእዛዝ መሠረት ከሶ ስለ ሕዝቡ ፡ ስለ አርሶ አደሩ ረሀብ ፡ ስለ ጽልመተ-ገባሊሼቪክ ቡድንርቴዎች ጭቆና ፡ እንዳያስብና « ማህበር ለማቋቋም ነጻነት » ብቻ እንዲዋጋና ይህን በሚመለከት ለዛሩ መንግሥት « አቤቱታ » እ፣ ዲያቀርብ ለማድረግ ብዙ ጣሩ ። ይህ ሜንሼቪኮች አብዮቱን ለማጥላላት ከአርሶ አደሩ ጋር አንድነት እንዳይመሠረት ለማድረግ የሚያደርጉት ስብከት ፡ የቡርዧውን ፍላጐት ለመጠበቅ የሚደረግ መሆኑንና ሠርቶ አደሩ የአርሶ አደሩን አጋርነት ካገኘ በእርግጥ ዛሩን ድል ማድረግ ስለሚችል እንደ ሜንሼቪኮች ያሉ መጥፎ እረኞች የአብዮቱ ጠላት ስለሆኑ ከመካከላቸው መንግለው እንዲያወጡ ቦልሼቪኮች ለሠርቶ አደሩ ገለጹ ።

«የአርሶ አደሩ ኑሮ» በሚለው አምዱ ፕራቭዳ ስለምን ይጽፍ ነበር?

(19)13 ዓ ም በሚመለከት ረገድ ከተጻፉ ደብዳቤዎች አንዳንድ ምሳሌዎችን እንውሰድ)

« የገጠሩ ሁኔታ » በሚል ርእስ ከሳማራ የተላከ አንድ ደብዳቤ ፡ በኖቮካስቡላት ቡጉልማ ኡዩዝድ መንደር ከአካባቢው ለሚለቁ ገበሬዎች የሚከፋፈል የወል መሬት ይለካ ከነበረ ሠራተኛ ጋር ተጋጭተዋል በመባል ከተከሰሱ 45 አርሶ አደሮች መካከል አብዛኛዎቹ የረጅም ጊዜ እሥራት እንደተበየነባቸው ያስረዳል ።

ከፕስኮቭ ግዛት የተላከ አጭር ደብዳቤ « (ዛሻላዩ ጣቢያ አጠገብ በሚገኘው) በፕሲትሳ መንደር የሚገኙ አርሶ አደሮች የገጠር ፖሊሶችን በመሣሪያ እንደተቃወሟቸው ይገልጻል ። በርካታ ሰዎች ቆስለዋል ። ግጭቱ የተደረገው በእርሻ አካባቢ በተነሳ ውዝግብ ሳቢያ ነበር ። የገጠር ፖሊሶች ወደ ፕሲትሳ ተልከዋል ፡ ምክትል ገገርውና ነገረ ፈጁ ወደ መንደሩ ጉዞ ጀምረዋል ። »

ከዑፋ ግዛት የተላከ ደብዳቤ የገበሬ ይዞታዎች በብዛት በመሸጥ ላይ መሆናቸውንና ረሀቡና አርሶ አደሮች ከመንደሩ እንዲለቁ የሚፈቅደው ደንብ ገበሬው መሬቱን በብዛት እንዲያጣ እያደረጉ መሆናቸውን ያስረዳል ። የቦሪሶቭካን መንደር እንውሰድ ። እዚህ 543 ዲሲያቲን (በሩስያ የመሬት መለኪያ) የእርሻ መሬት ነበራቸው ። በረሀቡ ጊዜ አምስት አርሶ አደሮች መሬት ሶስት ወይም አራት ጊዜ ከዚህ በላይ የሚያወጣ ሆኖ ሳለ ፡ 31 ዲሲያቲን መሬት ለአንድ ዲሲያቲን ከ25 እስከ 33 ሩብሎች በሚደርስ ሂሣብ በርካሽ ሸጡ ። በዚሁ መንደር ሰባት ገበሬዎች ደግሞ 177 ዲሲያቲን መሬት ለአንድ ዲሲያቲን ከ18 እስከ 20 ሩብሎች ሂሣብ በመውሰድ በዓመት 12 በመቶ ለመክፈል ለስድስት ዓመት በወለድ አግድ አስያዙ ። የሕዝቡ ድህነትና የአራጣው መጠን ሲታሰብ ፡ ከተበዳሪዎቹ ውስጥ ግማሹ ያህል እንኳን በስድስት ዓመት ውስጥ ይህን ያህል ከፍተኛ ገንዘብ መክፈል ስለማይችሉ ከ177 ዲሲያቲን ውስጥ ግማሹ የአራጣ አበዳሪዎቹ ንብረት ሆኖ እንደሚቀር ግልጽ ነው ።

« በሩስያ የትልልቅ መሬት ከበርቴና የትናንሽ አራሾች የመሬት ባለቤትነት » በሚል ርእስ በፕራቭዳ በወጣው ጽሑፍ ፣ በበዝባዥ መሬት ከበርቴዎች እጅ ምን ያህል ከፍተኛ የመሬት ሀብት እንዳለ ለሠርቶ አደሮችና ለአርሶ አደሮች አሳይቷል ። ሠላሳ ሺ ትልልቅ ባለመሬቶች ብቻ 70,000,000 ዲሲያቲን መሬት አላቸው ። 10,000,000 የአርሶ አደር ቤተሰቦች ይህን ያህል መሬት ብቻ ነው የነበራቸው ። አርሶ አደሮች ፣ ሀብታም ገበሬዎችን ጨምሮ እያንዳንዳቸው በአማካይ7 ዲሲያቲን መሬት ሲኖራቸው የእያንዳንዱ ትልልቅ ባለመሬት አማካይ የመሬት መጠን 2,300 ዲሲያቲን ነበር ። በተጨማሪ አምስት ሚሊዮን የትናንሽ አርሶ አደር ቤተሰቦች ፣ ግማሽ ያህሉ አርሶ አደር ማለት ነው ፣ እያንዳንዳቸው ከአንድ እስከ ሁለት ዲሲያቲን ብቻ ነው የነበራቸው ። እነዚህ አሀዞች የአርሶ አደሮች ድህነትና የረሀብ ምክንያት የመሬቱ ሥሪት እንደሆነና አርሶ አደሮች ከችግሩ ራሳቸውን ማውጣት የሚችሉት በሠርቶ አደሩ በሚመራ አብዮት ብቻ እንደሆነ በጉልህ አሳይተዋል ።

ከገጠሩ ጋር ግንኙነት ባላቸው ሠራተኞች አማካይነት ፕራቭዳ ወደ መንደሮች በመግባት በፖለቲካ የተራመዱ አርሶ አደሮችን ለአብዮታዊ ትግል አነሳሳ ።

ፕራቭዳ መሰራጨት በጀመረበት ወቅት ሕቡእ የሶሻል — ዲሞክራቲክ ድርጅቶች በጠቅላላ በቦልሼቪኮች ሥር ነበሩ ። በሌላ በኩል ግን ሕጋዊ የድርጅት መልኮች ፣ የሸንጐው ቡድን ፣ ጋዜጦች ፣ የመረዳጃ ፣ ማህበሮችን ፣ የሞያ ማህበራት ፣ የመሳሰሉት ከሜንሼቪኮች እጅ አልወጡም ነበር ። ቦልሼቪኮች በታኞችን ከሠርቶ አደሩ ሕጋዊ መድረኮች ለማባረር ቆራጥ ትግል ማካሄድ ነበረባቸው ። እድሜ ለፕራቭዳ፣ ይህ ጦርነት በድል አድራጊነት ተፈጸመ ።

ፕራቭዳ፣የፓርቲውን መርሆና ፣የሰፊውን ሠርቶ አደር መደብ አብዮታዊ ፓርቲ ለመመሥረት የትግል ማእከል ሆነ ። ፕራቭዳ ሕጋዊ መድረክ ላይ ያሉ ድርጅቶችን በቦልሼቪክ ፓርቲ ሕቡእ ማእከሎች ዙሪያ በማሰባሰብ የሠርቶ አደሩን መደብ እንቅስቃሴ ወደ አንድ ግብ ፣ ለአብዮቱ ዝግጅት ለማድረግ መራ ።

ፕራቭዳ ከሠራተኞች በብዛት ደብዳቤዎች ይደርሱታል ። በአንድ ዓመት ብቻ ከሠራተኞች የተላኩ ከአሥራ አንድ ሺ በላይ ደብዳቤዎችን አውጥቷል ። ነገር ግን ፕራቭዳ ከሠርቶ አደሩ መደብ ጋር ግንኙነት የሚያደርገው በደብዳቤ ብቻ አልነበረም ። በየቀኑ ከፋብሪካዎች የመጡ በርካታ ሠራተኞች የስነ ጽሑፍ ማዘጋጀውን ቢሮ ይጐበኛሉ ። በፕራቭዳ የሥነ ጽሑፍ ማዘጋጃ ክፍል የፓርቲው ድርጅታዊ ሥራ ከፍተኛ ትኩረት ይሰጠዋል ። እዚህ ከፓርቲ ህዋስ ተወካዮች ጋር ስብሰባዎች ይደረጋሉ ፣ በወፍጮዎችና በፋብሪካዎች ስላለው የፓርቲ ሥራ ዘገባዎች ይሰ



ማሉ ፣ ከዚህም ነበር የፓርቲው የቅዱስ ፒተርስበርግ ኮሚቴና የማእከላዊ ኮሚቴ ዘገባዎች የሚተላለፉት ።

የሠርቶ አደሩን መደብ አብዮታዊ ፓርቲ ለመመስረት ከበታኞች ጋር ለሁለት ዓመት ተኩል በተደረገው ያላሰለሰ ትግል የተነሳ፣ በ1914 ዓም ቢጋ ላይ ቦልሼቪኮች ለቦልሼቪክ ፓርቲና ለፕራቭዳ ታክቲክ የአራት አምስተኛውን የፖለቲካ ንቃት ያላቸው ሠራተኞች ድጋፍ ማግኘት ችሏል ። ለምሣሌ ፣ በ1914 ለሠራተኞች ጋዜጦች ገንዘብ ካዋጡት 7,000 የሠራተኞች ቡድኖች መካከል 5,600 ቡድኖች ለቦልሼቪኮች ሲያዋጡ 1.400 ቡድኖች ብቻ ለሜንሼቪኮች በማዋጣታቸው ይህ ሊታወቅ ተችሏል ። በሌላ በኩል ግን ሜንሼቪኮች ጋዜጦቻቸውን ለማዘጋጀት ከሚያስፈልገው ወጭ ከግማሽ በላይ የሚያዋጡ ለዘብተኛ ቡርዧና የቡርዧ ምሁራን « ሀብታም ወዳጆች» ነበሯቸው ።

በዚያን ጊዜ ቦልሼቪኮች « ፕራቭዲስቶች » ተብለው ይጠሩ ነበር። ጠቅላላው የአብዮታዊ ወዛደር ትውልድ ፣ በመጨረሻ የጥቅምቱን ሕብረተሰብአዊ አብዮት የሠራው ወዛደር የተኮተኮተው በፕራቭዳ ነበር ። ፕራቭዳ በአሥርና በመቶ ሺ በሚቆጠሩ ሠራተኞች የተደገፈ ነበር ። በአብዮታዊ እንቅስቃሴው ወቅት (1912—14) የቦልሼቪክ ፓርቲ ጠንካራ መሠረት ፣ በኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት ጊዜ የዛሩ አገዛዝ ጥቃት ሊያጠፋው ያልቻለ መሠረት ተጣለ ።

« የ1912 ፕራቭዳ በ1917 ቦልሼቪዝም እንዲያሸንፍ የመሠረት ድንጋይ የተጣለበት ነበር ። » (ስታሊን)

ሌላው ሕጋዊ መድረኩን ይጠቀም የነበረው የፓርቲ ክፍል በአራተኛው መንግሥታዊ ሸንጐ ውስጥ የሚገኘው የቦልሼቪክ ቡድን ነበር።

በ1912 መንግሥቱ ለአራተኛው ሸንጐ ምርጫ እንዲካሄድ ወሰነ። ፓርቲያችን በምርጫው መሳተፍ በጣም ጠቃሚ መሆኑን ተረዳ ። የሸንጐው ሶሻል ዲሞክራቲክ ቡድንና ፕራቭዳ በአገር አቀፍ ደረጃ በሰፊው ሕዝብ መካከል አብዮታዊ ሥራዎችን የሚያከናውኑ የቦልሼቪክ ፓርቲ ዋነኛ መሠረቶች ነበሩ ።

የቦልሼቪክ ፓርቲ ፣ በሸንጐው ምርጫ የመንግሥቱን ፓርቲዎችና ለዘብተኛ ቡርዧውን (ሕገመንግሥታዊ ዲሞክራቶችን) እየተቃወመ በራሱ መፈክር ሥር ራሱን ችሎ ተሳተፈ ። በምርጫው ውድድር ወቅት የቦልሼቪኮች መፈክር ዲሞክራቲክ ሪፐብሊክ ፣ በቀን 8 የሥራ ሰዓትና የሁዳድ ባለቤትነትን ማስቀረት የሚል ነበር ።

የአራተኛው ሸንጐ ምርጫ በ1912 በልግ ተካሄደ ። በጥቅምት መጀመሪያ ላይ ፣ መንግሥቱ ፣ በቅዱስ ፒተርስበርግ ባለው የምርጫ ሂደት ስላልተደሰተ በብዙ ትላልቅ ፋብሪካዎች በሠርቶ አደሩ የምርጫ መብት

ውስጥ ጣልቃ ሊገባ ሞከረ ። ይህን በመቃወም ፣ የፓርቲው የቅዱስ ፒተርስበርግ ኮሚቴ ፣ በስታሊን አሳሳቢነት የትላልቅ ፋብሪካዎች ሠራተኞች የአንድ ቀን የሥራ ማቆም አድማ እንዲያደርጉ ጥሪ አቀረበ ። በእስቸጋሪ ሁኔታ ላይ በመውደቁ የተነሳ ፣ መንግሥቱ ከሁኔታው እንዲቆጠብ ተገደደና ሠራተኞች የፈለጉትን መረጡ ። አብዛኛው ሠርቶ አደር ለወኪሎቻቸውና ለሸንጎ አባላት በስታሊን የረቀቀው ኃላፊነት እንዲሰጥ መረጠ ። « የቅዱስ ፒተርስበርግ ሠርቶ አደሮች ለሠራተኛው የሸንጎ አባላት የሰጡት ኃላፊነት » በ1905 ሳይከናወን ስለቀረው ሥራ ጥሪ ያደርጋል ።

« እኛ እንደምንገምተው » ይላል የተሰጠው ኃላፊነት « ሩስያ ምናልባት ከ1905 የባሰ ሊሆን በሚችል የሰፊው ሕዝብ እንቅስቃሴ ዋዜማ ላይ ናት . . . በ1905 እንደሆነው ሁሉ በእነዚህ እንቅስቃሴዎች ግንባር እኛ የሩስያ ወዛደሮች በሩስያ ሕብረተሰብ ውስጥ እጅግ የተራመድን መደብ እንሆናለን ። ብቸኛ አጋሩም በሩስያ እርነት እጅግ የሚደሰተው ጭቁኑ አርሶ አደር ይሆናል ። »

የሕዝቡ የወደፊት ድርጊት በሁለት ግንባሮች የሚካሄድ የትግል መልክ — በዛሩ አገዛዝ ላይና ከዛሩ አገዛዝ ጋር ለመስማማት በሚፈልገው ለዘብተኛ ቡርዧ ላይ እንዲሆን አሳስቧል ።

ሌኒን ሠርቶ አደሩን ለአብዮታዊ ትግል ለሚጋብዘው ኃላፊነት ከፍተኛ ግምት ሰጥቶታል ። ሠርቶ አደሮች በአስተላለፉት ውሳኔ ይህን ጥሪ እንደተቀበሉ ገልጸዋል ።

ቦልሼቪኮች በምርጫው ድል አድርገው ጓድ ባዳዬቭ ለሸንጎው በቅዱስ ፒተርስበርግ ሠራተኞች ተመረጠ ።

ለሸንጎው በተደረገው ምርጫ ሠርቶ አደሮች ከሌላው የሕብረተሰብ ክፍል በተለዩ ሁኔታ ነበር ድምጽ የሰጡት ( ይህ የሠርቶ አደሮች ክፍል በመባል ይታወቃል) ። ከሠራተኛው ክፍል ከተመረጡት ዘጠኝ የሸንጎ አባላት ስድስቱ ፤ ባዳዬቭ ፣ ፔትሮቭስኪ ሙራኖቭ ፤ ሣሞይሎቭ ፤ ሻጉቭና ማሊኖቭስኪ የቦልሼቪክ ፓርቲ አባል ነበሩ (የኋለኛው ወደ ኋላ ሰላይ ሆኖ ተገኘ) ። የቦልሼቪክ ተወካዮች የተመረጡት ከአራት አምስተኛ ያላነሱ የሠርቶ አደር መደቦች ከሚገኙባቸው ታላላቅ የኢንዱስትሪ አካባቢዎችነበር ። በሌላ በኩል ለሸንጎው የተመረጡ በርካታ በታኞች ከሠራተኛው ክፍል ኃላፊነት አልተሰጣቸውም ፣ ማለትም በሠራተኞች አልተመረጡም ነበር ። የዚህም ውጤት በሸንጎው ውስጥ ከስድስት ቦልሼቪኮች ጋር ሲነጻጸር ሰባት በታኞች መኖራቸው ነበር ። በመጀመሪያ ቦልሼቪኮችና በታኞች በሸንጎው ውስጥ በጋራ የሶሻል ዲሞክራቲክ ቡድን መሠረቱ በጥቅምት 1913 ፣ የቦልሼቪኮችን አብዮታዊ ሥራ ካደናቀፉት በታኞች ጋር ቆራጥ ትግል ካካሄደ በኋላ ፣



የቦልሼቪክ ተወካዮች በፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ ትእዛዝ መሠረት ከሶሻል ዲሞክራቲክ ቡድን ወጥተው ራሱን የቻለ የቦልሼቪክ ቡድን መሠረቱ ።

የቦልሼቪክ ተወካዮች በሸንጎው ውስጥ ፈላጭ ቆራጩን ሥርዓት በማጋለጥና በሠራተኞች ላይ ስለሚደረገው ጭቆናና በሠራተኛው ሕዝብ ላይ ካፒታሊስቶች ስለሚያደርጉት ኢ-ሰብአዊ ብዝበዛ እንዲያስረዳ መንግሥቱን በመጠየቅ አብዮታዊ ንግግር አደረጉ ።

በዱማው ውስጥ ስለ ገጠሩ ጥያቄም ፣ አርሶ አደሮች የመሬት ከበርቴዎችን እንዲዋጉ ጥሪ በማድረግ ጉልተ-ሁዳድ እንዲወረስና ለአርሶ አደሩ እንዲሰጥ የማይደግፉትን ሕገ-መንግሥታዊ ዲሞክራቲክ ፓርቲን አጋለጡ ።

ቦልሼቪኮች ለመንግሥቱ ሸንጎ በቀን 8 የሥራ ሰዓት እንዲታወጅ የሚያሳስብ የሕግ ረቂቅ አቀረቡ ። በእርግጥ ይህ በእነዚህ ጽልመተ-መቶዎች ሸንጎ ሊጸድቅ አልቻለም ፣ ግን ከፍተኛ ቅስቀሳ ማድረግ ችሏል ።

በዱማው ውስጥ ያለው የቦልሼቪክ ቡድን መመሪያ ከሚያገኙት ከፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴና ከሌኒን ጋር የቀረበ ግንኙነት ነበራቸው ። እነዚህ ጓድ ስታሊን ቅዱስ ፒተርስበርግ ይኖር በነበረበት ወቅት በቀጥታ ይመሩ የነበሩት በሱ ነበር ።

የቦልሼቪክ ተወካዮች ራሳቸውን በዱማው ውስጥ ብቻ ሳይወስኑ በዱማው ውጭም ከፍተኛ ሥራ ያከናውኑ ነበር ። ወፍጮዎችንና ፋብሪካዎችን ይጎበኛሉ ፣ በሠርቶ አደር ማእከሎች እየተዘዋወሩ ንግግሮች ያደርጋሉ ፣ የፓርቲውን ውሣኔ የሚያስረዱበት የምስጢር ስብሰባ ያዘጋጃሉ ፣ አዲስ የፓርቲ ድርጅቶችም ይመሠርታሉ ። ተወካዮች ሕጋዊ ድርጊታቸውን ከሕቡእ ፣ ምስጢራዊ አሠራር ጋር በብልሀት አጣምረው ሠርተዋል ።

## 3. በሕጋዊ ድርጅቶች ውስጥ የቦልሼቪኮች ድል መቀዳጀት ፤ የአብዮታዊ እንቅስቃሴ ባለማቋረጥ መነሳሳት ፤ የኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት ዋዜማ ፤

የቦልሼቪክ ፓርቲ በዚህ ወቅት በሁሉም የወዛደሩ መደብ ትግል መልክ ምሣሌ ሆነ ። ሕቡእ ድርጅት መሠረተ ። የምስጢር ጽሁፎች አሳተመ ። በሰፊው ሕዝብ ውስጥ አብዮታዊ ሥራ በምስጢር አካሄደ ። ቀስ በቀስም በሕጋዊ የሠርቶ አደሩ መደብ ድርጅቶች ውስጥ አመራሩን ያዘ። ፓርቲው በሙያ ማህበራት ውስጥ አመራር ለመያዝና በሕዝብ ምክር ቤት በዩኒቨርሲቲ የማታ ትምህርት ክፍል ፣ በክበቦችና በበጐ አድራጐት ማህበሮች ሁሉ ተፅዕኖ ለማሳደር ጥረት አድርጓል ፣ እነዚህ ህጋዊ ድርጅቶች ለረጅም ጊዜ የበታኞች መጠለያ በመሆን አገልግለዋል ። ቦልሼቪኮች

ሕጋዊ ማሕበራትን የፓርቲያችን ጠንካራ ድጋፍ ለማድረግ በኃይል መታገል ጀመሩ ። ሕቡእና ሕጋዊ ሥራዎችን በብልሀት በማጣመር ቦልሼቪኮች በሁለቱ ዋና ከተሞች ፣ በቅዱስ ፒተርስበርግና በሞስኮ የሚገኙትን የአብዛኛዎችን የሙያ ማሕበራት ድርጅቶች ድጋፍ ማግኘት ችለዋል ። በተለይ በ1913 በቅዱስ ፒተርስበርግ የሚገኙ የብረታ ብረት ሠራተኞች የሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴ በሚመርጡበት ወቅት የተገኘው ድል ከፍተኛ ነበር ፣ በስብሰባው ላይ ከተገኙት 3,000 የብረታ ብረት ሠራተኞች መካከል 150 ብቻ ለበታኞች ድምጽ ሰጡ ።

በአራተኛው ዱማ ውስጥ እንደሚገኘው እንደ ሶሻል ዲሞክራቲክ ቡድን ያለ እጅግ ከፍተኛ ሕጋዊ ድርጅትም ተመሳሳይ ነበር ማለት ይቻላል ። ምንም እንኳን ዱማው ውስጥ ሜንሼቪኮች ሰባት ተወካይ ሲኖራቸው ቦልሼቪኮች ስድስት ቢኖራቸውም ፣ በብዛት የሠርቶ አደር መደብ ካልሆኑ ወረዳዎች የተመረጡት ሜንሼቪኮች አንድ አምስተኛውን ሠርቶ አደር ብቻ ሲወክሉ ፣ ከሀገሪቱ ዋና የኢንዱስትሪ ማእከሎች (ቅዱስ ፒተርስበርግ፣ ሞስኮ ፣ ኢቫኖቮ—ቮዝኔሴንስክ ፣ ኮስትሮማ ፣ አካቴሪኖስላቭና ካርኮቭ ) የተመረጡት ቦልሼቪኮች የሀገሪቱን አራት አምስተኛ የሠርቶ አደር መደብ ይወክሉ ነበር ። ሠርቶ አደሮች የራሳቸው አድርገው የሚቆጥሩት የነበረው ስድስቱን ቦልሼቪኮች (በዲየቭተሮቭስኪና ሌሎችን) እንጂ ሰባቱን ሜንሼቪኮች አልነበረም ።

የዛሩ መንግሥት ከሚያደርስበት አረመኔአዊ ጥቃትና ከበታኞችና ከትሮትስካይቶች ከሚሰነዘርበት የስም ማጉደፍ ዘመቻ አንጻር የቦልሼቪክ ፓርቲ የሕጋዊ ድርጅቶችን ድጋፍ ማግኘት የቻለው ሕቡእ ፓርቲውን መጠበቅ ስለቻለና አባሎቹን ጥብቅ ዲሲፕሊን እንዲያደርጉ ማድረግ ስለቻለ፣የሠርቶ አደሩን መደብ ፍላጐት በቆራጥነት ስለጠበቀ፣ ከሰፊው ሕዝብ ጋር የጠበቀ ግንኙነት ሊጠብቅ በመቻሉና ከሠርቶ አደሩ መደብ እንቅስቃሴ ጠላቶች ጋር የማይታረቅ ትግል በማካሄዱ ነው ።

ስለሆነም በሕጋዊ ድርጅቶች ውስጥ የቦልሼቪኮች ድል ማድረግና የሜንሼቪኮች ድል መመታት በሁሉም መስመር እያደገ ሄደ ። ከዱማው መድረክ ከሚደረገው ቅስቀሳም ሆነ ከሠራተኛ ጋዜጦች እንዲሁም በሌሎችም ሕጋዊ ድርጅቶች ሜንሼቪኮች እንዲተሩ ተገደዱ ። አብዮታዊው እንቅስቃሴ ሜንሼቪኮችን ጠራርጐ ከቦልሼቪኮች ዙርያ የተሰበሰበውን የሠርቶ አደሩን መደብ ጠንካራ ድጋፍ አገኘ ።

ሁሉንም ከፍተኛ ለማድረግ ፣ ሜንሼቪኮች የብሔርን ጥያቄ በሚመለከት እርቃናቸውን ቀሩ ። በሩስያ ጠረፎች አካባቢ የሚገኙ አብዮታዊ እንቅስቃሴዎች የብሔርን ጥያቄ በሚመለከት ግልጽ መርሐ ግብር ፈለጉ ፤ ሜንሼቪኮች ግን ይህን በሚመለከት ማንንም ከማያረካው ከቡንዲስቶች « ባሕላዊ አውቶኖሚ » በስተቀር ሌላ አልነበራቸውም ። በብሔር ጥያቄ



ላይ በጓድ ስታሊን ጽሑፍ « ማርክሲዝምና የብሔር ጥያቄ » እንዲሁም «የብሔሮች የራስን እድል በራስ የመወሰን መብትና» «በብሔር ጥያቄ ላይ አንገብጋቢ ማስታወሻዎች» በሚሉት በሌኒን ጽሑፎች እንደተገለጸው የቦልሼቪክ ፓርቲ ብቻ ነበር ማርክሲስት መርሐ ግብር የነበረው ።

ሜንሼቪኮች እንዲህ ዓይነቱ ሽንፈት ከደረሰባቸው በኋላ የነሐሴው ቡድን መንኰታኰት መጀመሩ አስደናቂ አልነበረም ። ከተለያዩ ክፍሎች የተመሰረተ በመሆኑ የቦልሼቪኮችን ኃይል መቋቋም ስላልቻለ መፈረካከስ ጀመረ ። ቦልሼቪዝምን ለመዋጋት የተመሠረተው የነሐሴው ቡድን በቦልሼቪኮች ክርን ተንኳኮተ ። መጀመሪያ ከቡድኑ የወጡት ከፔሪዩዳይቶች (ቦግዳኖቭ ፣ ሊናቻሪስኪና ሌሎች) ሲሆኑ ፣ ቀጥሎ ሊቶች ፣ ተከታትሎም የተቀሩት ተበታተኑ ።

ከቦልሼቪኮች ጋር ባደረጉት ትግል በመሸነፋቸው የተነሳ ደምሳሾች ሁለተኛው ዓለም አቀፍ እርዳታ እንዲያደርግላቸው ጠየቁ ። ሁለተኛው ዓለም አቀፍም ሊረዳቸው ቀረበ ። « በፓርቲው ውስጥ ሰላም » ለመመስረት ፣ በቦልሼቪኮችና በሜንሼቪኮች መካከል « አስታራቂ » ነን በሚል ስም ሁለተኛው ዓለም አቀፍ ቦልሼቪኮች የደምሳሾችን ታራቂ ፖሊሲ መተቸታቸውን እንዲያቆሙ ጠየቁት ። ቦልሼቪኮች ግን የማይታረቁ ነበሩ ፣ የአድር ባይን ሁለተኛው ዓለም አቀፍ ውሣኔ ለመቀበልና ስምምነት ለማድረግ ፈቃደኛ ሳይሆኑ ቀሩ ።

የቦልሼቪኮች ድል ድንገተኛ አልነበረም ፣ ሊሆንም አይችልም ነበር ። ድንገተኛ ያልሆነው ቦልሼቪኮች ብቻ ማርክሲስት ንድፈ-ሐሳብ ፣ ግልጽ መርሐ-ግብርና በጦርነት የጠነከረና የተፈተነ አብዮታዊ የወዛደር ፓርቲ ስላላቸው ሳይሆን ፣ የቦልሼቪኮች ድል በመነሳሳት ላይ ያለውን የአብዮት ማእበልም ስላንጸባረቀ ነው ።

የሠርቶ አደሩ አብዮታዊ እንቅስቃሴ ከከተማ ወደ ከተማና ከአካባቢ ወደ አካባቢ እየተሰራጨ በፍጥነት አደገ ። በ1914 መጀመሪያ ላይ ሠርቶ አደሮች ያደረጓቸው የሥራ ማቆም አድማዎች ፣ ለእንቅስቃሴው ድጋፍ ሰጭ ከመሆን አልፈው ከፍተኛ ደረጃ ላይ ደረሱ ። ይበልጥ ቆራጥና ከምን ጊዜውም የበለጠ ሠርቶ አደሮችን ያቀፉ ሆኑ ። በጥር 9 ፣ 250,000 ሠርቶ አደሮች ሥራ አቆሙ ፣ ከነዚህ ውስጥ 140,000 በቅዱስ ፒተርስበርግ የሚገኙ ነበሩ ። በግንቦት 1 ፣ ከግማሽ ሚሊዮን በላይ ሥራ ሲያቆሙ ፣ ከነዚህ ውስጥ ከ250,000 በላይ በፒተርስበርግ ነበር ። ሠርቶ አደሮች በአድማው ከሚገመተው በላይ ቆራጥነት አሳዩ ። በቅዱስ ፒተርስበርግ በኦቡኮቭ ሥራዎች የተደረገው የሥራ ማቆም አድማ ከሁለት ወር በላይ ሲቆይ ፣ በሌስነር ሥራዎች የተደረገው ደግሞ ለሶስት ወራት ቆይቷል ። በቅዱስ ፒተርስበርግ በሚገኙ በርካታ ፋብሪካዎች በሠራተኞች ላይ ይደረግ የነበረው ጠቅላላ ግፍ በሰላማዊ ሰልፍ ለተደገፈው የ115,000 ሠርቶ አደሮች ሥራ ማቆም አድማ መንስኤ ነበር ። እንቅስቃሴው

መስራጨት ጀመረ ። በ1914 መጀመሪያው አጋማሽ ላይ (የሐምሌን መጀመሪያ ጨምሮ) በጠቅላላው 1,425,000 ሠርቶ አደሮች በሥራ ማቆም አድማዎች ተሳትፈዋል ።

በግንቦት ፣ በባኩ ያሉ የዘይት ሠራተኞች ያደረጉት ጠቅላላ የሥራ ማቆም አድማ የጠቅላላውን የሩስያ ወዛደሮች ስሜት ቀሰቀሰ ። የሥራ ማቆም አድማ የተደረገው በተደራጀ መልክ ነበር ። ሰኔ 20 ቀን በባኩ 20,000 ሠራተኞች ሰላማዊ ሰልፍ አደረጉ ። በባኩ ሠራተኞች ላይ ፖሊስ አሰቃቂ እርምጃ ወሰደ ። አድራጐቱን በመቃወምና ከባኩ ሠራተኞች ጋር ያላቸውን አንድነት ለመግለጽ በሞስኮ የሥራ ማቆም አድማ ተደረገ ፣ ወደ ሌሎችም ከተሞች ተሠራጨ ።

ሐምሌ 3 ቀን በቅዱስ ፒተርስበርግ በሚገኘው የፑቲሎቭ ሥራዎች ከባኩው ሥራ ማቆም ጋር የተያያዘ ስብሰባ ተደረገ ። ፖሊስ በሠራተኞች ላይ ተኩስ ከፈተ ። የቅዱስ ፒተርስበርግ ወዛደሮች በቁጣ ማእበል ተጥለቀለቁ ። ሐምሌ 4 ቀን በቅዱስ ፒተርስበርግ የፓርቲ ኮሚቴ ጥሪ መሠረት 90,000 ሠራተኞች ድርጊቱን በመቃወም ሥራ አቆሙ ። ቁጥሩ በሐምሌ 7 ወደ 130,000 ፣ በሐምሌ 8 ወደ 150,000 እንዲሁም በሐምሌ 11 ላይ ወደ 20,000 አሸቀበ ።

በሁሉም ፋብሪካዎች ሁከት ተስፋፋ ፣ በየቦታው ስብሰባዎችና ትእይንተ ሕዝቦች ይደረጉ ጀመር ። ሠራተኞች በምሽጐች ላይ ድንጋይ እስከ መወርወር ደረሱ ። በባኩና ባሉድዝም ምሽጐች ተሠሩ ። በብዙ ስፍራዎች ፖሊስ በሠራተኞች ላይ ተኩስ ከፈተ ። መንግሥቱ ንቅናቄውን ለመግታት « አስቸኳይ » እርምጃዎች ወሰደ ፣ ዋና ከተማዋ የጦር ሠፈር ሆነች ፣ ፕራቭዳ ታፈነ ።

ነገር ግን በዚህ ወቅት ዓለም አቀፋዊ ግምት የሚሰጠው አዲስ ሁኔታ ፣ በመድረክ ላይ ብቅ አለ ። ሁኔታው የድርጊቶችን ጠቅላላ ሂደት የለወጠው የኢምፔሪያሊስት ጦርነት ነበር ። በሐምሌው አብዮታዊ እድገት ወቅት ነበር ፣ የፈረንሳይ ፕሬዚዳንት ፓይንኬ ፣ ወደፊት ስለሚደረገው ጦርነት ከዛሩ ጋር ለመነጋገር ቅዱስ ፒተርስበርግ የገባው ። ከጥቂት ቀናት በኋላ ጀርመን በሩስያ ላይ ጦርነት አወጀች ። የዛሩ መንግሥት የቦልሼቪክ ድርጅቶችን ለመደምሰስና የሠርቶ አደሩን መደብ እንቅስቃሴ ለመምታት በጦርነቱ ተጠቀመ ። የአብዮቱ እርምጃ ለዛሩ ከአብዮት መዳኛ በሆነው በዓለም ጦርነት ተቋረጠ ።

## አጭር ድርሞ

በአዲሱ አብዮታዊ መነሳሳት ወቅት (1912—14) ፤ የቦልሼቪክ ፓርቲ የሠርቶ አደሩን መደብ እንቅስቃሴ በቦልሼቪክ መፈክር ስር ወደ አዲስ አብዮት መራ ። ፓርቲው ሕቡእና ሕጋዊ ሥራዎችን ማቀናጀት ችሏል ። የበታኞችና የግብረ አበሮቻቸውን — የትሮትስካይቶችንና ኦትዞቪስቶችን — ተቃውሞ በመምታት ፓርቲው በሁሉም ሕጋዊ የእንቅስቃሴ መልኮች አመራሩን መያዝና ሕጋዊ ድርጅቶችን ለአብዮታዊ ሥራው መሠረት ማድረግ ችሏል ።

በሠራተኛው መደብ እንቅስቃሴ ውስጥ የሚገኙትን የሠርቶ አደሩ መደብ ጠላቶችንና ወኪሎቻቸውን በመዋጋት ፣ ፓርቲው አባሎቹን አጠናክሮ ከሠራተኛው መደብ ጋር ያለውን ግንኙነት አስፋፍቷል ። የመንግሥቱን ዱማ ለአብዮታዊ ቅስቀሳ ሥራ በሰፊው በመጠቀምና የሰፊውን ሠርቶ አደር ልሣን ፣ ፕራቭዳን በመመስረት ፣ ፓርቲው አዲሱን አብዮታዊ ትውልድ ፣—ፕራቭዲስቶችን አሰልጥኗል ። በኢምፔሪያሊስት ጦርነት ወቅት ይህ የሠርቶ አደሩ ክፍል ለዓለም አቀፋዊነትና ለወዛደሩ አብዮት እርማ ታማኝ ሆኖ ቆይቷል ። በመጨረሻም በጥቅምቱ 1917 አብዮት ጊዜ የቦልሼቪክን ፓርቲ ማእከል መስርቷል ።

በኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት ዋዜማ ፓርቲው የሠርቶ አደሩን መደብ በአብዮታዊ ድርጊቱ መርቷል ። እነዚህ በኢምፔሪያሊስት ጦርነት ለጊዜው የተቋረጡና ከሶስቱ ዓመት በኋላ የዛሩን መገርሰስ ያስከተሉ ግንባር ቀደም ሥራዎች ነበሩ ። የቦልሼቪክ ፓርቲ አስቸጋሪውን የኢምፔሪያሊስት ጦርነት ወቅት የተያያዘው የወዛደራዊ ዓለም አቀፋዊነትን እርማ ሳያዛንፍ ነበር ።

ምዕራፍ ስድስት

# የቦልሼቪክ ፓርቲ በኢምፔሪያሊስት ጦርነት ወቅት ፤ ሁለተኛው አብዮት በሩሲያ

## (1914—መጋቢት 1917)

### 1. የኢምፔሪያሊስት ጦርነት መፈንዳትና መንስኤዎቹ ፤

(በአዲሱ አቆጣጠር 27) ፥ 1914 ፥ የዛሩ መንግሥት የከ
ሐምሌ 14 (በአዲሱ አቆጣጠር ነሐሴ 1 ቀን ) ጀርመን
ተት አዋጅ አወጀ ፤ ሐምሌ 19 (በአዲሱ አቆጣጠር ነሐሴ 1 ቀን ) ጀርመን
በሩስያ ላይ ጦርነት አወጀች ።

ሩስያ ጦርነት ውስጥ ገባች ።
ሩስያ ጦርነት ውስጥ ገባች ። በሌኒን የሚመራው የቦልሼቪክ
ጦርነት ከመጀመሩ ቀደም ሲል ፥ በሌኒን የሚመራው የቦልሼቪክ
ጦርነት ከመጀመሩ ቀደም ሲል ፥ በዓለም አቀፍ ሶሻሊ
ፓርቲ ጦርነቱ የማይቀር መሆኑን ተንብዮ ነበር ። በዓለም አቀፍ ሶሻሊ
ስት ኮንግሬሶች ሌኒን በጦርነት ወቅት ሶሻሊስቶች አብዮታዊ መሥመር
የሚከተሉበትን ሁኔታ ለመወሰን የሚያስችሉ ሀሳቦች አቅርቦ ነበር ።

ጦርነት ከካፒታሊዝም ጋር አብሮ መሄዱ የማይቀር መሆኑን ሌኒን
ጠቁሟል ። የውጭ ግዛቶችን መዝረፍ ፥ ቅኝ ግዛቶችን መያዝና ማስቃየት
እንዲሁም አዲስ ገበያዎችን መያዝ ለብዙ ጊዜ የካፒታሊስት ሀገሮች የወ
ረራ ጦርነት መንስኤ ሆኖ ቆይቷል ። ለካፒታሊስት ሀገሮች ፥ ጦርነት ፥
የሠራተኛውን መደብ እንደመበዝበዝ ሁሉ የተፈጥሮ ሕግና ትክክለኛ
ነው ።

በተለይ ካፒታሊዝም ወደ ከፍተኛና የመጨረሻ የእድገት ደረጃው
ኢምፔሪያሊዝም በተሸጋገረበት በአሥራ ዘጠነኛው ክፍል ዘመን መጨ
ረሻና በሀያኛው ክፍለ ዘመን መጀመሪያ ላይ ጦርነት ማስከተሉ የማይቀር
ሆነ ። በካፒታሊዝም ሥር ኃይለኛ የካፒታሊስት ማህበራትና (ሞኖፖሊ
ዎች) ባንኮች በካፒታሊስት መንግሥታት ሕይወት የበላይነትን አገኙ ።
ገንዘባዊ ወረት የካፒታሊስት መንግሥታት አዛዥ ሆነ ። ገንዘባዊ ወረት
አዲስ ገበያ ፥ አዲስ ቅኝ ግዛቶችን መያዝ ፥ ወረት ወደ ውጭ ለመላክ
አዲስ ስፍራ ፥ አዲስ የጥሬ ሐብት ምንጭ ፈለገ ።

ነገር ግን በአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን መጨረሻ ላይ መላውን
የዓለም ክፍል ካፒታሊስት መንግሥታት ተከፋፍለው ይዘው ነበር ።
ይሁን እንጂ በዘመነ ኢምፔሪያሊዝም የካፒታሊዝም እድገት ባልተመ
ጣጠነና በከፍተኛ ደረጃ ይቀጥላል ፤ አንዳንድ ፥ ቀድሞ ከፍተኛ የእድገት
ደረጃ ላይ የነበሩ ሀገሮች አሁን የኢንዱስትሪ እድገታቸው በተነጻጻሪ ዝግ
ያለ ሲሆን ሌሎች ቀድሞ ኋላ ቀር የነበሩ ፈጣን እመርታ በማሳየት ይቀ
ድሟቸዋል ። በተነጻጻሪ የኢምፔሪያሊስት መንግሥታት የምጣኔ ሀብትና



ወታደራዊ ጥንካሬም ለውጥ እያሳየ ነበር ። በመሆኑም ዓለምን እንደገና የመከፋፈል ትግል ተነሳ ፥ ይህም ትግል የኢምፔሪያሊስትን ጦርነት የማይቀር አደረገው ። የ1914 ጦርነት ዓለምንና የተጽእኖ ክልልን እንደገና ለመከፋፈል የተደረገ ጦርነት ነበር ። ሁሉም የኢምፔሪያሊስት መንግስታት ለዚህ የረጅም ጊዜ ዝግጅት በማድረጋቸው የሁሉም ሀገሮች ኢምፔሪያሊስቶች በጦርነቶች ተጠያቂ ነበሩ ።

በተለይ ግን ፥ ጀርመንና አውስትሪያ በአንድ በኩል ፥ ፈረንሳይና ታላቋ ብሪታኒያ ፥ እንዲሁም የኋለኞቹ ሁለቱ ጥገኛ የነበረችውን ሩስያን ጨምሮ ፥ በሌላ በኩል ለዚህ ጦርነት ዝግጅት አድርገው ነበር ። የሶስቱ አባል ሀገሮች ኢንቴንቴ ፥ የታላቋ ብሪታኒያ ፥ የፈረንሳይና የሩስያ ቃል ኪዳን በ1907 ተመሠረተ ። ጀርመን ፥ አውስትሪያ — ሐንጋሪና ኢጣሊያ ሌላ የኢምፔሪያሊስት ቃል ኪዳን መሠረቱ ። ነገር ግን የ1914 ጦርነት ሲጀመር ኢጣሊያ ከዚህ ቃል ኪዳን ወጥታ በኋላ ከኢንቴንቴ ጋር ተቀላቀለች ። ጀርመንና አውስትሪያ—ሐንጋሪ በቡልጋሪያና በቱርክ ይረዱ ነበር ።

ጀርመን ለኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት ዝግጅት ያደረገችው የታላቋ ብሪታኒያንና የፈረንሳይን ቅኝ ግዛቶቻቸውንና ከሩስያ ፥ ክሬን ፥ ፖላንድንና የባልቲክን ግዛቶች ለመውሰድ ባላት ዓላማ መሠረት ነበር ። የባግዳድን ባቡር ሐዲድ በመዘርጋት፥ጀርመን ታላቋ ብሪታኒያ በመካከለኛ ምሥራቅ የነበራትን የበላይነት ስጋት ላይ ጣለች። የጀርመን ባሕር ኃይል ዕድገትም ታላቋ ብሪታኒያን አሰጋት ።

ዛሪስት ሩስያ ቱርክን ከፋፍላ ለመውሰድ ከመፈለጓም በላይ ኮንስታንቲኖ ፕልንና (constantinople) ከጥቁር ባሕር ወደ ሜዲትራኒያን የሚያመሩ የባሕር ወሽመጦችን (the Dardanelles) ለመያዝ ዓለመች ። የዛሪስት ሩስያ እቅድ የአውስትሪያ-ሐንጋሪ ክፍል የሆነችውን ጋሊሲያን መያዝንም ይጨምራል ።

ታላቋ ብሪታኒያ ፥ ከጦርነቱ በፊት ሸቀጦቿ የብሪታኒያን ሸቀጦች ከዓለም ገበያ በማስለቀቅ ላይ የነበረውን አደገኛ ጠላቷን ፥ —ጀርመንን በጦርነቱ ለመምታት ፈለገች ። በተጨማሪም ፥ ታላቋ ብሪታኒያ ሜሶፖታሚያንና ፍልስጥኤምን ከቱርክ ለመውሰድና በግልጽ ጽኑ መሠረት እንዲኖራት አቀደች ።

የፈረንሳይ ካፒታሊስቶች ፥ ሁለቱን ሀብታም የድንጋይ ከሰልና የብረት አካባቢዎች የሳር(Saar) ሸለቆንና ፥ በ1870—71 በተደረገው ጦርነት ጀርመን ከፈረንሳይ ወስዳ የነበረችውን አልሲስ ሎሬንን ከጀርመን ለመውሰድ ፈለጉ ።

በእንዲህ ያለ ሁኔታ ፥ በሁለት የካፒታሊስት መንግሥታት ቡድኖች መካከል የተነሳው ከባድ ቅራኔ የኢምፔሪያሊስቱን ጦርነት አስከተለ ።

ይህ ዓለምን እንደገና ለመከፋፈል የተነሳው አስቃቂ ጦርነት የሁሉንም ኢምፔሪያሊስት ሀገሮች ጥቅም ስለነካ ፣ ጃፓን ፣ አሜሪካና ሌሎችም በርካታ ሀገሮች ቀስ በቀስ በጦርነቱ ውስጥ ገቡ ።

### ጦርነቱ የዓለም ጦርነት ሆነ

ቡርዧዎች ለኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት የሚያደርጉትን ዝግጅት ከሕዝቡ ከባድ ምስጢር አድርገው ያዙት ። ጦርነቱ በተጀመረ ጊዜ እያንዳንዱ የኢምፔሪያሊስት መንግሥት ጐረቤቶቹን እንዳልወረረ ፣ ነገር ግን በእነሱ የተወረረ መሆኑን ለማሳመን ሞከረ ። ቡርዧዎች የጦርነቱን እውነተኛ ዓላማና ኢምፔሪያሊስት የሌሎችን ግዛት በኃይል የመያዝ ባሕሪውን በመሸሸግ ሕዝቡን አታለሉት ። እያንዳንዱ ኢምፔሪያሊስት መንግሥት የራሱን ሀገር ለመከላከል ጦርነት እያካሄደ መሆኑን ገለጸ ።

የሁለተኛው ዓለም አቀፍ አድር ባዮች ቡርዧዎች ሕዝቡን እንዲያታልሉ ድጋፍ ሰጡ ። የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ሶሻል — ዲሞክራቶች የሕብረተሰብአዊነትን ዓላማ ፣ የወዛደሩን ዓለም አቀፋዊ አንድነት ዓላማ በአሳፋሪ ሁኔታ ካዱ ። ጦርነቱን በመቃወም ፈንታ ፣ የወራሪ ሀገሮችን ሠርቶ አደሮችና አርሶ አደሮች አባት ሀገርን መከላከል በሚል ስም እርስ በርሳቸው እንዲዋጉ በመገፋፋት ቡርዧውን አገዙ ።

ሩስያ ከኢንቴንቴ ማለትም ፣ ከፈረንሳይና ከታላቋ ብሪታኒያ ጐን በኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት ውስጥ መግባቷ በአጋጣሚ አልነበረም ። ከ1914 በፊት እጅግ ጠቃሚ የሆኑ የሩስያ ኢንዱስትሪዎች በውጭ ካፒታሊስቶች እጅ ፣ በይበልጥም በፈረንሳይ ፣ በታላቋ ብሪታኒያ በቤልጂግ ፣ ማለትም በኢንቴንቴ ሀገሮች ካፒታሊስቶች እጅ መሆናቸው ግልጽ ነበር ። ከሩስያ የብረታ ብረት ፋብሪካዎች እጅግ ከፍተኛው በፈረንሳይ ካፒታሊስቶች እጅ ነበር ። በጠቅላላው፣ወደ ሶስት አራተኛው (72 በመቶ) የብረታ ብረት ሥራ በውጭ ካፒታል እጅ ነበር ። በዳኔዝ ሸለቆ የሚገኘው የከሰል ኢንዱስትሪም እንዲሁ ። በእንግሊዝና በፈረንሣይ ካፒታል ባለቤትነት የሚሠሩ የዘይት ጉድጓዶች ከሀገሪቱ የዘይት ምርት ግማሹን ያህል ያወጣሉ ። ከሩስያ ኢንዱስትሪ ከፍተኛ ትርፍ ወደ ውጭ ባንኮች ፣ በብዛት ወደ እንግሊዝና ፈረንሳይ ይጐርፋል ። እነዚህ ሁሉ ሁኔታዎች ፣ የዛሩ መንግሥት ከእንግሊዝና ከፈረንሳይ ከተበደረው በብዙ ሺ ሚሊዮን የሚቆጠር እዳ ጋር ተዳምሮ ሩስያን የእነዚህ ሀገሮች አጫፋሪና ግማሽ ቅኝ አደረጋት ።

የሩስያ ቡርዧዎች ኃይላቸውን ለማጠናከር ባላቸው ዓላማ መሠረት፤ አዲስ ገበያ ለማግኘት ፣ በጦርነት ኮንትራት ከፍተኛ ትርፍ ለማግኘትና የጦርነቱን ሁኔታ አጋጣሚ በመጠቀም አብዮታዊ እንቅስቃሴውን ለመምታት ጦርነቱ ውስጥ ገቡ ።

ዛሪስት ሩስያ ለጦርነት ዝግጁ አልነበረችም ። የሩስያ ኢንዱስትሪዎች ከሌሎች የካፒታሊስት ሀገሮች ኢንዱስትሪዎች ጋር ሲነጻጸር እጅግ



ኋላ ቀር ነበሩ ። በብዛት ይጠቀሙባቸው የነበሩት የተበላሹ መሣሪያዎችንና ጊዜው ያለፈባቸውን ወፍጮዎችና ፋብሪካዎች ነበር ። በከፊል ገባርነት ላይ የተመሠረተ የመሬት ሥሪትና በብዛት የደኸዩና የተጐሳቆሉ አርሶ አደሮች በመኖራቸው የተነሳ እርሻዋ ለተራዘመ ጦርነት ጠንካራ መሠረት መሆን አይችልም ነበር ።

የዛሩ ዋና ደጋፊዎች ፊውዳል የመሬት ከበርቴዎች ነበሩ ። ጽልመተ-መቶዎቹ የመሬት ከበርቴዎች ፣ ከታላላቅ ካፒታሊስቶች ጋር በመተባበር ሀገሪቱንና የመንግሥቱን ሽንጕ በበላይነት ይዘውታል ። የዛሩን አገዛዝ የውስጥና የውጭ ፖሊሲ ሙሉ በሙሉ ደገፉ ። የሩስያ ኢምፔሪያሊስት ቡርዧዎች በአንድ በኩል አዳዲስ ገበያዎችንና አዲስ ግዛት ለመያዝ ፣ በሌላ በኩል የሠርቶ አደሩንና የአርሶ አደሩን እንቅስቃሴ ለመምታት ተስፋቸውን በዛሩ ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ መዳፍ ላይ ጣሉ ።

የለዘብተኛ ቡርዧ ፓርቲ—ሕገ መንግሥታዊ ዲሞክራቲክ ፓርቲ-የተቃውሞ መልክ አሳየ ፣ ነገር ግን የዛሩን አገዛዝ የውጭ ፖሊሲ ሙሉ በሙሉ ደገፈ ።

ከጦርነቱ መጀመሪያ አንስቶ ፣ የንዑስ ከበርቴ ፓርቲዎች ፣ ሶሻሊስት አብዮታውያንና ሜንሼቪኮች ፣ የሕብረተሰብአዊነትን ሰንደቅ ሽፋን በማድረግ ፣ የጦርነቱን ኢምፔሪያሊስት ወራሪ ባሕሪ በመሸሸግ ቡርዧው ሕዝቡን እንዲያታልል ረድተዋል ። የቡርዧውን « አባት ሀገር » « ከፕራሽያ አረመኔዎች » የመከላከልን አስፈላጊነት ሰብከዋል ፣ « የሲቪልን ሰላም » ፖሊሲ ደግፈዋል ፣ እንዲህም በማድረግ የጀርመን ሶሻል ዲሞክራቶች የጀርመንን ቄሳር አገዛዝ « በሩስያ አረመኔዎች » ላይ ጦርነት ለማካሄድ እንደረዱት ሁሉ ፣ የሩስያው ዛር ጦርነት እንዲያካሂድ ረድተውታል ።

የቦልሼቪክ ፓርቲ ብቻ ለታላቁ አብዮታዊ ዓለም አቀፋዊነት ዓላማ ታማኝ ሆኖ በመቆየት የዛሩን ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ ፤ የመሬት ከበርቴዎችን ካፒታሊስቶችንና የኢምፔሪያሊስቱን ጦርነት በቆራጥነት ለመዋጋት ማርክሲስት አቋም ያዘ ። ከጦርነቱ መጀመሪያ አንስቶ ፣ ጦርነቱ የተጀመረው ሀገሪቱን ለመጠበቅ ሳይሆን ፣ የውጭ ግዛት ለመያዝ ፣ ለመሬት ከበርቴዎችና ካፒታሊስቶች ጥቅም የውጭ ሀገሮችን ለማስዘረፍ በመሆኑ ሠርቶ አደሮች በዚህ ጦርነት ላይ ቆራጥ ጦርነት ማካሄድ እንዳለባቸው የቦልሼቪክ ፓርቲ አስታወቀ ።

### የሠርቶ አደሩ መደብ ቦልሼቪክ ፓርቲን ደገፈ

በእርግጥ ፣ በጦርነቱ መጀመሪያ ላይ በምሁራንና በሀብታም ገበሬዎች የታየው የቡርዧ ብሔረተኛነት የሠርቶ አደሩን የተወሰነ ክፍል መበከል ችሏል ። እነዚህ ግን በብዛት የወሮበሎች ቡድን የሆነው « የሩስያ ሕዝብ ማህበር » አባላትና የሶሻሊስት አብዮተኞችና የሚንሼቪኮች ተከ

ታይ የሆኑ አንዳንድ ሠርቶ አደሮች ነበሩ ። እነዚህ በምንም ዓይነት የሠርቶ አደሩን እስተሳሰብ አላንጸባረቁም ፣ ማንጸባረቅም አይችሉም ። በጦርነቱ መጀመሪያ ላይ በዛሩ እገዛዝ በተቀነባበረው ትእይንተ ሕዝብ የተሳተፉትም እነዚህ ክፍሎች ብቻ ነበሩ ።

### 2/ የሁለተኛው ዓለም ዓቀፍ ፓርቲዎች ከሀገሮቻቸው ኢምፔሪያሊስት ገዢዎች ጋር መተባበራቸው ፣ የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ወደ ተለያዩ የሶሻል ትምክህተኞች ፓርቲ መከፋፈል ፡-

ሌኒን የሁለተኛውን ዓለም አቀፍ አድርባይነትና የመሪዎቹን ወላዋይ ዝንባሌ በመደጋገም አስጠንቅቆ ነበር ። የሁለተኛው ዓለም አቀፍ መሪዎች ጦርነት መቃወማቸውን ብቻ የሚናገሩና ፣ ጦርነት ቢነሳ ግን አስተሳሰባቸውን ለውጠው ከኢምፔሪያሊስት ቡርዧው ጐን በመሰለፍ ጦርነቱን እንደሚደግፉ ሁልጊዜ ይናገር ነበር ። ቀደም ሲል ሌኒን የተናገረው በጦርነቱ መጀመሪያ እለት ታየ ።

በ1910 ፣ በኮፐን ሐገን የተደረገው የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ኮንግሬስ ፣ በሸንጐ ውስጥ የሚገኙ ሶሻሊስቶች የጦርነትን ብድር በመቃወም ድምጽ እንዲሰጡ ተወስኖ ነበር ። በ1912 የባልካን ጦርነት መጀመሪያ ላይ የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ኮንግሬስ የካፒታሊስቶችን ትርፍ ለማሳደግ ሲባል ሠርቶ አደሮች እርስ በርሳቸው መዋጋት ወንጀል መሆኑን ገለጸ ። ይህን ነበር ያሉት ፣ በውሣኔአቸውም ያስተላለፉት ።

ነገር ግን ማእበሉ ሲነሳ ፣ የኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት ሲጀመርና ይህን ውሣኔ በተግባር የመተርጐሚያው ጊዜ ሲመጣ ፣ የሁለተኛው ዓለም አቀፍ መሪዎች ከሀዲዎች ፣ ወዛደሩን የሸጡና የቡርዧው አገልጋይ መሆናቸውን አረጋገጡ ። የጦርነቱ ደጋፊዎችም ሆኑ ።

በነሐሴ 4 ፣1914 በዱማው ውስጥ የሚገኝ የጀርመን ሶሻል ዲሞክራቶች ለጦርነቱ ብድር እንዲፈቀድ የድጋፍ ድምጽ ሰጡ ፣ የኢምፔሪያሊስቱን ጦርነት በመደገፍ ድምጽ ሰጡ ። በፈረንሳይ ፣ በታላቋ ብሪታኒያ ፣ በቤልጂግና በሌሎችም ሀገሮች የሚገኙ አብዛኛዎቹ ሶሻሊስቶች ያደረጉት እንዲሁ ነበር ።

የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ሕልውና ጠፋ ። አንዱ ሌላውን ወደሚቃወሙ ሶሻል — ትምክህተኛ ፓርቲዎች ተከፋፈሉ ።

የሶሻሊስት ፓርቲዎች መሪዎች ወዛደሩን ክደው የሶሻል—ትምክህተኛነትን አቋም በመያዝ የኢምፔሪያሊስት ቡርዧ ደጋፊ ሆኑ ። ኢምፔሪያሊስት መንግሥታት የሠርቶ አደሩን መደብ በሀሰት እንዲያታልሉና በብሔረተኛነት መርዝ እንዲበክሉ ረድዋቸው ። የአባትን አገር መከላከል የሚል ሽፋን በመጠቀም ፣ እነዚህ ሶሻል—ከዳተኞች የጀርመንን



ሠርቶ አደሮች በፈረንሣይ ሰርቶ አደሮች ላይ ፣ እንዲሁም የእንግሊዝንና የፈረንሳይን ሠርቶ አደሮች በጀርመን ሠርቶ አደሮች ላይ ማነሳሳት ጀመሩ ። ከሁለተኛው ዓለም አቀፍ ውስጥ ዓለም አቀፋዊነት አቋማቸውን ያልለቀቁ ከቁጥር የማይገቡ በጣም ትንሽ ክፍሎች ብቻ ነበሩ ፣ በእርግጥ እነዚህ በቆራጥነት ይህን አላደረጉም ፣ ጉዞአቸው ከማእበሉ ተቃራኒ ነበር እንጂ ።

የኢምፔሪያሊስቱን ጦርነት መታገል የሚለውን አርማ በእስቸኳይና ባለመጠራጠር ያነሳ የቦልሼቪክ ፓርቲ ብቻ ነበር ። በ1914 በልግ ላይ ሌኒን ስለጦርነቱ በጻፈው በኩረ-ሀሳብ የሁለተኛው ዓለም አቀፍ መውደቅ ድንገተኛ እንዳልሆነ ጠቁሟል ። ሁለተኛው ዓለም አቀፍ የአብዮታዊው ወዛደር ግንባር ቀደም ክፍሎች ለረጅም ጊዜ ደባቸውን በማጋለጥ ያስጠነቅቁ በነበሩት አድርባዮች ተውጠዋል ።

የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ፓርቲዎች ከጦርነቱ ቀደም ሲል በአድርባይነት ተበክለው ነበር ። አድርባዮቹ አብዮታዊው ትግል እንዲወገዝ በይፉ ሰብከዋል ፣ « በሰላማዊ መንገድ ካፒታሊዝም ወደ ሶሻሊዝም » ስለሚያድግበት ንድፈ-ሀሳብ ሰብከዋል ። ሁለተኛው ዓለም አቀፍ አድርባይነትን መዋጋት አልፈለገም ፣ የፈለገው ከአድር ባይነት ጋር በሰላም አብሮ በመኖር ፣ አድርባይነት ጥብቅ መሠረት እንዲያገኝ ለማድረግ ነበር ። ከአድር ባይነት ጋር የመታረቅን ፖሊሲ በመከተል ፣ ሁለተኛው ዓለም አቀፍ ራሱ አድር ባይ ሆነ ።

ኢምፔሪያሊስት ቡርዧው ከቅኝ ግዛቶችና ኋላ ቀር ሀገሮችን በመበዝበዝ ከሚያገኘው ትርፍ ከፊሉን በመጠቀም ከሠለጠኑ ሠራተኞች መካከል የላይኛውን ክፍል በከፍተኛ አበልና በሌሎች ክፍያዎች በመደለል ፣ ወዛደራዊ መሳፍንት የሚባለውን በመፍጠር ይገዛቸው ጀመር ። ይህኛው የሠራተኛ ክፍል በርካታ የሞያ ማኅበራትና የሕብረት ሥራ ማኅበራት መሪዎችን ፣ የማዘጋጃ ቤትና የሸንጐ አባላትን ፣ ጋዜጠኞችንና የሶሻል ዲሞክራቲክ ድርጅቶች ሠራተኞችን ያጠቃልላል ። ጦርነቱ ሲጀመር ፣ እነዚህ ሰዎች ጥቅማቸው እንደሚቀርባቸው ስለገመቱ የአብዮቱ ጠላት ፣ የራሳቸው ቡርዧና የኢምፔሪያሊስት አገዛዛቸው ቆራጥ ደጋፊ ሆኑ ።

### አድርባዮቹ ሶሻል ትምክህተኞች ሆኑ

የሶሻል—ትምክህተኞች ፣ የሩስያ ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች በሀገር ውስጥ በሠርቶ አደሩና በቡርዧው መካከል የመደብ እርቅ ተመስርቶ በውጭ ሀገሮች ላይ ጦርነት እንዲካሄድ መስበክ ጀመሩ ። በጦርነቱ ተጠያቂ ማን እንደሆነ በመሸሸግና የተወሰነ ሐገር ቡርዧ በኃላፊነት የማይጠየቅ መሆኑን በመግለጽ ሰፊውን ሕዝብ አታለሉ ። በርካታ ሶሻል ትምክህተኞች የየሀገሮቻቸው ኢምፔሪያሊስት አገዛዝ ሚኒስቴሮች ሆኑ ።

መሀከለኞች (Centrists) በመባል የሚጠሩት ስውር ሶሻል ትምክህተኞችም ለወዛደሩ ዓላማ አደገኛነታቸው ከነዚህኛው ያነሰ አልነበረም ። መሀከለኞች — ካውትስኪ ፣ ትሮትስኪ ፣ ማርቶቭና ሌሎችም ሶሻል ትምክህተኞችን በመደገፍ ወዛደሩን ከዱ ። ደባቸውን ፣ ጦርነቱን ስለ መዋጋት ወዛደሩን ለማታለል የታቀደ « ግራ » ንግግር በማድረግ ሸፈኑ ። እንደ እውነቱ ከሆነ መሀከለኞች ጦርነቱን ደግፈዋል ። ስለ ጦርነቱ ብድር ድምጽ በሚሰጥበት ወቅት ፣ ብድሩን በመቃወም ሳይሆን ድምጽ አለመስጠት የሚለው ሀሳባቸው ፣ ጦርነቱን መደገፍ ማለት ነው። እንደ ሶሻል ትምክህተኞች ፣ እነሱም ኢምፔሪያሊስት አገዛዛቸው ጦርነትን ሲያካሂድ እክል እንዳይገጥመው በጦርነቱ ወቅት የመደብ ትግሉ እንዲወገዝ ጠየቁ ። መሀከለኛው ትሮትስኪ ስለጦርነቱና ስለሶሻሊዝም ባሉ ከፍተኛ ጥያቄዎች በሙላ ሌኒንንና ቦልሼቪክ ፓርቲውን ተቃውሟል ።

ከጦርነቱ መጀመሪያ አንስቶ ሌኒን አዲስ ዓለም አቀፍ ፣ ሶስተኛውን ዓለም አቀፍ ለመመሥረት ኃይል ማሰባሰብ ጀመረ ። በህዳር 1914 ጦርነቱን በመቃወም ባወጣው መግለጫ የቦልሼቪክ ፓርቲ ማእከላዊ ኮሚቴ አሳፋሪ ክስረት በደረሰበት በሁለተኛው ዓለም ዓቀፍ ምትክ ሶስተኛው ዓለም አቀፍ እንዲመሠረት ጥሪ አቀረበ ።

የካቲት 1915 ፣ የኢንቴንቴ ሀገሮች ሶሻሊስቶች ስብሰባ በሎንደን ተደረገ ። በዚህ ስብሰባ ላይ ጓድ ሊትቪኖቭ በሌኒን መመሪያ መሠረት ፣ ሶሻሊስቶች(ቫንዴርቬልዴ ፣ ሳምባትና ጉስዴ) ከቤልጂግና ከፈረንሳይ ቡርዧ አገዛዝ ሥራቸውን እንዲለቁ፣ ከኢምፔሪያሊስቶች ፈጽሞ እንዲላቀቁና እንዳይተባበሯቸው በመጠየቅ ንግግር አደረገ ። ሶሻሊስቶች በሙላ በየሀገራቸው ባለው የኢምፔሪያሊስት አገዛዝ ላይ ቆራጥ ትግል እንዲያካሂዱና ለጦርነቱ ብድር የድጋፍ ድምጽ የሚሰጡትን እንዲያወግዙ ጠየቀ ። ግን በዚህ ስብሰባ ሊትቪኖቭን የሚደግፍ ድምጽ አልቀረበም ።

በ1915 መስከረም መጀመሪያ ላይ የዓለም አቀፋውያን የመጀመሪያ ስብሰባ ዚመርዋልድ (Zimerwald) ውስጥ ተደረገ ። ሌኒንን ይህ ስብሰባ በጦርነቱ ላይ ዓለም አቀፋዊ እንቅስቃሴ ለማምጣት « የመጀመሪያው እርምጃ » ነው ብሎ ጠራው ። በዚህ ስብሰባ ሌኒን የዚመርዋልድን ግራ ቡድኖች መሠረተ ። ነገር ግን በዚመርዋልድ ግራ ቡድን ውስጥ በጦርነቱ ላይ ትክክለኛና የጸና አቋም የያዘው በሌኒን የሚመራው የቦልሼቪክ ፓርቲ ብቻ ነበር ። የዚመርዋልድ ግራ ቡድን ጀርመን ውስጥ ቦርቤቴ (Heralp) የሚል መጽሔት አወጣ ። ሌኒን ለዚህ መጽሔት ጽሑፎችን አቅርቧል ።

በ1916 ዓለም አቀፋውያን ስዊስ ውስጥ በምትገኝ ኪንታል በምትባል መንደር ሁለተኛውን የዓለም አቀፋውያን ስብሰባ ማድረግ ቻሉ ። ይህ ሁለተኛው የዚመርዋልድ ስብሰባ በመባል ይታወቃል ። በዚህ ጊዜ በአብዛኛዎቹ ሀገሮች የዓለም አቀፋውያን ቡድኖች የተመሠረቱ ሲሆን ፣



በዓለም አቀፋውያንና በሶሻል—ትምክህተኞች መካከል ያለው ልዩነት ይበልጥ ተካሮ ነበር ። ነገር ግን በዚህ ወቅት እጅግ ጠቃሚው ነገር ሰፊው ሕዝብ በጦርነቱ ተጽእኖና ባስከተለው ጉዳት የተነሳ ወደ ግራ አዘንብሎ ነበር ። የኪንታል ስብሰባ ያወጣው መግለጫ የዚመርዋልዱ መግለጫ ወደፊት እርምጃና በተለያዩ በማይጣጣሙ ቡድኖች መካከል የተደረገው ስምምነት ውጤት ነበር ።

ነገር ግን እንደ ዚመርዋልዱ ስብሰባ ሁሉ ፣ የኪንታሉም ስብሰባ ፣ የኢምፔሪያሊስቱን ጦርነት ወደ እርስ በርስ ጦርነት መለወጥ ፣ በጦርነቱ የራስን ኢምፔሪያሊስት ሀገር እንዲሸነፍ ማድረግ ፣ እንዲሁም ሶስተኛውን ዓለም አቀፍ መመስረት የሚለውን የቦልሼቪክ ፖሊሲ አልተቀበለውም ። ይሁን እንጂ የኪንታሉ ስብሰባ በመጨረሻ ሶስተኛው ዓለም አቀፍ የተመሠረተባቸውን ዓለም አቀፋዊ ክፍሎች ለማጠናከር ረድቷል።

ሌኒን እንደ ሮዛ ሉክሰምበርግና ካርል ሊብክኔት ያሉ በግራ ሶሻል ዲሞክራቶች መካከል የሚገኙ ዋገቂ ዓለም አቀፋውያንን ወቅሶ፣ ወዲያውም ትክክለኛ አቋም እንዲይዙ ረድቷቸዋል ።

3. <u>በጦርነት ፣ በሰላምና በአብዮት ጥያቄዎች ላይ የቦልሼቪክ ፓርቲ ንድፈ-ሀሳብና ታክቲኮች ።</u>

ቦልሼቪኮች ፣ አብዛኛዎቹ ግራ ሶሻል ዲሞክራቶች እንዳደረጉት ስለ ሰላም በማቃሰትና ራሳቸውን ስለ ሰላም ፕሮፓጋንዳ በመንዛት ብቻ እጃቸውን አጣጥፈው የሚቀመጡ አይደሉም ። ቦልሼቪኮች ጠብ እጫሪ ኢምፔሪያሊስት ቡርዧውን እስከመደምሰስ ድረስ ለሰላም የሚደረገውን አብዮታዊ ትግል ይደግፋሉ ። ቦልሼቪኮች የሰላምን ዓላማ የሚያዛምዱት ከወዛደሩ አብዮት ድል ዓላማ ጋር ነው ። ጦርነትን ለማጥፋትና ትክክለኛን ሰላም ፣ የሌሎች ግዛት ሳይወረርና የጦር ካሣ ሳይከፈልበት የሚገኘውን ሰላም ማግኛው እርግጠኛ መንገድ ኢምፔሪያሊስት ቡርዧውን መደምሰስ ነው ።

ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች አብዮትን በማውገዝ በጦርነት ጊዜ « የሲቪሉን ሰላም » መጠበቅ በሚለው አሳፋሪ መፈክር ተቃራኒ ፣ ቦልሼቪኮች « የኢምፔሪያሊስቱን ጦርነት ወደ እርስ በርስ ጦርነት መለወጥ የሚል » መፈክር አራመዱ ። ይህ መፈክር ማለት ሠርቶ አደሩ ሕዝብ ፣ የወታደር ልብስ የለበሱ የታጠቁ ሠርቶ አደሮችንና አርሶ አደሮችን ጨምሮ ፣ ጦርነቱ እንዲያከትምና ትክክለኛ ሰላም ማግኘት ከፈለጉ መሣሪያቸውን ወደ ራሳቸው ቡርዧ በመመለስ የዚህን አገዛዝ መደምሰስ አለባቸው ማለት ነው ።

የቡርዧውን አባት አገር መጠበቅ ከሚለው የሜንሼቪኮችና የሶሻሊስት አብዮተኞች ፖሊሲ በተቃራኒ ፣ ቦልሼቪኮች « በኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት የራስን ገዢ መደብ እንዲሸነፍ ማድረግ » የሚል ፖሊሲ አራመዱ ። ይህም ማለት ፣ የጦርነት ብድርን በመቃወም ድምጽ መስጠት ፣ በጦር ሠራዊቱ ውስጥ ሥውር አብዮታዊ ድርጅቶችን መመስረት ፣ በግንባር ባሉ ወታደሮች መካከል ወንድማማችነትን መፍጠር ፣ በጦርነቱ ላይ የሠርቶ አደሮችንና የአርሶ አደሮችን አብዮታዊ ተግባር ማደራጀትና ይህንን ድርጅት በራስ ኢምፔሪያሊስት መንግሥት ላይ ማስነሳት ማለት ነው።

ቦልሼቪኮች የዛሩ አገዛዝ በኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት መሸነፍ ሕዝቡ በዛሩ አገዛዝ ላይ ድልን እንዲቀዳጅ አመቺ ስለሚያደርግና የሠርቶ አደሩ መደብ ከካፒታሊስት ባርነትና ከኢምፔሪያሊስት ጦርነት ነጻ ለመውጣት የሚያካሂደውን ትግል እግቡ ለማድረስ ስለሚረዳ ይደገፋል የሚል አቋም ያዙ ። ሌኒን የራስ ኢምፔሪያሊስት አገዛዝ እንዲሸነፍ መጣር ያለባቸው የሩስያ አብዮታውያን ብቻ ሳይሆኑ ፣ ጦርነት በማካሄድ ላይ ያሉ ሀገሮች አብዮታዊ ፓርቲዎች ሁሉ ይህን ፖሊሲ መከተል እንዳለባቸው አሳስቧል ።

ቦልሼቪኮች የሚቃወሙት ማንኛውንም ዓይነት ጦርነት አልነበረም ። ወራሪ ፣ ኢምፔሪያሊስት ጦርነቶችን ብቻ ነበር የሚቃወሙት። ቦልሼቪኮች ሁለት ዓይነት ጦርነቶች መኖራቸውን ያምናሉ ።

ሀ/ ትክክለኛ ጦርነቶች ፦— የወረራ ጦርነት ሳይሆን ሕዝቡን ከውጭ ወረራና ቅኝ ግዛት ለማድረግ ከሚደረግ ሙከራ የሚጠብቅ ፣ ወይም ሕዝቡን ከካፒታሊስት ባርነት ነጻ ለማውጣት ፣ ወይም በመጨረሻ ቅኝና ጥገኛ ሐገሮችን ከኢምፔሪያሊዝም መንጋጋ ለማላቀቅ የሚደረጉ የአርነት ጦርነቶች ሲሆኑ ።

ለ/ ትክክል ያልሆኑ ጦርነቶች የውጭ ሀገሮችንና የውጭ ሕዝቦችን ለመውረርና ለመግዛት የሚደረጉ የወረራ ጦርነቶች ናቸው ።

የመጀመሪያውን ዓይነት ጦርነት ቦልሼቪኮች ደግፈዋል ። ሁለተኛውን ዓይነት ጦርነት በሚመለከት ግን ቦልሼቪኮች በዚህ ላይ እስከ አብዮትና የራስን ኢምፔሪያሊስት መንግሥት እስከ መገልበጥ ድረስ ቆራጥ ትግል ማካሄድ የሚል አቋም ነበር የወሰዱት ።

ለዓለም ሠርቶ አደር መደብ ትልቅ ጥቅም የሰጠው በጦርነቱ ጊዜ ሌኒን ያቀረበው የንድፈ — ሀሳብ ሥራ ነበር ። በ1916 ጸደይ ላይ ሌኒን ኢምፔሪያሊዝም ፣ ከፍተኛው የካፒታሊዝም ደረጃ በሚል ርእስ መጽሐፍ ደረሰ ። በዚህ መጽሐፍ ላይ ኢምፔሪያሊዝም የካፒታሊዝም ከፍተኛ ደረጃ መሆኑን ፣ « ከተራማጅ » ካፒታሊዝም ወደ በሰበሰ ካፒታሊዝም ፣ ደምመጣጭ ካፒታሊዝም በተሸጋገረበት ደረጃ ላይና ኢምፔሪያሊዝም በመሞት ላይ ያለ ካፒታሊዝም መሆኑን አሳየ ። ይህ ማለት ግን ካፒታሊዝም



ያለ ወዛደሩ አብዮት ፣ በራሱ ይሞታል ፣ ይበሰብሳል ማለት አይደለም ። ካፒታሊዝም ያለ ሠርቶ አደሩ መደብ አብዮት የማይደመሰስ መሆኑን ሌኒን ሁሌ አስተምሯል ። በመሆኑም ሌኒን ፣ ኢምፔሪያሊዝም ሟች ካፒታሊዝም መሆኑን እየገለጸ ፣ ወዲያውም « ኢምፔሪያሊዝም የወዛደሩ ሕብረተሰብ አብዮት ዋዜማ መሆኑን » አሳይቷል ።

በዘመነ ኢምፔሪያሊዝም የካፒታሊስት ቀንበር ይበልጥ ጨቋኝ እንደሚሆን ፣ በኢምፔሪያሊዝም ሥር ወዛደሩ በካፒታሊዝም መሠረት ላይ የሚያደርገው አመጽ ከፍ እንደሚልና በካፒታሊስት ሀገሮች የአብዮታዊ ኃይሎች መነሳሳት ምክንያቶች እየበዙ እንደሚሄዱ ሌኒን አሳይቷል ።

በዘመነ ኢምፔሪያሊዝም በቅኝ ግዛቶች በጥገኛ ሀገሮች አብዮታዊው ቀውስ እየተካረረ እንደሚሄድ ፣ በኢምፔሪያሊዝም ላይ የሚያምጹ ኃይሎች ፣ ከኢምፔሪያሊዝም ቀንበር ነጻ ለመውጣት የሚታገሉ የአርነት ቡድኖችም እንደሚበራከቱ ሌኒን አሳይቷል ።

በኢምፔሪያሊዝም ስር የእድገት አለመስተካከልና የካፒታሊዝም ቅራኔዎች በተለይ እየተካረረ እንደሚሄድ ፣ የገበያና የወረት ማራገፊያ ስፍራ ለማግኘት የሚደረገው ትግል ፣ ለቅኝ ግዛቶች ፣ ለጥሬ ሀብት ምንጭ የሚደረገው ትግል ፣ ዓለምን ለመከፋፈል ኢምፔሪያሊስቶች በየጊዜው የሚያደርጉትን ጦርነት የማይቀር እንደሚያደርጉት ሌኒን አሳይቷል ።

ለኢምፔሪያሊስት ጦርነቶች መንስኤ የሚሆነው ፣ የኢምፔሪያሊዝምን ጥንካሬ የሚያሳንሰውና ኢምፔሪያሊዝምን ደካማ ነጥቡ ላይ ለመስበር የሚያስችለው ይህ የካፒታሊዝም ያልተመጣጠነ እድገት እንደሆነም ሌኒን አሳይቷል ።

ከዚህ ሁሉ ሌኒን የሰጠው መደምደሚያ ወዛደሩ ኢምፔሪያሊዝምን በአንድ ስፍራ ወይም በበርካታ ስፍራዎች መስበር እንደሚችለው የሶሻሊዝም ድል በመጀመሪያ በበርካታ አገሮች ወይም በአንድ አገር እንኳን ቢሆን የሚቻል መሆኑን ፣ በካፒታሊዝም ያልተመጣጠነ እድገት የተነሳ ሶሻሊዝም በሁሉም ሀገሮች በአንድ የቡርዧ አገር ሆነው ሲቆዩ ፣ ሶሻሊዝም በአንድ ወይም በበርካታ አገሮች ድል ማድረግ እንደሚችል ነው ።

ሌኒን በኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት ወቅት በሠራቸው ሁለት ጽሑፎች ስለነዚህ ብሩህ ሀሳቦች ያቀረባቸው ቅመራዎች እነሆ ፣

1/ « ያልተመጣጠነ የምጣኔ-ሀብትና የፖለቲካ እድገት የካፒታሊዝም ፍጹም ሕግ ነው ። በመሆኑም ፣ የሶሻሊዝም ድል በመጀመሪያ በብዙ ወይም በአንድ ካፒታሊስት አገር ብቻ ሊመጣ ይችላል ። የዚያ አገር ድል አድራጊ ወዛደር ፣ ካፒታሊስቶችን ወርሶ የራሱን ሶሻሊስት ምርት ካደራጀ በኋላ ፣ የሌሎችን አገሮች ጭቁን መደቦች ወደ ዓላማው በመሳብ በሌላው ዓለም ላይ ፣ በካፒታሊስቱ ዓለም ላይ ይነሳል . . .»

(«የአውሮፓ የተባበሩ ሀገሮች መፈክር» ከሚለው ጽሁፍ ፣ በነሐሴ 1915 የተጻፈ ፦ ሌኒን ፣ ምርጥ ሥራዎች ፣ የእንግሊዘኛ እትም ቅጽ 5 ገጽ 141)

2/ « በተለያዩ አገሮች የካፒታሊዝም እድገት ፍጹም ባልተመጣጠነ
ሁኔታ ይቀጥላል ። በሸቀጥ ምርት ሥርዓት ከዚህ ሌላ መሆን አይችልም።
ከዚህ መረዳት የሚቻለው ሶሻሊዝም በሁሉም አገሮች በአንድ ጊዜ
ድል ማድረግ እንደማይችል ነው ። ሌሎች አገሮች ለተወሰነ ጊዜ የቡርዧ
ወይም ቅድመ ቡርዧ ሆነው ሲቆዩ ፣ ሶሻሊዝም በአንድ ወይም በበርካታ
አገሮች ድል ማድረግ ይችላል ። ይህ ከሌሎች አገሮች ቡርዧ ጋር ግጭት
ብቻ ሳይሆን፣ቡርዧዎች የሶሻሊስት ሀገርን ወዛደር ለመደምሰስ በቀጥታ
እንዲነሱ ያደርጋል ። በዚህን ጊዜ በኛ በኩል የሚደረገው ጦርነት ሕጋ
ዊና ትክክለኛ ጦርነት ይሆናል ። ለሶሻሊዝም ፣ ሌሎችን አገሮች ከቡርዧ
ነጻ ለማውጣት የሚደረግ ጦርነት ይሆናል ። «የወዛደሩ አብዮት የጦር
ነት መርሀ— ግብር » ከሚለው ጽሑፍ በ1916 በልግ የተጻፈ ፣
(ሌኒን ፣ ስብስብ ሥራዎች ፣ የሩሲያ እትም ፣ ቅጽ 19 ገጽ 325)

ይህ የተሟላና አዲስ የሶሻሊስት አብዮት ንድፈ-ሐሳብ ፣ በተለ
ያዩ አገሮች የሶሻሊዝም ድል ሊመጣ እንደሚችል የሚያረጋግጥ ንድፈ
ሐሳብ ፣ የዚህን ድል ሁኔታዎችን የወደፊት ተስፋውን የሚያሳይ ፣ መሠ
ረተ ሀሳቡ ቀደም ሲል ሌኒን « በዲሞክራሲያዊ አብዮት ወቅት የሶሻል
ዲሞክራሲ ሁለት ታክቲኮች » በሚል ርእስ በ1905 ባቀረበው ጽሑፍ
የተገለጸ ንድፈ-ሐሳብ ነበር ።

ይህ ንድፈ-ሐሳብ ፣ በተለያዩ አገሮች የሶሻሊዝም ድል አይቻልም ፣
በመሆኑም በሰለጠኑ ሀገሮች በሞላ በአንድ ጊዜ ይመጣል የሚል አቋም
ከያዙት በቅድመ-ኢምፔሪያሊስት ካፒታሊዝም ወቅት ከነበሩ ማርክሲ
ስቶች አመለካከት ጋር መሠረታዊ ልዩነት አለው ። ኢምፔሪያሊስት ካፒ
ታሊዝምን በሚመለከት ፣ ኢምፔሪያሊዝም ፣ የካፒታሊዝም የመጨረሻ
ደረጃ በሚለው መጽሐፉ ሌኒን ይህ ጊዜው ያለፈበት አመለካከት መሆኑን
አስረድቶ በሁሉም አገሮች ሶሻሊዝም ድል ማድረግ የማይችል ፤ ግን
በአንድ ካፒታሊስት ሀገር የሶሻሊዝም ድል የሚቻል ስለመሆኑ አዲስ
ንድፈ-ሀሳብ በማቅረብ ተከቷል ።

ስለ ሶሻሊስት አብዮት ሌኒን ያቀረበው ንድፈ-ሀሳብ ከሚገመት
በላይ ጠቃሚ የሆነው ማርክሲዝምን በአዲስ ንድፈ-ሀሳብ በማበልጸጉና
ማርክሲዝምን በማራመዱ ብቻ ሳይሆን ፣ ለተለያዩ ሀገሮች ወዛደሮች አብ
ዮታዊ ተስፋ በመክፈቱ ፣ በራሳቸው ብሔራዊ ቡርዧ ላይ የማጥቃት እር
ምጃ እንዲጀምሩ በማነሳሳቱ ፣ ይህን የማጥቃት እርምጃ ለመውሰድ የጦ
ርነት ሁኔታዎችን እንዲጠቀሙ በማስተማሩና በወዛደሩ አብዮት ድል እም
ነታቸውን በማጠናከሩም ጭምር ነው ።

በጦርነት ፣ በሰላምና በአብዮት ጥያቄ ላይ የቦልሼቪኮች አቋም እን
ዲህ ነበር ።

በዚህ አቋም መሠረት ነው ቦልሼቪኮች በሩስያ ተግባራዊ ሥራቸ
ውን ያካሄዱት ።



በጦርነቱ መጀመሪያ ላይ ፣ ፖሊስ ከፍተኛ የማጥቃት እርምጃ እየ
ወሰደ እንኳን ፣ በዱማው ውስጥ የሚገኙ የቦልሼቪክ አባላት—ባዳዬቭ ፣
ፔትሮቪስኪ ፣ ሙራኖቭ ፣ ሳሞይሎቭና ሻጉቭ— በርካታ ድርጅቶችን እየ
ጉበኙ ቦልሼቪኮች ስለጦርነቱና ስለአብዮቱ ስላላቸው ፖሊሲ ገለጻ ያደ
ርጉ ነበር ። በህዳር 1914 በዱማው ውስጥ የሚገኘው ቦልሼቪክ ቡድን
ስለ ጦርነቱ ፖሊሲ ለመወያየት አንድ ስብሰባ አካሄደ ። በሶስተኛው ቀን
በስብሰባው የተገኙት በሞላ ታሰሩ ። በዱማው የሚገኙ የቦልሼቪክ አባ
ላት የሲቪል መብታቸው ተገፎ ወደ ምሥራቅ ሳይቤሪያ በግዞት እንዲ
ላኩ ተበየነባቸው ። የዛሩ መንግሥት « በከፍተኛ ከሀዲነት » ከሰሳቸው።

የዱማው አባላት ለፍርድ ቤቱ ያቀረቡት ሀሳብ ለፓርቲያችን ጥቅም
ነበረው ። የቦልሼቪክ አባላት የፍርድ ቤቱን መድረክ የዛሩን የወራሪነት
ፖሊሲ ማጋለጫ አድርገው በመጠቀም ፣ ራሳቸውን በቆራጥነት አቀረቡ።

በዚህ ጉዳይ ተጠያቂ ከነበሩት አንዱ የሆነው የካሜኔቭ አቀራረብ
ግን ፍጹም የተለየ ነበር ። ፈሪ በመሆኑ የተነሳ ፣ የመጀመሪያው አደጋ ሲያ
ጋጥመው የቦልሼቪክን ፓርቲ ፖሊሲ ካደ ። ካሜኔቭ ከቦልሼቪኮች ጋር
በጦርነቱ ጥያቄ ላይ አለመስማማቱን ለፍርድ ቤቱ ገልጾ ፣ ይህን ለማረጋ
ገጥ ሜንሼቪኩ ጆርዳኒስኪ ለምስክርነት እንዲቀርብ ጠየቀ ።

ቦልሼቪኮች የጦርነቱን ፍላጐት ለማሟላት የተቋቋመውን የጦር ኢ
ንዱስትሪዎችን ኮሚቴና ሜንሼቪኮች ሠርቶ አደሩን በኢምፔሪያሊስት
ቡርዧው ተጽእኖ ሥር ለማምጣት ያደረጉትን ሙከራ በመቃወም ከፍ
ተኛ ሥራ አከናውነዋል ። የኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት ሕዝባዊ ጦርነት መ
ሆኑን ሁሉንም ሰው ማሳመን የቡርዧው ከፍተኛ ፍላጐት ነበር ። በጦር
ነቱ ወቅት ቡርዧው በመንግሥት ጉዳዮች ተጽእኖ ማድረግና የገጠሩና
የከተማ ሕብረት የሚል የራሱ የሆነ ሀገር አቀፍ ድርጅት መመሥረት ችሎ
ነበር ። ሠርቶ አደሮችንም ፣ በራሱ አመራርና ተጽእኖ ሥር ማምጣት ለቡ
ርዧው አስፈላጊ ነበር ። ቡርዧው የጦርነት ኢንዱስትሪ ኮሚቴዎችን
« የሠርቶ አደር ቡድኖች » በመመሥረት ይህን ለማግኘት አሰበ ። ሜን
ሼቪኮች ይህን ሀሳብ ተቀበሉ ። በእነዚህ የጦርነት ኢንዱስትሪ ኮሚቴዎች
ውስጥ ሰፊውን ሠርቶ አደር መደብ ፈንጂዎችን ፣ ጠመንጃዎችን ፣ ጥይ
ቶችንና ሌሎችንም የጦር መሣሪያዎች በብዛት እንዲያመርቱ የሚገፋፉ
የሠርቶ አደሮች ተወካዮች መኖር ለቡርዧው ከፍተኛ ጥቅም ነበረው ።
« ማንኛውም ነገር ለጦርነቱ ፣ ሁሉም ለጦርነቱ » የቡርዧው መፈክር
ነበር ። እንደውነቱ ከሆነ ይህ መፈክር ማለት « የቻልከውን ያህል በጦር
ነት ኮንትራትና የውጭ ግዛትን በመያዝ በልጽግ» ማለት ነበር። ሜንሼቪ
ኮች በዚህ በቡርዧው አስመሣይ ጀግንነት እቅድ ከፍተኛ ሚና ነበራቸው።
በሰርቶ አደሩ መካከል የጦርነት ኢንዱስትሪ ኮሚቴ « የሰርቶ አደር ቡድ
ኖችን » ለማስመረጥ ከፍተኛ ዘመቻ በማካሄድ ካፒታሊስቶችን ረድተ
ዋል ። ቦልሼቪኮች ይህን እቅድ ተቃውመዋል ። በጦርነቱ ኢንዱስትሪ

ኮሚቴ ሰርቶ አደሮች እንዳይሣተፉ ጥረዋል ፣ ውጤትም አግኝተውበታል ። ነገር ግን በቀንደኛው ሜንሼቪክ ፣ ቮዝዴቭና ፣ በሰላዩ በአብሮሲሞቭ የሚመሩ ጥቂት ሰርቶ አደሮች በጦርነት ኮሚቴ ውስጥ ሰርተዋል ። ይህ ሆኖ በመስከረም 1915 የሰርቶ አደሮች ተወካዮች በጦርነቱ ኢንዱስትሪ «የሰርቶ አደርን ቡድኖች » ለመምረጥ የመጨረሻ ስብሰባ ባደረጉበት ወቅት አብዛኛዎቹ በዚህ መሳተፉን ተቃውመው ተገኙ ። አብዛኛዎቹ የሠርቶ አደሩ ተወካዮች በጦርነቱ ኢንዱስትሪ መሣተፉን በመቃወሙና ለሰላምና የዛሩን አገዛዝ ለመደምሰስ መቆም የሰርቶ አደሮች አላማ እንደሆነ በመግለጽ ጠንካራ ውሳኔ አስተላለፉ ።

ቦልሼቪኮች በጦሩና በባህር ሃይሉ ውስጥ ከፍተኛ ሥራ ማከናወን ጀመሩ ። ጦርነቱ ላስከተለው ከግምት በላይ ሥጋትና ለሕዝቡ መሰቃየት ማን ተጠያቂ መሆን እንደሚገባው ለወታደሮችና ለመርከበኞች አስረዱ፣ ሕዝቡ ከኢምፔሪያሊስቱ እልቂት ለመውጣት አንድ መንገድ ብቻ እንዳለውና ይህም አብዮት እንደሆነ አስረዱ ። ቦልሼቪኮች በጦር ሰራዊቱና በባህር ሃይሉ ውስጥ ፣ በግንባርም በደጀንም ፣ ሴሎችን በመመስረት ጦርነቱን እንዲቃወሙ ጥሪ የሚያደርጉ ጽሑፎችን አሰራጩ ።

በክሮንስታድ ፣ ቦልሼቪኮች ከፓርቲው የፔትሮግራድ ኮሚቴ ጋር የቅርብ ግንኙነት ያለው«የክሮንስታድ ወታደራዊ ድርጅቶች ማእከላዊ ቡድን » መሠረቱ ። በጦር ሰፈሩ ውስጥ እንዲሠራ የፔትሮግራድ ፓርቲ ኮሚቴ ወታደራዊ ድርጅት ተቋቋመ ። በነሐሴ 1916 የፔትሮግራድ አካባቢ ኃላፊ ያቀረበው ዘገባ « በክሮንስታድ ቡድን ነገሮች በደንብ የተደራጁ ፣ ስውርና አባላቱም ዲሲፕሊን ያላቸው ጥንቁቅ ሰዎች ናቸው ። ቡድኖቹ በባሕር ዳርቻም ተወካዮች አሏቸው » የሚል ነበር ።

በጦር ግንባር ፣ ፓርቲው ለውጊያ በተሰለፉ ወታደሮች መካከል ወንድማማችነት እንዲመሰረትና የዓለም ቡርዧ የሁሉም ጠላት መሆኑን በማስረዳት ፣ ጦርነቱ ሊያበቃ የሚችለው የኢምፔሪያሊስቱን ጦርነት ወደ እርስ በርስ ጦርነት ለውጦ መሣሪያን ወደ ራስ ቡርዧና በአገዛዙ ላይ በማዞር ብቻ መሆኑን በመግለጽ ቅስቀሳ አደረገ ። የወታደር ቡድኖች የማጥቃት እርምጃ ለመውሰድ የሚያደርጉት እምቢታ እየጨመረ ሄደ ። እንዲህ ዓይነት ሁኔታዎች በ1915 ነበሩ ፤ በ1916ም እየበዙ ሄዱ ።

በተለይ በሰሜን ግንባር ፣ በባልቲክ ግዛት ባለው ጦር ውስጥ ያለው የቦልሼቪኮች ድርጊት ከፍተኛ ነበር ። በ1917 መጀመሪያ ላይ የሰሜኑ ግንባር ጦር አዛዥ ፣ ጄኔራል ሩዝስኪ በግንባሩ የቦልሼቪኮች አብዮታዊ ሥራ የተፋፋመ መሆኑን ለጠቅላይ መምሪያው ገለጸ ።

ጦርነቱ በሕዝቦች ኑሮ ፣ በዓለም የሠርቶ አደር መደብ ኑሮ ከፍተኛ ለውጥ አስከተለ ። የመንግሥታት እጣ ፣ የሕዝቦች ፣ እጣ ፣ የሶሻሊስት እንቅስቃሴ እጣ በአደጋ ላይ ነበር ። ስለዚህ ጦርነቱ ራሳቸውን ሶሻሊስት



ለሚሉ ፓርቲዎችና ፈለጎች በሞላ መፈተኛ ነበር ። እነዚህ ፓርቲዎችና ፈለጎች ለሶሻሊዝም ዓላማ ፣ ለዓለም አቀፋዊ ዓላማ ታማኝ ሆነው ይቆዩ ወይስ የሠርቶ አደሩን መደብ በመክዳት ፣ እርግጫቸውን ጥለው በብሔራዊ ቡርዧዎች ጫማ ስር ለመውደቅ ይመርጣሉ ? — ይህ ነበር የጊዜው ጥያቄ ።

የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ፓርቲዎች ፈተናውን እንዳልተቋቋሙ ፣ የሠርቶ አደሩን መደብ እንደከዱና ለየሀገሮቻቸው ኢምፔሪያሊስት ቡርዧዎች እጃቸውን እንደሰጡ ጦርነቱ አሳየ ።

እነዚህ በመካከላቸው አድርባይነትን ያሰፈኑ ፣ ከአድር ባዮች ጋር ፣ ከብሔረተኞች ጋር እርቅ ያደረጉ ፓርቲዎች ከዚህ የተለየ ማድረግ አይችሉም ነበር ።

ፈተናውን በአሸብራቂ ቀለም ያለፈና ለሶሻሊዝም ዓላማ ፣ ለወዛደሩ ዓለም አቀፍነት ዓላማ ታማኝ ሆኖ የቆየ የቦልሼቪክ ፓርቲ ብቻ መሆኑን ጦርነቱ አሳየ ።

ይህ የተጠበቀ ነበር ፤ አዲሱ ዓይነት ፓርቲ ብቻ ፣ በአድር ባይነት ላይ የማያቋርጥ ትግል ለማካሄድ ቆራጥ መንፈስ ያለው ፓርቲ ብቻ ፣ ከአድርባይነትና ከብሔረተኝነት ነጻ የሆነ ፓርቲ ብቻ ፣ እንዲህ ዓይነቱ ፓርቲ ብቻ ነው ይህን ታላቅ ፈተና ማለፍና ለሠርቶ አደሩ መደብ ዓላማ ለሶሻሊዝም ዓላማና ለዓለም አቀፋዊነት ዓላማ ታማኝ መሆን የሚችል ።

የቦልሼቢክ ፓርቲ እንዲህ ዓይነት ፓርቲ ነበር ።

## 4/ የዛሩ ጦር ሠራዊት ሽንፈት ፣ የምጣኔ-ሀብቱ ቀውስ ፤ የዛሩ አገዛዝ መፍለስ ፤

ጦርነቱ መካሄድ ከጀመረ ሶስት ዓመት ሆነው ። በጦርነቱ ፣ ወይም በጦርነት ውስጥ በደረሰባቸው መቁሰል ወይም የጦርነቱ ሁኔታ ባስከተለው በሽታ በሚሊዮን የሚቆጠሩ ሰዎች አልቀዋል ። ቡርዧዎችና የመሬት ከበርቴዎች ከጦርነቱ ብዙ ሀብት እያካበቱ ነበር ። የሠርቶ አደሩና የአርሶ አደሩ ሥቃይና መከራ እየጨመረ ሄደ ። ጦርነቱ የሩስያን ምጣኔ ሀብታዊ ኑሮም እያቃወሰ ነበር ። ወደ አሥራ አራት ሚሊዮን የሚሆኑ መሥራት የሚችሉ ሰዎች ከምጣኔ ሀብቱ ሥራ ተገልለው ወደ ወታደራዊው ክፍል ተወሰዱ ። ወፍጮዎችና ፋብሪካዎች ቀጥ አሉ ። በሠራተኛ እጥረት የተነሳ የእርሻው ሥራ ቀነሰ ። በግንባር ላይ ያሉ ሕዝቦችና ወታደሮች ተራቡ ፣ የሚያደርጉት ጫማ አጡ ፣ ታረዙም ። ጦርነቱ የሀገሪቱን ሀብት ማሟጠጥ ጀመረ ።

የዛሩ ሠራዊት የተደጋገመ ሽንፈት ገጠመው ። የዛሩ ሠራዊት የጠመንጃዎች ፣ የፈንጂዎችና የቀላል መሣሪያዎች እንኳን እጥረት ስለነበረበት የጀርመን ከባድ መሣሪያዎች በዛሩ ሠራዊት ላይ የቦምብ ናዳ አወ

ረዱበት ። እንዳንድ ጊዜ በአንድ መሣሪያ ሶስት ወታደሮች መጠቀም ነበረባቸው ፣ ጦርነቱ በመካሄድ ላይ እያለ ፣ የዛሩ የጦር ሚኒስቴር ሱኮምሊኖቭ ከጀርመን ሰላዮች ጋር ግንኙነት ያለውና የጦሩ ግንባር መሣሪያ እንዳይደርሰው ለማድረግ የጀርመን ስለላ ድርጅቶችን መመሪያ በተግባር ላይ የሚያውል እንደሆነ ታወቀ ። እንዳንድ የዛሩ ሚኒስትሮችና ጀኔራሎች የጀርመን ሠራዊት እንዲያሸንፍ ጥረዋል ፣ ወታደራዊ ምስጢሮችን ለጀርመኖች አሳልፍው ሰጥተዋል ። የዛሩ ወታደሮች ብዙ ችግር ደርሶባቸው እንዲያፈገፍጉ መደረጋቸው የሚያስደንቅ አልነበረም ። በ1916 ላይ ጀርመኖች ፖላንድንና በከፊል የባልቲክ ግዛቶችን ያዙ ።

እነዚህ ሁሉ ሠርቶ አደሮች ፣ አርሶ አደሮች ወታደሮችና ምሁራን የዛሩን አገዛዝ እንዲጠሉ ሰፊው ሕዝብ በጦርነቱና በዛሩ አገዛዝ ላይ አብዮታዊ እንቅስቃሴውን ከኋላም ሆነ በግንባር ፣ በመሀልና በጠረፍ አካባቢዎች እንዲያፋፍሙ አደረጉ ።

በሩስያ ኢምፔሪያሊስት ቡርዧም ውስጥ ችግር ተስፋፋ ። ከጀርመን ጋር የተናጠል ስምምነት ለማድረግ ይፈልጉ የነበሩ እንደ ራስፑቲን ያሉ ወስላቶች በዛሩ አስተዳደር ከፍተኛ ቦታ መያዛቸው ቁጣውን አባባሰ ። የዛሩ መንግሥት ጦርነቱን በደንብ ማካሄድ እንደማይችል ቡርዧው ይበልጥ እየገባው ሄደ ። ዛሩ ፣ ሥልጣኑን ላለመልቀቅ ሲል ከጀርመን ጋር የተናጠል ስምምነት እንዳያደርግ ፈራ ። ስለዚህ የሩስያ ቡርዧ ዛር ኒኮላስ ዳግማዊን አውርዶ በምትኩ ከቡርዧው ጋር ግንኙነት የነበረውን ሚካኤል ሮማኖን ለመተካት መፈንቅለ መንግሥት አዘጋጁ ። በዚህ መንገድ ሁለት ወፎች በአንድ ድንጋይ ለመግደል ፣ በመጀመሪያ ራሱ ሥልጣን ለመጨበጥና የኢምፔሪያሊስቱን ጦርነት ለመምራት ፣ በሁለተኛ ደረጃ በመነሳሳት ላይ የነበረውን አብዮታዊ ማእበል በትንሽ መፈንቅለ መንግሥት ለመግታት ፈለጉ ።

በዚህ የሩስያ ቡርዧዎች ዛሩ ጦርነቱን ለመምራት እንደማይችል ከተረዱት ከእንግሊዝና ከፈረንሳይ መንግሥታት ሙሉ ድጋፍ ነበራቸው ። እነሱም የዛሩ መንግሥት ከጀርመን ጋር የተናጠል የሰላም ስምምነት እንዳያደርግ ፈሩ ። የዛሩ መንግሥት ከጀርመን ጋር የተናጠል ስምምነት ከፈረመ ፣ የእንግሊዝና የፈረንሳይ መንግሥታት የሚያጡት የጠላትን ኃይል ወደራሱ ግንባር የመለሰ አጋር ብቻ ሳይሆን ፣ ፈረንሳይን የሚያገለግሉ በብዙ ሺ የሚቆጠሩ የሩስያ ወታደሮችንም ጭምር ነበር ። በዚህ የተነሳ የእንግሊዝና የፈረንሳይ መንግሥታት መፈንቅለ መንግሥቱን ደገፉ ።

ስለሆነም ዛሩ ብቻውን ሆነ ።

በግንባሩ የተደጋገመ ሽንፈት እየደረሰ ፣ የምጣኔ ሀብቱ መዛባት ይበልጥ እየከረረ መጣ ። በ1917 ጥርና ታህሣሥ ላይ የምግብ ፣ የጥሬ ሀብትና የነዳጅ ስርጭት አለመስተካከል አስከፊ ደረጃ ላይ ደረሰ ። የምግብ ሸቀጣሸቀጦች ለፔትሮግራድና ለሞስኮ መድረስ አልቻሉም ። ፋብሪካዎች



በተከታታይ መዘጋት ስለጀመሩ ይህ የሥራ አጡን መጠን እጅግ ከፍ አደረገ ። በተለይ የሠርቶ አደሮች የኑሮ ሁኔታ አስከፊ ነበር ። ከዚህ አስከፊ ሁኔታ ለመውጣት ያለው ብቸኛ መንገድ የዛሩን ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ መገልበጥ መሆኑን ብዙ ሰዎች እያመኑ ሄዱ ።

በእርግጥ የዛሩ አገዛዝ በአስከፊ ቀውስ ውስጥ ነበር ።
ቡርዧው ለቀውሱ መፍትሔ በመፈንቅለ መንግሥት ለማግኘት ፈለገ ።

ሕዝቡ ግን የራሱን መፍትሔ አገኘለት ።

## 5/ የየካቲቱ አብዮት ፣ የዛሩ አገዛዝ መገርሰስ ፣ የሶቪየት ሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ተወካዮች ሶቪየት መመሥረት ፣ የጊዜአዊው መንግሥት መቋቋም ፤ ጥምር የሁለት ወገን ሥልጣን ፤

1917 ዓ. ም. በጥር 9 የተደረገው የሥራ ማቆም አድማ ተከፈተ ። በዚህ የሥራ ማቆም አድማ ወቅት በፔትሮግራድ ፣ በሞስኮ ፣ በባኩና በኒዝኒ — ኖቭጐሮድ ሰላማዊ ሰልፎች ተደረጉ ። በጥር 9 የሥራ ማቆም አድማ በሞስኮ ወደ አንድ ሶስተኛው ሠርቶ አደሮች ተካፈሉ ። በትቤርስኮ ቦሌቫርድ (አውራጐዳና) ሁለት ሺ ሰዎች የተካፈሉበት ሰላማዊ ሰልፍ በፈረሰኛ ፖሊሶች ተበተነ ። ፔትሮግራድ ውስጥ ፣ በቪበርግ ቋሲ በተደረገው ሰላማዊ ሰልፍ ወታደሮችም ተካፍለዋል ።

« የአጠቃላዩ የሥራ ማቆም አድማ ሐሳብ በየእለቱ አዳዲስ ደጋፊዎች እያገኘና በ1905 እንደነበረው በጣም እየተዛመተ መሄዱን » የፔትሮግራድ ፖሊሶች አስታወቁ ።

ሜንሼቪኮች የሠርቶ አደሮች ሰልፍ የመንግሥቱ ዱማ በሚከፈትበት በየካቲት 14 እንዲደረግ ሀሳብ አቀረቡ ። ሠርቶ አደሩ ሰፊ ሕዝብ ግን በቦልሼቪኮች በመመራት ወደ መንግሥቱ ዱማ ሳይሆን ወደ ሰላማዊ ሰልፉ ሄዱ ።

በየካቲት 18 /1917 በፔትሮግራድ የሚገኙ የፑቲሎቭ ሠራተኞች የሥራ ማቆም አድማ አደረጉ ። በየካቲት 22 የአብዛኛው ታላላቅ ፋብሪካዎች ሠርቶ አደሮች ሥራ አቆሙ ። በዓለም አቀፍ የሴቶች ቀን ፣ የካቲት 23( መጋቢት 8) ፣ በፔትሮግራድ የቦልሼቪክ ኮሚቴ ጥሪ መሠረት ሠርቶ አደር ሴቶች ረሀብን ፣ ጦርነትንና የዛሩን አገዛዝ በመቃወም ሰላማዊ ሰልፍ አደረጉ ። የፔትሮግራድ ሠርቶ አደሮች የሠርቶ አደር ሴቶችን ሰላማዊ ሰልፍ ከተማ አቀፍ የሥራ ማቆም እንቅስቃሴ በማድረግ ደገፉ ። የፖለቲካዊ የሥራ ማቆም አድማ በዛሩ ላይ አጠቃላይ የፖለቲካ ሰላማዊ ሰልፍ ወደ ማድረግ ደረጃ ከፍ አለ ።

በየካቲት 24(መጋቢት 9) ሰላማዊ ሰልፉ በከፍተኛ ደረጃ ቀጠለ ። ወደ 200,000 ሠርቶ አደሮች ሥራ አቆሙ ።

በየካቲት 25 (መጋቢት 10)መላው የፔትሮግራድ ሠርቶ አደር መደብ
አብዮታዊ እንቅስቃሴው ውስጥ ገባ ። በየቀበሌው ተፈነጣጥረው ይደ
ረጉ የነበሩት የፖለቲካ የሥራ ማቆም አድማዎች አንድ ላይ አጠቃላይ
የከተማው ሆነው ተነሱ ። በየቦታው ሰላማዊ ሰልፎችና ከፖሊስ ጋር ግጭ
ቶች ተደረጉ ። ሰፊው ሠርቶ አደር ሕዝብ «የዛሩ አገዛዝ ይውደም !» «ጦር
ነት ይውደም ! » « ዳቦ እንፈልጋለን ! » የሚሉ መፈክሮችን አነሳ ።

የካቲት 26 (መጋቢት 11) ጧት ፖለቲካዊው የሥራ ማቆም አድ
ማና ሰላማዊ ሰልፉ የአመጽ መልክ ያዘ ። ሠርቶ አደሮች ፖሊሶችንና ጸ
ጥታ ጠባቂዎችን ትጥቅ አስፈትተው ራሳቸው ታጠቁ ። ቢሆንም ፣ ከፖ
ሊሶች ጋር የተደረገው ግጭት በዝናሜኒስካያ አደባባይ በሰላማዊ ሰልፈ
ኞች ላይ በተከፈተው ተኩስ ተበተነ ።

የፔትሮግራድ ወታደራዊ አካባቢ አዛዥ ፣ ጀኔራል ካባሎቭ ሠርቶ
አደሮች እስከ የካቲት 28(መጋቢት 13) ወደ ሥራቸው ካልተመለሱ ወደ
ጦር ግንባር የሚላኩ መሆኑን አስታወቀ ። የካቲት 25 (መጋቢት 10)
ዛሩ 1 « በዋናው ከተማ ያለውን ሁከት ከነገ ሳያልፍ እንዲቆም እንድታ
ደርግ አዝሃለሁ » ሲል ለጀኔራል ካባሎቭ ትእዛዝ ሰጠ ።

ነገር ግን አብዮቱን « እንዲቆም ማድረግ » የሚቻልበት ጊዜ አልነ
በረም ።

የካቲት 26( መጋቢት 11) የፓብሎቭስኪ ሬጂመንት ተጠባባቂ ባታ
ሊዮን 4ኛ ክፍል በሠርቶ አደሮች ላይ ሳይሆን ከሠርቶ አደሮች ጋር ይጋጩ
በነበሩ ፈረሰኛ ፖሊሶች ላይ ተኩስ ከፈተ ። የወታደሮችን ድጋፍ ለማግ
ኘት በተለይ ፣ ሠርቶ አደር ሴቶች በቀጥታ ለወታደሮች ንግግር በማድረግ
ወንድማማችነታቸውን በመግለጽና የተጠላውን የዛሩን ፈላጭ ቆራጭ
አገዛዝ ለመደምሰስ ሕዝቡን እንዲረዱ ጥሪ በማቅረብ እጅግ ከፍተኛና
ያልተቆጠበ ጥረት አድርገዋል ።

በዚያን ወቅት ተግባራዊ ሥራው ይመራ የነበረው ዋና ጽሕፈት ቤቱ
ፔትሮግራድ በሆነውና በጓድ ሞሎቶቭ ይመራ በነበረው በፓርቲአችን
ማእከላዊ ኮሚቴ ቢሮ ነበር ። የካቲት 26(መጋቢት 11) የማእከላዊ ኮሚ
ቴው ቢሮ በዛሩ አገዛዝ ላይ የትጥቁ ትግል እንዲቀጥልና ጊዜአዊ አብዮ
ታዊ መንግሥት እንዲቋቋም ጥሪ በማድረግ መግለጫ አወጣ ።

በየካቲት 27( መጋቢት 12) የፔትሮግራድ ወታደሮች በሠርቶ አደ
ሮች ላይ ተኩስ እንከፍትም ከማለታቸውም በላይ በአመጹ ከሕዝቡ ጐን
መሰለፍ ጀመሩ ። የካቲት 27 ጧት ላይ አመጹን መሳተፍ የጀመሩ ወታ
ደሮች ቁጥር ከ10,000 ያልበለጠ ሲሆን ወደ ማታ ከ60,000 በላይ ሆነ ።

በአመጹ የተካፈሉ ሠርቶ አደሮችና ወታደሮች የዛሩን ሚኒስትሮ
ችና ጀኔራሎች ማሰርና አብዮተኞችን ከእስር ቤት እየፈቱ መልቀቅ ጀ



መሩ ። የተለቀቁ የፖለቲካ እስረኞች በአብዮታዊው ትግል መሳተፍ ጀ
መሩ ።

በየጉዳናዎቹ ፣ በቤቶች ጣሪያ ላይ አውቶማቲክ ጠመንጃዎችን ይዘ
ው ከተቀመጡ ፖሊሶችና ጸጥታ አስከባሪዎች ጋር የሚደረገው የተኩስ
ልውውጥ አሁንም መካሄዱን ቀጠለ ። ነገር ግን ወታደሮች በፍጥነት ከሠ
ርቶ አደሮች ጐን ተሰለፉ ። ይህ የዛሩን ፈላጭ ቆራጭ አገዛዝ እድል ወሰነ።

በፔትሮግራድ የአብዮቱ ድል ማድረግ ዜና ወደ ሌሎች ከተሞችና
ጦር ግንባሮች በተሰራጨ ጊዜ ሠርቶ አደሮችና ወታደሮች በየቦታው የዛ
ሩን ባለ ሥልጣን ማውረድ ጀመሩ ።

የየካቲቱ የቡርዧ ዲሞክራሲያዊ አብዮት አሸነፈ ።

አብዮቱ በድል አድራጊነት ሊወጣ የቻለው «ሰላም ፣ ዳቦና ነጻነት»
የሚጠይቁ በሚሊዮን የሚቆጠሩ የወታደር ልብስ የለበሱ አርሶ አደሮችን
እንቅስቃሴ የመራው የሠርቶ አደሩ መደብ በመሆኑ ነው ። የወዛደሩ
የበላይነት ነበር ፤ የአብዮቱን ግብ መምታት የወሰነው ።

> « አብዮቱ የተካሄደው በወዛደሩ ነው ። ወዛደሩ ጀግንነቱን አሳ
> ይቷል፣ደሙን አፍስሷል ፣ ሰፊውን ምዝብርና ደሀ ሕዝብ ከጐኑ
> አሰልፏል ። » ሲል ሌኒን በአብዮቱ የመጀመሪያ ወቅት
> ጽፏል ። (ሌኒን ስብስብ ሥራዎች ፣ የሩሲያ እትም ፣ ቅጽ 20 ፣ ገጽ 23 - 4)

የ1905 የመጀመሪያው አብዮት ፣ ሁለተኛው የ1917 አብዮት ፈጣን
ድል እንዲያገኝ መንገድ ጠርጓል ።

> « የሩሲያ ወዛደር በሶስቱ የአብዮት ዓመታት 1905—07 ከፍ
> ተኛ የመደብ ጦርነት ባያደርግ ኖሮና አብዮታዊ ኃይሉን ባያ
> ሳይ የሁለተኛውን አብዮት የመጀመሪያ ደረጃ በጥቂት ቀናት
> መፈጸም አይቻልም ነበር» ሲል ሌኒን ጽፏል ( ሌኒን ምርጥ ሥራ
> ዎች የእንግሊዝኛ እትም ቅጽ 6 ገጽ 3 - 4)

በመጀመሪያዋ የአብዮት እለት ሶቪየቶች ተነሱ ። የአብዮቱ ድል
ማድረግ በሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ሶቭየቶች ድጋፍ ይወሰናል ። ያመጹ
ሠርቶ አደሮችና ወታደሮች የሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ተወካዮች ሶቪ
የቶችን መሠረቱ ። የ1905 አብዮት ሶቪየቶች የትጥቁ አመጽ አካልና እንዲ
ሁም የአዲሱ አብዮታዊ ኃይል ጥንስስ መሆናቸውን አሳይቷል ። የሶቭየቶች
ሀሳብ በሰፊው ሠርቶ አደር መደብ በመጸነሱ የተነሳ የዛሩ አገዛዝ እንደ
ተገረሰሰ ወዲያው በተግባር ላይ ዋለ ። የ1905 ሶቭየቶች የተመሰረቱት በሠ
ርቶ አደሮች ተወካዮች ብቻ ሲሆን ፣ የየካቲት 1917 ሶቭየቶች ግን በቦል
ሼቪኮች አሳሳቢነት በሠርቶ አደሮችና በወታደሮች ተወካዮች ተመሠ
ረቱ ።

ቦልሼቪኮች የሰፊውን ሕዝብ ትግል በየጐዳናዎቹ በመምራት ላይ እያሉ፣ አጐብዳጅ ፓርቲዎች ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች በሶቭየቶች ውስጥ መቀመጫ እየያዙ፣ ብዙውን ክፍል በመያዝ ላይ ነበሩ። ይህን ሁኔታ በተለይ ያመቻቸው ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች በፔትሮግራድ ጐዳናዎች በነጻ ሲንሸራሸሩ አብዛኞዎቹ የቦልሼቪክ መሪዎች በእስር ወይም በስደት ላይ መሆናቸው ነበር። ሌኒን ውጭ በስደት ላይ ነበር፣ ስታሊንና ስቬርድሎቭ ሳይቤሪያ በግዞት ላይ ነበሩ። ውጤቱም የፔትሮግራድ ሶቪየቶች የሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴው በአጐብዳጆች፣ ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች መመራቱ ነበር። በሞስኮና በሌሎችም በርካታ ከተሞች ተመሳሳይ ነበር። በኢቫኖቮ—ቮዚኒስኪ፣ ክራስኖሪያስኪና በሌሎች ጥቂት ስፍራዎች ብቻ ነበር ቦልሼቪኮች ከመጀመሪያ አንስቶ የሶቪየቶች አብዛኛው ክፍል የነበሩት።

የታጠቁ ሕዝቦች—ሠርቶ አደሮችና ወታደሮች—ተወካዮቻቸውን የሕዝቡ ሥልጣን አካል እንዲሆኑ ወደ ሶቪየት ላኩ። የሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ሶቪየቶች ሽንጐ የአብዮታዊውን ሕዝብ ጥያቄ እግቡ የሚያደርሱ መሆኑንና በመጀመሪያ ደረጃ ሰላም እንደሚመጣ አመኑ።

ነገር ግን የሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ሥልጣን ያልነበረው እምነት መጥፎ ሁኔታ ላይ ጣላቸው። ሶሻሊስት አብዮተኞችና ሜንሼቪኮች ጦርነቱን ለማቆምና ሰላም ለማምጣት ምንም ዓላማ አልነበራቸውም። አብዮቱን ጦርነቱ እንዲቀጥል ለመጠቀም አቀዱ። አብዮቱንና የሕዝቡን አብዮታዊ ጥያቄ በሚመለከት፣ ሶሻሊስት አብዮተኞችና ሜንሼቪኮች አብዮቱ እንዳበቃና አሁን ይህን አቋም ወደ « ጤናማ » ሁኔታ በመተላለፍ ከቡርዧው ጋር ጐን ለጐን ሕገ መንግሥታዊ ኑሮ መጀመር እንደሚያስፈልግ ገመቱ። ስለዚህ የፔትሮግራድ ሶቭየት ሶሻሊስት አብዮተኛና ሜንሼቪክ መሪዎች ጦርነቱን የማቆምን ጥያቄ ማለትም፣ የሰላምን ጥያቄ ወደ ጐን ለማለትና ሥልጣኑን ለቡርዧው ለማስረከብ ከፍተኛ ጥረት አደረጉ።

የካቲት 27 (መጋቢት 12) 1917፣ የአራተኛው መንግሥታዊ ዱማ ለዘብተኛ አባላት፣ ከሶሻሊስት አብዮተኞችና ከሜንሼቪኮች ጋር ስውር ስምምነት ስላደረጉ፣ በዱማው ፕሬዚዳንት፣ በመሬት ከበርቴውና በፊላጭ ቆራጩ በሮድዚያንኮ የሚመራ የመንግሥቱ ዱማ ጊዜአዊ ኮሚቴ አቋቋሙ። ከጥቂት ቀናት በኋላ፣ የመንግሥቱ ዱማ ጊዜአዊ ኮሚቴና የሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ዱማ ሶሻሊስት አብዮተኛና ሜንሼቪክ ተወካዮች መሪዎች፣ ከቦልሼቪኮች በምስጢር በመያዝ ከየካቲቱ አብዮት ቀደም ሲል፣ ዳግማዊ ዛር ኒኮላስ እንኳን የመንግሥቱ ጠቅላይ ሚኒስትር ሊያደርገው ፈልጐ በነበረው በልዑል ሊቮብ የሚመራ አዲስ፣— ጊዜአዊ የቡርዧ መንግሥት ለመመሥረት ተስማሙ። ጊዜአዊው መንግሥት የሕገ መንግሥታዊ ዲሞክራቶችን መሪ፣ ሚሊዮኮቭን፣ የጥቅምታውያንን (Octoberists) መሪ ጉችኮቭንና ሌሎችንም የካፒታሊስት መደብ ቀንደኛ ተወካዮችን፣ « የዲሞክራሲ » ተወካዮችንና ሶሻሊስት-አብዮታውያን ከረኒስኪን ያቅፋል።



የሶቪየት ሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴ ሶሻሊስት አብዮተኛና ሜንሼቪክ ተወካዮች በእንዲህ ያለ ሁኔታ ሥልጣኑን ለቡርዧው አሳልፈው ሰጡ። እንዲያውም የሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ተወካዮች ሶቪየቶች ይህን ሲሰሙ፣ የቦልሼቪኮችን ተቃውሞ ወደ ጐን በመጣል የሶሻሊስት አብዮተኞችንና የሜንሼቪኮችን መሪዎች ድርጊት ተቀበሉ።

በእንዲሁ ያለ ሁኔታ፣ ሌኒን እንዳስቀመጠው በሩሲያ « የቡርዧና ቡርዧ የሆኑ መሬት ከበርቴዎች » አዲስ የመንግሥት ሥልጣን ተመሠረተ።

ነገር ግን ከቡርዧው መንግሥት ጐን ለጐን ሌላ ኃይል — የሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ተወካዮች ሶቪየት ነበር። በሶቪየቱ ውስጥ የወታደሮች ተወካዮች በይበልጥ ለጦርነቱ የተንቀሳቀሱ አርሶ አደሮች ነበሩ። የሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ተወካዮች ሶቪየት በዛሩ አገዛዝ ላይ የሠርቶ አደሩና የአርሶ አደሩ ሕብረት፣ የሥልጣናቸው አካልና የሠርቶ አደሩ መደብና የአርሶ አደሩ አምባገነንነት አካል ነበር።

የዚህም ውጤት ልዩ የሁለት ሥልጣኖች መተሳሰር የሁለት አምባገነንነት፣ በጊዜአዊው መንግሥት በሚወከለው የቡርዧው አምባገነንነትና በሠርቶ አደሮችና በወታደሮች ተወካዮች ሶቭየት የሚወከለው የወዛደሩና የአርሶ አደሩ አምባገነንነት ነበር።

ውጤቱም የሁለት ወገን (dual) ሥልጣን ነበር።

በመጀመሪያ ላይ አብዛኛዎቹ ሶቪየቶች ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች የሆኑት ለምንድነው ?

ድል አድራጊ ሠርቶ አደሮችና አርሶ አደሮች በፈቃዳቸው ሥልጣን ለቡርዧው መልቀቃቸውን እንዴት ብሎ መግለጽ ይቻላል ?

ሌኒን በሚሊዮን ከሚቆጠሩ ሕዝቦች ፡ የፖለቲካ ልምምድ የሚያጥራቸው፣ ተቀስቅሰው ወደ ፖለቲካ ሥራ እንዲገቡ መገፋፋታቸውን በመጠቆም ገልጾታል። ከነዚህም አብዛኞዎቹ ትንንሽ ንብረት የነበራቸው፣ አርሶ አደሮች፣ በቅርቡ አርሶ አደር የነበሩ ሠርቶ አደሮች፣ በቡርዧውና በወዝ አደር መካከል የሚዋልሉ ሕዝቦች ነበሩ። ሩስያ በዚያን ጊዜ ከሁሉም ትላልቅ የአውሮፓ ሀገሮች እጅግ ንዑስ ከበርቴ የነበረች ናት። በዚህ ሀገር ውስጥ፣ « ትልቅ የንዑስ ከበርቴ ማእበል በቁጥር ብቻ ሳይሆን በርእዮተ ዓለምም የመደብ ንቃት ያለውን ወዛደር ወደ ራሱ ሳበ፣ ማለትም ብዙ ሠርቶ አደሮችን በንዑስ ከበርቴ ፖለቲካ አመለካከት በከላቸው» (ሌኒን ምርጥ ሥራዎች፣ የእንግሊዝኛ እትም፣ ቅጽ 6፣ ገጽ 49)

ይህ መሠረታዊ የንዑስ ከበርቴ ማእበል ነበር ንዑስ ከበርቴ ሚንሼቪኮችንና ሶሻሊስት አብዮተኛ ፓርቲዎችን ወደፊት የገፋቸው ።

ሌላው ምክንያት በጦርነቱ ጊዜ በወዛደሩ ውስጥ የተደረገው ለውጥና በአብዮቱ መጀመሪያ ላይ ወዛደሩ በቂ የመደብ ንቃትና ድርጅት ማጣቱ እንደነበረ ሌኒን ጠቁሟል ። በጦርነቱ ወቅት በወዛደሩ በራሱ ውስጥ ትልቅ ለውጥ ነበር ። ወደ 40 ከመቶ መደበኛ ሠራተኞች ለጦርነት ተወስደዋል ። ብዙ ለወዝ አደሩ ሳይኮሎጂ ባዕድ የነበሩ ትንንሽ ባለንብረቶች ባለሞያዎችና ባለሱቆች ወደ ጦርነቱ እንዳይንቀሳቀሱ በመፍራት ፋብሪካዎች ውስጥ ተቀጠሩ ።

ይህኛው የንዑስ ከበርቴ ክፍል ነበር ፣ የንዑስ ከበርቴ ፖለቲከኞችን ሚንሼቪኮችንና ሶሻሊስት አብዮተኞችን ለማሳደግ ለም አፈር የሆነው ።

በዚህ የተነሳ ነው ፣ ብዙ ሰዎች በፖለቲካ ልምድ የሌላቸው ፣ ወደ ንዑስ ከበርቴዎች ሥራዎች ውስጥ በመግባት ፣ በመጀመሪያው የአብዮት ድል በመሳከር ፣ በመጀመሪያው ወራት ራሳቸውን በአጉብዳጅ ፓርቲዎች ሥር የጣሉትና ለቡርዧው የመንግሥትን ሥልጣን መልቀቅ የሶቪየቶችን ሥራ አያደናቅፍም የሚል ከንቱ እምነት የተከተሉት ።

ከቦልሼቪክ ፓርቲ ፊት የተደቀነው ተግባር በትእግሥት በማስረዳት ፣ የጊዜአዊውን መንግሥት ኢምፔሪያሊስት ባህሪ እንዲገነዘብ የሰፊውን ሕዝብ ዓይን መክፈት ፣ የሶሻሊስት አብዮተኞችንና የሚንሼቪኮችን ደባ ማጋለጥ ፣ እንዲሁም ጊዜአዊው መንግሥት በሶቪየቶች መንግሥት ካልተተካ በቀር ሰላም ሊመጣ እንደማይችል ማሳየት ነበር ።

ለዚህም ሥራ የቦልሼቪክ ፓርቲ ራሱን በከፍተኛ ኃይል አሰማራ ። ሕጋዊ መጽሔቶቹን ማውጣት ቀጠለ ። ፕራቭዳ ጋዜጣ ከየካቲቱ አብዮት በኋላ በአምስተኛው ቀን ፔትሮግራድ ውስጥ መጣ ፣ ሶሻል ዲሞክራት ከጥቂት ቀናት በኋላ በሞስኮ ወጣ ። ፓርቲው በለዘብተኛ ቡርዧው በሚንሼቪኮችና በሶሻሊስት አብዮተኞች ላይ እምነት በማጣት ላይ ያለውን ሰፊ ሕዝብ መምራቱን ቀጠለ ። ከሠርቶ አደሩ መደብ ጋር በአንድነት የመሥራቱን አስፈላጊነት ለወታደሮችና ለአርሶ አደሮች በጽሞና አስረዳ ። አብዮቱ ወደፊት ካልገፋና የቡርዧው ጊዜአዊ መንግሥት በሶቭየቶች መንግሥት ካልተተካ አርሶ አደሮች ሰላምም ሆነ መሬት ማግኘት እንደማይችሉ ገለጸላቸው ።

## አጭር ድርሞ ።

በካፒታሊስት ሀገሮች መካከል በነበረው ያልተመጣጠነ እድገት ፣ በዋነኛ ሀይሎች መካከል የኃይል ሚዛን በመዛባቱ ፣ ኢምፔሪያሊስቶች በጦርነት ዓለምን እንደገና ለመከፋፈልና አዲስ የኃይል ሚዛን ለመፍጠር በመፈለጋቸው የተነሳ የኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት መጣ ።



የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ፓርቲዎች የሠርቶ አደሩን መደብ ፓርቲዎች ዓላማ ባይክዱ ኖሮ ፣ የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ስለ ጦርነቱ ያሳለፉቸውን ውሣኔዎች ባይጥሱ ኖሮ ፣ የሠርቶ አደሩን መደብ በኢምፔሪያሊስት መንግሥታቸውና በጦርነት ፈላጊዎች ላይ እንዲነሱ ለማድረግ ቢደፍሩ ኖሮ ጦርነቱ ይህን ያህል አጥፊ መሆን ፣ ምናልባትም ይህን ዓይነት መልክ መያዝ ባልቻለም ነበር ።

የሶሻሊዝምና ለዓለም አቀፋዊነት ዓላማ ታማኝ ሆኖ በራሱ ኢምፔሪያሊስት መንግሥት ላይ የርስ በርስ ጦርነት ያደራጀ የቦልሼቪክ ፓርቲ ብቻ ነበር ። ሌሎች የሁለተኛው ዓለም አቀፍ ፓርቲዎች በሞላ ፣ በመሪዎቻቸው በኩል ከቡርዧው ጋር በመተሳሰር ፣ ራሳቸውን በኢምፔሪያሊዝም ጫማ ስር አድርገው ወደ ኢምፔሪያሊስቶች ገቡ ።

ጦርነቱ ፣ የአጠቃላዩ የካፒታሊዝም ቀውስ ነጸብራቅ በመሆኑ ይህንኑ ቀውስ ይበልጥ አካረረ ፣ የዓለምን ካፒታሊዝምም አዳከመ ። የካፒታሊዝምን ድክመት ለመጠቀም የሩስያ ሠርቶ አደሮችና የቦልሼቪክ ፓርቲ በዓለም የመጀመሪያዎቹ ነበሩ ። በኢምፔሪያሊስቱ ግንባር አለመግባባት እንዲፈጠር አደረጉ ፣ ዛሩን ገረሰሱ ፣ የሠርቶ አደሮችና የወታደሮች ተወካዮችን ሶቪየቶች አቋቋሙ ።

በመጀመሪያው የአብዮቱ ድል በመሳከርና ከአሁን በኋላ ሁሉ ነገር የተስተካከለ ይሆናል በሚለው በሚንሼቪኮችና በሶሻሊስት አብዮተኞች አስተሳሰብ በመታለል ፣ እጅግ በርካታ ንዑስ ከበርቴዎች ፣ ወታደሮች ፣ ሰራተኞችም ጭምር እምነታቸውን በጊዜአዊው መንግሥት ላይ ጣሉ ፣ ደገፉትም ።

የቦልሼቪክ ፓርቲ በመጀመሪያው የአብዮቱ ድል ለተሳከሩት ሰፊ ሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ፣ የአብዮቱ የተሟላ ድል ገና ሩቅ እንደሆነ ፣ ሥልጣኑ በቡርዧው ጊዜአዊ መንግሥት እጅ እስካለ ድረስ ፣ ሶቪየቶች በአጉብዳጆች ሚንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች ስር እስካሉ ድረስ ፣ ሕዝቡ ዳቦም ሆነ መሬት ወይም ሰላም ማግኘት እንደማይችልና ስለሆነም የተሟላ ድል ለማግኘት አንድ ተጨማሪ እርምጃ ተወስዶ ሥልጣን ወደ ሶቪየቶች መተላለፍ እንዳለበት የመግለጹ ኃላፊነት ከፊታቸው ተደቀነ ።

## ምእራፍ ሰባት ።

# የቦልሼቪክ ፓርቲ ለጥቅምቱ ሶሻሊስት አብዮት የዝግጅትና የትግባር መግለጫ ወቅት

(ሚያዝያ 1917—1918)

### 1/ ከየካቲቱ አብዮት በኋላ በሀገሪቷ ውስጥ የነበረው ሁኔታ ፤ ፓርቲው ከሕቡእ በመውጣት ግልጽ ፖለቲካዊ ሥራዎች ወደ ማከናወን መሸጋገሩ ፤ የሌኒን ወደ ፔትሮግራድ መምጣት ፥ የሌኒን የሚያዝያው በኩረ ሀሳብ ፥ ወደ ሶሻሊስት አብዮት ለሚደረገው ሽግግር የፓርቲው መመሪያ ፦—

የድርጊቶች ሂደትና የጊዜያዊው መንግሥት ባሕርያት ከእለት ወደ ዕለት የቦልሼቪኮችን መስመር ሀቀኛነት አዳዲስ ማረጋገጫዎችን በማቅረብ አረጋገጠ ። ጊዜያዊ መንግሥት ለሕዝቡ ሳይሆን ለሕዝቡ ጠላቶች ፥ ለሰላም ሳይሆን ለጦርነት የቆመና ለሕዝቡ ሰላም ፥ መሬት ወይም ዳቦ ለመስጠት የማይፈልግና የማይችል መሆኑን የሚመሰክሩ ማረጋገጫዎች እየጨመሩ ሄዱ ። ቦልሼቪኮች የሰጡት የማብራሪያ ሥራ የለማ አፈር አገኘ ።

ሠራተኞቹና ወታደሮች የዛሩን መንግሥት ገርሥሰው መጣልና የዘውዳዊውን አገዛዝ ሥሮችና ቅርንጫፎች ደብዛውን ሲያጠፉ ጊዜያዊው መንግሥት ግን ዘውዳዊውን መንግሥት ለማቆየት በግልጽ ይጥር ነበር ። በመጋቢት 2 ቀን 1917 ዓ. ም. ጉችኮቭና ሹልጂ ዛሩን ሂደው እንዲያነጋግሩ በሚስጥር ተላኩ ። ቡርዧዎች ሥልጣኑ የኒኩላስ ሮማኖቭ ወንድም ለሆነው ለሚካኤል ለመስጠት ይፈልጋሉ ። ይሁን እንጂ የምድር ባቡር ሠራተኞች ስብሰባ ላይ ጉችኮቭ «ንጉሥ ሚካኤል ለዘላለም ይኑር» በማለት ንግግሩን ሲያበቃ ሠራተኞቹ ጉችኮቭ አሁኑኑ ተይዞ እንዲመረመር ሲሉ ጥያቄ አቀረቡ ። « አጭር ሌባ ከረጅሙ ሌባ አይለይም » በማለት ተቃወሙ ።

ሠራተኞቹ ዘውዳዊው አገዛዝ እንዲያንሰራራ በምንም ዓይነት እንደማይፈቅዱ ግልጽ ነበር ።

ጭቁን ወዝአደሮችና አርሶ አደሮች ለአብዮቱ ደማቸውን ሲያፈሱ ጦርነት ያከትማል ብለው ተስፋ በማድረግ ነበር ። ለዳቦና ለመሬት ሲታገሉ ምጣኔ-ሀብታዊው ቀውስ መፍትሔ እንዲያገኝ ብርቱ እርምጃ እንዲደረግ በመጠየቅ ነበር ። ይሁንና ጊዜያዊው መንግሥት ለነዚህ እጅግ አንገብጋቢ የሕዝብ ጥያቄዎች አሁንም መልስ መስጠት አልቻለም ። የካፒታሊስትና የመሬት ከበርቴው ተወካዮች እንደሚያደርጉት እነርሱም



አደረጉ ። መሬት እንዲሰጣቸው የሚፈልጉትን ገበሬዎች ፍላጐት ለማርካት ወይም ለሠራተኛው መደብ ዳቦ ለመስጠት ይህ መንግሥት ፈጽሞ ሀሳብ የለውም ። ምክንያቱም ይህን ለመፈጸም ከፈለገ የትላልቅ የእህል ነጋዴዎችን ፍላጐት መጣስና ከመሬት ከበርቴዎችና ከሀብታም ገበሬዎች በተገኘው መንገድ ሁሉ እህል መውሰድ ይኖርበታል ። ይህ መንግሥት ደግሞ ይህንን ለማድረግ አይፈልግም ። ምክንያቱም መንግሥቱ ራሱ ከዚህ መደብ ፍላጐት ጋር በጽኑ የተሳሰረ ነውና ። ወይንም ለሕዝቡ ሰላምን መስጠት አይችልም ። ከእንግሊዝና ከፈረንሣይ ኢምፔሪያሊስቶች ጋር የተሳሰረ እንደመሆኑ መጠን ጊዜያዊው መንግሥት ጦርነቱን ለማቆም አንዳችም ሀሳብ የለውም ። በተቃራኒው የአብዮቱን አጋጣሚ በመጠቀም ሩስያ በኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት ውስጥ ብርቱ ተሳታፊ እንድትሆን ይጥራል ። ኢምፔሪያሊስት መሆኑን ለማረጋገጥ ኮንስታንቲኖፕል ፥ የባህር ወሽመጡንና ጋሊሺያን ለመያዝ እቅድ አውጥቶ ነበር ።

ሕዝቡ በጊዜያዊ መንግሥት መመሪያ ላይ ያለው እምነት ወዲያውኑ እንደሚያከትም በጉልህ የሚታይ ነበር ።

ከየካቲቱ አብዮት በኋላ የተመሠረተው ሁለት ወገን ስልጣን ሊቀጥል እንደማይችል ግልጽ እየሆነ መጣ ። የድርጊቶች ሂደት ሥልጣኑ በአንድ ወገን ማለትም በጊዜያዊው መንግሥት ወይንም በሶቪየቶች መጠቃለል ማስፈለጉን ጠቆሙ ።

የሜንሼቪኮችና የሶሻሊስት አብዮተኞች ታራቂ መርሆ አሁንም ቢሆን በሰፊው ሕዝብ ውስጥ ድጋፉን አላጣም ። « ሕገመንግሥታዊው ሸንጐ ተመስርቶ ማናቸውንም ነገር በሰላማዊ መንገድ ያስተካክለዋል » ጦርነቱ መንግሥቱን ለመጠበቅ አስፈላጊ በመሆኑ እንጂ ሌላውን ለመውረር አይደለም ። በሚል እምነት ውስጥ አሁንም ጥቂት ሰራተኞችና እንዲያውም አያሌ ወታደሮችና ገበሬዎች ይገኛሉ ። እንደነዚህ ያሉትን ሰዎች ሌኒን በቅንነት የተሳሳቱ የጦርነቱ ደጋፊዎች ብሎ ይጠራቸዋል ። እነዚህ ሰዎች ከተስፋና ከማባበያዎች አንዱ የሆነውን የሶሺያሊስት አብዮታውያንንና የሜንሼቪኮችን መርሆ እስካሁን ድረስ ትክክል መመሪያ ነው ብለው ያስባሉ ። ነገር ግን የድርጊቶች ሂደትና የጊዜያዊው መንግሥት ባህርይ በየእለቱ እንደሚያሳዩትና የሶሻሊስት አብዮተኞችና የሜንሼቪኮች ታራቂ መመሪያ የማዘግያና አስተሳሰብ የመጋረጃ ማታለያ መሆኑን እንደሚያረጋግጡት ተስፋውና ማባበያዎቹ ውጤት እንደማይኖራቸው (እንደማይፈጸሙ) ሳይታለም የተፈታ ነበር ።

ጊዜያዊው መንግሥት የሰፊውን ሕዝብ አብዮታዊ እንቅስቃሴ በመቃወም የስርቆሽ ትግል በማድረግና ስውር ደባዎችን በአብዮቱ ላይ በመፈጸም ብቻ አይወሰንም ። አንዳንድ ጊዜ « ዲሲፕሊን ለማስፈን » በዲሞክራሲያዊ አርነት ላይ በተለይም ደግሞ በወታደሮች መሀከል «ስርዓት ለማስከበር» ግልጽ ማጥቃት እንዲወስድ ይገደዳል ። ይህን ማድረግ

ማለት ከቡርዧው ፍላጐት ጋር በሚጣጣሙ ፈለጐች ውስጥ አብዮቱን
መምራት ማለት ነው ። ነገር ግን በዚህ አቅጣጫ ያደረገው መላው ጥረት
ከሸፈና ሕዝቦች ዲሞክራሲያዊ እርንተቻቸውን በጉጉት በተግባር ተሮ
ገሙት ። እነርሱም ፣ የንግግር ፣ የጽሁፍ ፣ የድርጅት ፣ የስብሰባና የሰላማዊ
ሰልፍ ነጻነቶች ናቸው ። ሠራተኞችና ወታደሮች በሀገሪቱ ፖለቲካዊ ህይ
ወት ውስጥ ንቁ ተሳትፎ ለማድረግ እንዲችሉ ፣ የሁኔታው እውነተኛ
ግንዛቤ እንዳይኖራቸውና ቀጥሎ ምን መደረግ እንደነበረበት ለመወሰን
አዲስ ያገኙትን ዲሞክራሲያዊ መብቶች ሙሉ በሙሉ ለመጠቀም ከፍ
ተኛ ጥረት አደረጉ ።

ከየካቲት አብዮት በኋላ የዛሩ አገዛዝ አድህሮት የመጨረሻውን ደረጃ
ቢያዘበት በዚያ ሁኔታ ውስጥ በሕቡእ ይሠራ የነበረው የቦልሼቪክ ፓርቲ
ከህቡእነቱ ወጥቶ ፖለቲካዊና ድርጅታዊ ሥራዎችን ግልጽ በሆነ መንገድ
ማሳደጉን ጀመረ ። በዚያን ወቅት የቦልሼቪክ አባላት ቁጥር ከ40,000
ወይም ከ45,000 የሚበልጥ አልነበረም ። ይሁን እንጂ እነዚህ ሁሉ በትግሉ
ውስጥ እንደ ብረት የጠነከሩ ቆራጥ አብዮተኞች ነበሩ ። የፓርቲ ኰሚቴ
ዎች በዲሞክራሲያዊ ማእከላዊነት መመሪያ መሠረት እንደገና ተደራጁ ።
መላው የፓርቲው አካላት ፤ ከታች እስከ ላይ በምርጫ የተካሄዱ ነበሩ ።

ፓርቲው ሕጋዊ ሕልውናውን በጀመረበት ወቅት በአባላቱ መሀ
ከል የነበረው ልዩነት ግልጽ ሆነ ። ካሜኔቭና አያሌ የሞስኮ ድርጅት ሠራ
ተኞች ለምሳሌ ያህል ራይኩቭ ፣ ቡብኖቭና ኖጂን ጊዜያዊውን መንግሥ
ትና የተከላካዮችን መርሆ በተወሰኑ ሁኔታዎች በመደገፍ ከፊል ሜንሼ
ቪክ አቋም ያዙ ። ገና ከእስር የተመለሰው ስታሊን ሞልቶቭና ሌሎችም
ከፓርቲው አብዛኛው ወገን ጋር በመሆን በጊዜያዊው መንግሥት ላይ
እምነት የማጣት መርሆን በማራመድ ተከላካይነትን በመቃወምና ለሰ
ላም የኢምፔሪያሊስቶችን ጦርነት በመቃወም ንቁ የሆነ ትግል እንዲደ
ረግ ጥሪ አደረጉ ። አንዳንድ የፓርቲው ሠራተኞች በሁኔታው ወላወሉ ።
ይህ ደግሞ የፖለቲካዊ ኋላቀርነታቸው መግለጫ ፣ ለረጅም ጊዜያት በእ
ስር ቤትና በግዞት የመቆየታቸው ውጤት ነበር ።

የፓርቲው መሪ ፣ የሌኒን አለመኖር ለሁኔታው አንድ ስሜት ሰጥቶት
ነበር ። ከረዥም የስደት አመታት በኋላ ሚያዝያ 3,1917 ዓ. ም.
ሌኒን ወደ ሩሲያ ተመለሰ ።

የሌኒን መድረስ ለአብዮቱና ለፓርቲው ከፍተኛ ጠቀሜታ ነበር ።
በዚህን ጊዜ በስዊዘርላንድ ሆኖ ስለአብዮቱ የመጀመሪያ ዜና እን
ደደረሰው አስመልክቶ ለፓርቲውና ለሩስያ ሠራተኞች «ደብዳቤዎች
ከአፋር» የተሰኘውን ደብዳቤ ጻፈ ።

« ሠራተኞች ፣ የዛሩን አገዛዝ በመቃወም በተደረገው የርስበርስ ጦር
ነት ውስጥ የወዝአደሩን ጀግንነት ፣ የሕዝቡን ጀግንነትና ተአምራዊነት



አሳይታችኋል ። ለሁለተኛው የአብዮት ደረጃ ድል ጥርጊያ መንገድ ለመ
ክፈት የወዝአደሩ ድርጅት ፣ የመላው ሕዝብ ድርጅት ፤ የድርጅት ተአም
ሮችን ማሳየት ይኖርባችኋል ። » (የሌኒን ስብስብ ሥራዎች እንግሊዝኛ እትም
ሞስኮ 1947 ዓ. ም. ቅጽ 1 ገጽ 741)

ሚያዝያ ሶስት ቀን ምሽት ላይ ሌኒን ፔትሮግራድ ገባ ። በሺህ የሚ
ቆጠሩ ሠራተኞች ፣ ወታደሮችና መርከበኞች በፊንላንድ የባቡር ጣቢያና
በጣቢያው አደባባይ እንኳን ደህና ገባህ ለማለት ተሰብስበው ነበር ። ሌኒን
ከባቡሩ ላይ ሲወርድ የነበራቸውን ስሜት ለመግለጽ ፍጹም ያዳግታል ።
ሕዝቡ የሌኒንን ትከሻ በመያዝ ከፍ አደረጉትና ወደ ጣቢያው የእንግዳ
መቆያ ክፍል ይዘውት ሄዱ ። እዚያም ሜንሼቪኮች ቺኮሄይድዚና ስኩብሌ
ቭ የፔትሮግራድን ሶቪየቶች በመወከል እነርሱና ሌኒን «የጋራ ሊግ» የሚ
መሰርቱበትን « ተስፋ የገለጡበት » « የመቀበያ » ንግግር አደረጉ ። ይሁን
እንጂ ሌኒን ሊያዳምጣቸው አልቆመም ገፍትሮአቸው በማለፍ ወደ ሰፊው
ሠራተኞችና ወታደሮች ሄደ ። በብረት ለበስ መኪና ላይ በመውጣት ለሶ
ሻሊስት አብዮት ድል እንዲታገሉ ለሰፊው ሕዝብ ጥሪ ያደረገበትን ዝነኛ
ንግግሩን አደረገ ። ከረጅም ዓመት እስራት በኋላ ሌኒን የመጀመሪያው
ንግግሩን «ሶሻሊስት አብዮት ለዘላለም ይኑር» በሚሉ ቃላት ደመደመ ።

ወደሩስያ ከተመለሰ ወዲህ ሌኒን በአብዮታዊ ሥራዎች ውስጥ በከ
ፍተኛ ደረጃ ራሱን አስገባ ። በገባ በማግስቱ በቦልሼቪኮች ስብሰባ ላይ ጦር
ነትና አብዮት በሚሉ ርእሶች ዘገባ አቀረበ ፣ እንዲሁም ሜንሼቪኮችና
ቦልሼቪኮችም በሚገኙበት ስብሰባ ላይ የዚህን ዘገባ በኩረ ሀሳብ ደግሞ
አቀረበ ።

የሌኒን ዝነኛው የሚያዝያው በኩረ-ሀሣብ ከቡርዧው ወደ ሶሻሊስት
አብዮት ለተደረገው ሽግግር ፓርቲውና ወዝአደሩ የጠራ አብዮታዊ
መስመር እንዲኖራቸው አድርጐ ነበር ።

የሌኒን በኩረ-ሀሳብ ለፓርቲውና ለአብዮቱ ተከታታይ ተግባሮች
በጣም ሰፊ ቁም ነገር ያዘለ ነበር ። በሀገሪቷ ሕይወት ውስጥ አብዮት
ከፍተኛ ለውጥ ያስከትላል ። የዛሩ አገዛዝ መፈንገልን ተከትሎ የመጣው
አዲስ የትግል ሁኔታ በጀግንነትና በሙሉ እምነት በአዲሱ ጐዳና
ለመንዝ ፓርቲው አዲስ መሥመር ያስፈልጉታል ። የሌኒን በኩረ-ሀሳብ
ለፓርቲው ይህን አስፈላጊ መሥመር አበርክቷል ።

የሚያዚያው የሌኒን በኩረ-ሀሳብ ከቡርዧው ዲሞክራሲ ወደ ሶሻ
ሊስት አብዮት ፣ ከመጀመሪያው የአብዮት ደረጃ ወደሁለተኛው የአብ
ዮት ደረጃ—ወደ ሶሻሊስት የአብዮት ደረጃ ለመሸጋገር ፓርቲው ለሚያ
ደርገው ትግል ብልህ የሆነ እቅድ ዘርግቷል ። መላው የፓርቲው ታሪክ
ለዚህ ታላቅ ተግባር አዘጋጅቶታል ። ገና ከበፊቱ በ1905 ዓ. ም. ሌኒን በዲሞ
ክራሲያዊ አብዮት ውስጥ የሶሻል ዲሞክራሲ ሁለት ታክቲኰች በተሰ

ኘው ጽሁፉ የዛሩ አገዛዝ ተገርስሶ ከወደቀ በኋላ ወዝአደሩ የሶሻሊስትን አብዮት ለማምጣት ትግሉን መቀጠል አለበት ብሏል ። በአሁኑ በኩረ ሀሳብ ውስጥ አዲስ ነገር ቢኖር ወደ ሶሻሊስት አብዮት ለሚደረገው የመጀመሪያ ደረጃ ሽግግር ተጨባጭ ንድፈ-ሀሳባዊ መሠረት ያለው ፕላን መስጠታቸው ነበር ።

በምጣኔ-ሀብቱ መስክ የሽግግሩ እርምጃ መሬትን በመንግሥት ቁጥጥር ሥር ማድረግና ሁዳዳዊ ባለቤትነትን ማስቀረት ፤ መላውን ባንኮች በአንድ ብሔራዊ ባንክ ሥር አዋህዶ በሠራተኞች ሶቪየት ተወካዮች ሥር ማድረግና በማህበራዊ ምርትና በምርት ማከፋፈያዎች ላይ ቁጥጥር ማድረግ ነበሩ ።

በፖለቲካዊ መስክ ፤— ሌኒን ከፓርላሜንታዊ ሪፐብሊክ ወደ ሶቭየቶች ሪፐብሊክ ሽግግር መደረግ እንዳለበት አሳስቧል ። ይህ በማርክሲዝም ንድፈ-ሀሳብና ተግባር ውስጥ እጅግ ጠቃሚ የሆነ የእድገት እርምጃ ነው ። እስካሁን ድረስ ወደ ሶሻሊዝም ለሚደረገው ሽግግር ማርክሲስት ንድፈ-ሀሳባውያን ፓርላሜንታዊውን ሪፐብሊክ የሽግግሩ ምርጥ ፖለቲካዊ መልክ አድርገው ይመለከቱታል ። አሁን ግን ሌኒን ከካፒታሊዝም ወደ ሶሻሊዝም ሽግግር በሚደረግበት ወቅት ለኅብረተሰብ እጅግ ተስማሚ ፖለቲካዊ የድርጅት መልክ ተደርጐ መወሰድ ያለበት ፓርላሜንታዊ ሪፑብሊኮች ሳይሆን ያንን በሚተካው ሶቪየት ሪፐብሊክ መሆን አለበት ሲል አሳሰበ ።

«የአሁኑ የሩስያ ሁኔታ የተለየ ገጽታ» ይላል የሌኒን በኩረ-ሀሳብ ፤ «የወዝአደሩ መደባዊ ንቃተ ሕሊናና ድርጅቱ በቂ ባለመሆኑ ምክንያት ሥልጣን በቡርዧው መዳፍ ውስጥ ሊገባ ከቻለበት ከአብዮቱ የመጀመሪያ ደረጃ ፤ ስልጣን በወዝአደሩና በደሀ ገበሬ የኅብረተሰብ ክፍል እጅ የግድ በሚያስገባው ወደ የአብዮቱ ሁለተኛ ደረጃ መሸጋገርን የሚያሳይ ነው » (እላይ በተጠቀሰው መጽሀፍ ቅጽ 2 ገጽ 18)

እናም በመቀጠል ፤—

« ፓርላሜንታዊ ሪፐብሊክ ሳይሆን — ከሠራተኞች ሶቪየቶች ተወካዮች ወደ ፓርላሜንታዊ ሪፑብሊክ መመለስ የኋሊዮሽ ጉዞ ይሆናል ፤ ነገር ግን በመላው ሀገሪቱ ፤ ከታች እስከላይ የእርሻ ሰራተኞች የገበሬዎች ተወካዮችና የሠራተኞች ሶቪየቶች ሪፑብሊክ እንጂ » (እላይ በተጠቀሰው መጽሀፍ ገጽ 18)

በአዲሱ መንግሥት ፤ በጊዜያዊው መንግሥት ሥር ጦርነቱ ወደ የኢምፔርያሊስት ጦርነት መለወጡን ቀጥሏል ይላል ሌኒን ። ይህንን ለሰፊው ሕዝብ ማብራራትና ቡርዧዎች ካልተገረሰሱ በቀር ጦርነቱን በስግብግቦች ሰላም ሳይሆን በእውነተኛው ዲሞክራሲያዊ ሰላም ለመፈጸም እንደማይቻል ማሳየቱ የፓርቲው ተግባር ነው ።



የጊዜአዊውን መንግሥት አስመልክቶ ሌኒን የሰነዘረው መፈክር «ለጊዜያዊው መንግሥት አንዳችም ድጋፍ የለም ! » የሚል ነበር ።

ሌኒን ከዚህም በላይ በበኩረ-ሀሳቡ ውስጥ አሁንም ቢሆን በሶቪየቶች ውስጥ ፓርቲያችን ጥቂቱ ክፍል መሆኑን ያም ማለት ሶቭየቶች በወዝአደሩ ላይ የቡርዧውን ተጽእኖ በሚያሳድሩ በሜንሼቪኮችና በሶሻሊስት አብዮተኞች ሕብረት ተጽእና ሥር መውደቃቸውን ጠቆመ ። ስለሆነም የፓርቲው ተግባር እንደሚከተለው ይጠቃለላል ።

« የሠራተኞች ሶቪየቶች ተወካዮች የአብዮታዊው መንግሥት አንድ ብቸኛ መልክ መሆኑን ለሰፊው ሕዝብ መግለጽ አለብን ። ስለሆነም ተግባራችን ይህ መንግሥት ለቡርዧው ተጽእኖ ራሱን እስካላስገዛ ድረስ በተለይ ከሰፊው ሕዝብ ተግባራዊ ፍላጐት ጋር በማዛመድ የነርሱን የታክቲኮች ስህተት በትእግስት በዘዴና ባለማቋረጥ ማሳወቅ ነው ። እኛ ጥቂቶች እንደመሆናችን መጠን በመተቸትና ስህተቶችን በማጋለጡ ተግባር እንሰማራለን እንዲሁም ከዚሁ ጋር መላውን የመንግሥት ሥልጣን ወደ ሠራተኞች ሶቪየቶች ተወካዮች እንዲተላለፍ እናሳስባለን ። » (ሌኒን ስብስብ ሥራዎች ሩሲያ እትም ቅጽ 20 ገጽ 88)

ይህ ማለት ሌኒን በዚያን ወቅት የሶቪየቶችን እምነት ባተረፈው ጊዜያዊ መንግሥት ላይ የአመጽ ጥሪ ማድረግ አልነበረም ፤ ያም ማለት የሚፈልገው የመንግሥቱን መገርሰስ አልነበረም ። ነገር ግን የርሱ ፍላጐት በሶቭየቶች ውስጥ በማብራሪያና በምልመላ ተግባር በመገልገል አብዛኛውን ቁጥር ለመያዝና የሶቭየቶችን መርሆ ለመቀየር ብሎም በሶቭየቶች በኩል ጥምረቱን የመንግሥቱን ፖሊሲ ለመለወጥ ነበር ።

ለአብዮቱ ሰላማዊ እድገት የታሰበው መስመር ይህ ነበር ።

ሌኒን ከዚህም በላይ «የተበከለው ሸሚዝ» ወልቆ መጣል አለበት ፤ ፓርቲውም ከእንግዲህ ወዲህ ሶሻል—ዲሞክራቲክ ፓርቲ ተብሎ መጠራት የለበትም ሲል አሳሰበ ። የሁለተኛው አለም አቀፍ ፓርቲዎችና የሩስያ ሜንሼቪኮች ራሳቸውን ሶሻል—ዲሞክራቲክ ብለው ይጠራሉ ። ይህ ስም በአድርባዮች በሶሻሊዝም ከዳተኞች የተበከለና የሀፍረት ማቅ የተከናነበ ነው ። የቦልሼቪኮች ፓርቲ ማርክስና ኤንግልስ ለፓርቲያቸው በሰጡት ስያሜ ማለትም ኰሚኒስት ፓርቲ እየተባለ መጠራት እንዳለበት አሳሰበ ። የቦልሼቪኮች ፓርቲ ዘላቂውን ግብ ኰሚኒዝምን ለመመስረት በመሆኑ ይህ ስም ሳይንሳዊ በሆነ መንገድ እውነት ነው ። የሰው ዘር በቀጥታ ከካፒታሊዝም ወደ ሶሻሊዝም ብቻ ይሸጋገራል ። ይህም ማለት የምርት መገልገያዎች የጋራ ባለቤትነት ወደሆኑበትና እያንዳንዱ በሰራው መጠን ምርቶችን ወደሚከፋፈልበት ማለት ነው ። ሌኒን ሲናገር ፓርቲያችን አርቆ ይመለከታል ፤ ሶሻሊዝም በማይቀር ሁኔታ ቀስ በቀስ « ከያንዳንዱ እንደየችሎታው ፤ ለያንዳንዱ እንደ የፍላጐቱ» ወደሚለው ወደ ኮሚኒስት መርህ ይሸጋገራል ።

በመጨረሻም ሌኒን በበኩረ ሀሳቡ ላይ አዲስ ዓለም-አቀፍ ከአድርባዮችና ከሶሻል ትምክህተኞች ነፃ የሆነ ሶስተኛው ኰሚኒስት ዓለም-ዓቀፍ እንዲመሠረት ጠየቀ ።

የሌኒን በኩረ ሀሳብ የቡርዧዎችን፤የሜንሼቪኮችንና የሶሻሊስት አብዮተኞችን የቅዠት ጩኸት አጋልጧል ።

ሜንሼቪኮች « አብዮቱ በአደጋ ላይ ወድቋል » በሚል ማስጠንቀቂያ የሚጀምረውን አዋጅ አወጡ ። በሜንሼቪኮች አስተሳሰብ አደጋው ቦልሼቪኮች ሥልጣን ወደ ሰራተኞችና የወታደሮች ሶቪየቶች ተወካዮች እጅ እንዲሸጋገር በመጠየቃቸው እውነትነት ላይ ያረፈ ነበር ።

ፕሌክሀኖቭ ዩዲንስቲቭ (አንድነት) በተሰኘው ጋዜጣው ላይ የሌኒንን ንግግር «የቅዠት ንግግር» በማለት ገለጸው ። «ፕሌክሀኖቭ በተጨማሪም ሌኒን ብቻውን ከአብዮቱ ውጪ ይቀራል፣ እኛም የራሳችንን መንገድ ይዘን መጓዝ አለብን » ያለውን የሜንሼቪኮችን ቺካሄይድዝ ቃላት በመጥቀስ ጻፈ ።

በሚያዝያ 14 ቀን የፔትሮግራድ ከተማ የቦልሼቪክ ጉባኤ ተካሂዶ ነበር ። ጉባኤው የሌኒንን በኩረ ሀሳብ ተቀበለና የተግባሩ መሠረት አደረገው ።

በአጭር ጊዜ ውስጥ የፓርቲው የአካባቢ ድርጅቶች የሌኒንን በኩረ ሀሳብ አጸደቀ ።

ከአንዳንድ ግለሰቦች ለምሳሌ እንደነካሜኔቭ፣ራይኩቭና ፓያታኰቭ በስተቀር መላው ፓርቲ የሌኒንን በኩሩ ሀሳብ በታላቅ ደስታ ተቀበለው።

2/ የጊዜያዊው መንግሥት መናጋት መጀመር፤ የሚያዚያው የቦልሼቪክ ፓርቲ ጉባኤ ፤

ቦልሼቪኮች አብዮቱን ይበልጥ ለማሳደግ በሚዘጋጁበት ጊዜ ጊዜያዊው መንግሥት ጸረ-ሕዝብ ተግባሩን ማፋፋም ቀጥለ ። የጊዜያዊው መንግሥት የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ሚሊይኰቭ ሚያዝያ 18 ቀን «መላው ሕዝብ ወሳኝ የሆነውን ድል እስከተቀዳጀ ድረስ የአለም ጦርነቱን ወደፊት እንዲቀጥል ይፈልጋልና ለህብረቱ የተገቡ ግዴታዎች እንዲከበሩ ጊዜያዊው መንግሥት ይፈልጋል » ሲል ለህብረቱ ገለጸ ።

ስለሆነም ጊዜያዊው መንግሥት ዛሩ ላደረገው የጦር ስምምነት ፍፁምታማኝ መሆኑን በማረጋገጥ «በድል አድራጊነት ለማጠናቀቅ» ኢምፔሪያሊስቶች የሚፈልጉትን ያህል የህዝብ ደም ለማፍሰስ ቃል ገባ ።

ይህ መግለጫ ( « የሚሊይኰቭ ማሳሰቢያ » ) ሚያዝያ 19 ቀን ለሠራተኞችና ለወታደሮች ተሰማ ። ይህንን የጊዜያዊ መንግሥት ኢምፔሪያሊስት መርሆ ለመቃወም የቦልሼቪክ ፓርቲ ማእከላዊ ኰሚቴ ሚያዝያ 20 ቀን ለሰፊው ሕዝብ ጥሪ አደረገ ። በ « ሚሊይኩቭ ማሳሰቢያ » ግዴታ በማጉረምረም ሚያዚያ 20—21 ቀን (ግንቦት 3—4) 1917 ዓ. ም ከ100,000 የማያንሱ ሰራተኞችና ወታደሮች ሰላማዊ ሰልፍ አደረጉ ። ሠራተኞቹና ወታደሮቹ ከከተማዋ ዳርቻ አንስቶ የጊዜያዊው መንግሥት እስከሚገኝበት መሀከል ከተማ ድረስ « ምስጢራዊ ስምምነቱ ይገለጽ !» «ጦርነት ይውደም !» «ሥልጣን ለሶቪየቶች !» የሚሉ መፈክሮች የተጻፉባቸውን ሰንደቅ እንግበው በከፍተኛ ስሜት እያስተጋቡ ተጓዙ ። በኔቭስኪ ፕሮስፔርትና በሌሎችም ሥፍራዎች ላይ ከቡርዧው ቡድኖች ጋር ግጭት ተደርጎ ነበር ።

እንደ ጄኔራል ካርኔሎቭ የመሳሰሉ የወጣላቸው ጸረ-ሕዝቦች በሰላማዊ ሠልፈኞቹ ላይ የጥይት ናዳ እንዲወርድ ያልጠየቁበት ጊዜ አልነበረም ፤ እንዲያውም እንዲተኰስባቸው ትእዛዝ ሰጥተዋል ። ይሁን እንጂ ወታደሮቹ ይህንን ትእዛዝ በተግባር ለመፈጸም አልፈቀዱም ።

ሰላማዊ ሠልፍ በተደረገበት ወቅት ጥቂት የፔትሮግራድ የፓርቲ ኰሚቴ አባሎች (ባግዳተዮቭና ሌሎችም) ጊዜያዊ መንግሥት በአስቸኳይ እንዲወርድ የሚጠይቁ መፈክሮችን አነሱ ። ይሁንና የቦልሼቪክ ፓርቲ ማእከላዊ ኰሚቴ ይህንን « የግራ » አድርባይነት ባሕሪይ አወገዘ ። ፓርቲው በሶቪየቶች የበላይነትን ለማትረፍ (አብዛኛውን ክፍል ለመያዝ) የሚያደርገውን ጥረት የሚያደናቅፍና ሰላማዊ የአብዮት እድገት የሚለውን የፓርቲ መስመር ይቃረናል ። በመሆኑም ይህ መፈክር ወቅታዊና ትክክል አይደለም ሲል አወገዘው ።

የሚያዚያ 20—21 ቀን ድርጊቶች የጊዜያዊው መንግሥት ቀውስ መጀመሩን አሳይተዋል ።

በሜንሼቪኮችና በሶሻሊስት አብዮተኞች ታራቂ መርሆ ቀውስ የመጀመሪያው ጠንካራ ልዩነት ነበር ማለት ይቻላል ።

በሰፊው ሕዝብ ከፍተኛ ግፊት ግንቦት 2 ቀን 1917 ዓ. ም. ሚሊይኰቭና ጉችኮቭ ከጊዜያዊ መንግሥት ውስጥ ተወገዱ ።

የመጀመሪያውም ጭምር ጊዜያዊ መንግሥት ተመሠረተ ። ይህም መንግሥት ከቡርዧው ተወካዮች በተጨማሪ ሜንሼቪኮችን (ሶኰቢሌቭና ዜርቲሊ) እና ሶቭየት አብዮታውያንን (ቼርኖቭ ከረንስኪንና ሌሎችን) ጠቅሎ የያዘ ነበር ።

ስለሆነም በ1905 ዓ. ም. ለሶሻል—ዲሞክራቲክ ፓርቲ ተወካዮች በአብዮታዊ ጊዜያዊ መንግሥት ውስጥ መሳተፍ አይፈቀድም ይሉ የነ በሩት ሜንሼቪኮች አሁን የራሳቸው ተወካዮች በጸረ-አብዮተኛው ጊዜያዊ መንግሥት ውስጥ መሳተፍ የሚፈቀድ ሆኖ አገኙት ።

ስለሆነም ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች ወደ ቡርዧው ጸ አብዮተኞች ከድተው ገቡ ።

ሰባተኛው (ሚያዝያ) የቦልሼቪክ ፓርቲ ጉባኤ ሚያዝያ 24 ቀን 1917 ዓ. ም. ተሰበሰበ ። ፓርቲው የራሱን ሀልውና ካሳወቀበት ጊዜ ወዲህ ለመጀመሪያ ጊዜ ቦልሼቪክ ግልጽ የሆነ ጉባኤ አደረገ ። በፓርቲው ታሪክ ውስጥ የዚህ ጉባኤ ዓይነተኛነት ከፓርቲው ኰንግረስ ጋር የሚስተካከል ነበር ።

የሚያዝያው የመላው ሩሲያውያን ጉባኤ ፓርቲው በእመርታ እያደገ መሆኑን አሳይቶአል ። ጉባኤው 133 ድምጽ ባላቸው ተወካዮችና 18 ሀሳብ ማቅረብ የሚችሉ ግን ድምጽ በሌላቸው ተወካዮች ተካሄደ ። እነዚህ ተወካዮች የፓርቲውን 80 ሺህ ድርጅቶች ይወክላሉ ።

ጉባኤው ጦርነቱንና አብዮቱን አስመልክቶ በተነሱት መሠረታዊ ጥያቄዎች ላይ ተወያይቶበት የፓርቲውን መስመር ነደፈ። ማለትም በተጨባጭ ሁኔታ፣ በጦርነቱ በጊዜያዊ መንግሥት፣ በሶቪየቶች፣ በገጠር ጥያቄ፤ በብሔር ጥያቄ ወዘተ... ላይ ተወያይቶበት የፓርቲውን መሥመር ነደፈ።

በዘገባው ላይ ሌኒን ቀደም ብሎ በሚያዚያው በኩረ ሀሳቡ ላይ የሰነዘራቸውን መመሪያዎች በማጉላት የፓርቲው ተግባር ከመጀመሪያው የአብዮት ደረጃ « ማለትም . . . ስልጣኑን በቡርዧዎች እጅ ካስገባው — ስልጣንን በወዝአደሩና በደሀ ገበሬው እጅ የሚያስጨብጠው ወደ ሁለተኛው ደረጃ የሚደረገው ሽግግር ግቡን እንዲመታ ማድረግ ነው ። » (ሌኒን) ለሶሻሊስት አብዮት ፓርቲው ሊከተለው የሚገባው አቅጣጫ ተዘጋጀ ። የፓርቲው ወቅታዊ ተግባር « ስልጣን ለሶቭየቶች ! » በሚለው የሌኒን መፈክር ተገልፆ ነበር ።

«ስልጣን ለሶቪየቶች!» የሚለው መፈክር የሁለት ወገን ሥልጣን አስፈላጊነት ያብቃ ፤ በጊዜያዊ መንግሥትና በሶቪየቶች መሀከል የሥልጣን መከፋፈል ያክትም ፤ መላው ሥልጣን ለሶቪየቶች ይሰጥ፣ እንዲሁም የመሬት ከበርቴዎችና የካፒታሊስቶች ተወካዮች ከመንግሥቱ አካላት ይባረሩ ማለት ነበር ።

የሶሻሊስት አብዮተኞችና የሜንሼቪኮች ታራቂ መርሀ በሽንገላ ቃል ኪዳን ሕዝቡን ያታለለና በኢምፔሪያሊዝም ጦርነት ሊማግዳቸው የገፋፋውን ጸረ-አብዮት የቱን ያህል አደገኛ እንደነበረ በሚገባ ለሕዝቡ ለማሳየት እንዲቻል ጉባኤው እጅግ ጠቃሚ ከሆኑት የፓርቲ ተግባሮች ውስጥ አንድ «የጊዜያዊ መንግስት ባሕርይ የመሬት ከበርቴዎችና የቡርዧዎች አገዛዝ አካል መሆኑን» እውነተኛነት ለሰፊው ሕዝብ ያለመሰልቸት መግለጽ መሆኑን ወሰና ነበር ።

በጉባኤው ላይ ካሜኔቭና ራይኮቭ ሌኒንን ተቃወሙ ። የሜንሼቪኮችን በማስተጋባት በሩስያ ውስጥ ገና ለሶሻሊስት አብዮት አመቺ ሁኔታ አልተፈጠረምና በሩስያ ውስጥ ሊሆን የሚችለው የቡርዧው ሪፑብሊክ ብቻ ነው ሲሉ ተናገሩ ። ፓርቲውና ሠራተኛው መደብ ጊዜያዊውን



መንግስት «በመቆጣጠር» ራሳቸውን መወሰን አለባቸው ሲሉ አሳሰቡ ። እንደ እውነቱ ከሆነ ልክ እንደ ሜንሼቪኮች ካፒታሊዝምና የቡርዧውን ሥልጣን ለማቆየት የቆሙ ነበሩ ።

ዚኖቭየቭ እንዲሁ በጉባኤው ላይ ሌኒንን ተቃወመ ። ተቃውሞውም የቦልሼቪክ ፓርቲ በዚሜር ዋልዱ ሕብረት ውስጥ እንዳለው መቆየት ይኖርበታል ወይስ ከዚያ በመውጣት አዲስ አለም አቀፍ ይመሰርታል በሚለው ጥያቄ ላይ የተመሠረተ ነበር ። የጦርነቱ ወቅቶች እንዳሳዩን ይህ ሕብረት ለሰላም ፕሮፓጋንዳ በሚያካሂድበት ጊዜ በርግጥ የጦርነቱ ደጋፊዎች ከሆኑት ቡርዧዎች ጋር ያለውን ግንኙነት አያቋርጥም ። ስለሆነም ሌኒን በአስቸኳይ ከዚህ ሀብረት መውጣትና ሌላ አዲስ ኰሚኒስት ኢንተርናሽናል እንዲመሰረት አበክሮ አሳሰበ ። ዚኖቪየቭ ፓርቲው በዘመርዋልድ ሕብረት ውስጥ መቆየት አለበት ሲል ተቃወመ ። ሌኒን ይህን የዚኖቪየቭን ሀሳብ በጽኑ አውግዞ እነዚህን ታክቲኰቹን «ቁንጮ አድርባይና ጠንቀኛ » ሲል ጠራቸው ።

የሚያዝያው ጉባኤ በገጠርና በብሔር ጥያቄዎች ላይም እንዲሁ ተወያይቶበት ነበር ።

ሌኒን ስለገጠሩ ጥያቄ ካቀረበው ዘገባ ጋር ተያይዞ መሬት እንዲወረስና በገበሬዎች ኰሚቴ ሥር እንዲደላደል ጉባኤው ውሳኔውን አሳለፈ ። ቦልሼቪኮች ገበሬዎች ለመሬት እንዲታገሉ ጥሪ አደረጉ ። ቦልሼቪክ ፓርቲ አንድ ብቸኛ አብዮታዊ ፓርቲ መሆኑን ገበሬዎች ፣ የመሬት ከበርቴዎችን ለመፈንገል በሚያደርጉት ትግል በርግጥም የሚረዳቸው አንድ ብቸኛ ፓርቲ ቦልሼቪክ ብቻ መሆኑን በማሳየት አስመሰከሩ ።

ሌላው ትልቁ ነገር ጓድ ስታሊን ስለብሔሮች ጥያቄ ያቀረበው ዘገባ ነበር ። እንዲያውም ገና ከአብዮቱ በፊት በኢምፔሪያሊስቱ ጦርነት ዋዜማ ሌኒንና ስታሊን በብሔሮች ጥያቄ ላይ የቦልሼቪክ ፓርቲ መርሀ መሰረታዊ መመሪያዎችን ገልጸዋል ። ሌኒንና ስታሊን የወዝአደሩ ፓርቲ ጭቁን ሕዝቦች የሚያካሂዱትን ጸረ-ኢምፔሪያሊስት የሆነ ብሔራዊ የአርነት እንቅስቃሴ ትግል መደገፍ አለበት ሲሉ አሳወቁ ። በማስከተልም ቦልሼቪክ ፓርቲ ብሔሮች እስከ መገንጠልና የራሳቸውን መንግስት እስከመመስረት ድረስ እንኳ ቢሆን የራሳቸውን እድል በራሳቸው የመወሰን መብት እንዳላቸው አጥብቀው ደገፉ ።

ሌኒንና ስታሊን በጦርነቱ ወቅት ከቡካሪን ጋር በመሆን በብሔር ጥያቄ ላይ የብሔር ትምክህተኝነት አቋም ከወሰደው ከፓያታኮቭ ተቃውሞ ገጠማቸው ። ፓያታኮቭና ቡካሬን ብሔሮች የራሳቸውን እድል በራሳቸው የመወሰንን መብት ይቃወሙ ነበር ።

ፓርቲው በብሔር ጥያቄ ያለው ጠንካራና ጽኑ አቋም ለብሔሮች ፍጹም እኩልነትና ማናቸውንም ዓይነት ብሔራዊ ጭቆናና ብሔራዊ

መበላለጦችን ለማስወገድ በሚያደርገው ትግል ለፓርቲው ከፍተኛ ተደማጭነትና የጭቁን ብሔሮችን ድጋፍ አስገኘለት ።

በሚያዝያው ጉባኤ ላይ ጸድቆ የወጣው ውሳኔ ቃል እንደሚከተለው ነው ። «የራሳቸውን መደባዊ ክብር ለመጠበቅና ከተለያዩ ብሔረሰብ በመጡ ሰራተኞች መሀከል አንድነት እንዳይፈጠር ለማድረግ እንዲያስችላቸው ከፈላጭ ቆራጩና ከዘውዳዊው አገዛዝ የተወረሰውን የብሔሮች ጭቆና መርሆ የመሬት ከበርቴዎች ፤ ካፒታሊስቶችና ንዑስ ከበርቴዎች አጥብቀው ይደግፉታል ። ደካማ ብሔሮችን ለማስገበር ጥረታቸውን ያሳደጉ ዘመናዊ ኢምፔሪያሊስቶች ዘመናዊ ጭቆናን የሚያጠናክር አዲስ ምክንያት ነው ።

ለሁሉም ብሔሮችና ቋንቋዎች ፍጹም እኩልነት ዋስትና በሚሰጡ በጸና ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሥርዓትና መንግስታዊ አስተዳደር ሥር መላው ካፒታሊስት ሕብረተሰብ ውስጥ ብቻ የቤሔሮች ጭቆና መወገድ እስከሚችልበት ድረስ ሊወገድ ይችላል ።

«የሩስያ አካል የሆኑ ብሔሮች ሁሉ ለመገንጠልና የራሳቸውን ነጻ መንግስት እስከመመስረት ያላቸው መብት መታወቅ አለበት ። ይህን መብት መንፈግ ወይም በተግባር እንዲተረጐም ዋስትና የሚሰጥ እርምጃ አለመውሰድ በሀይል የመያዝንና የመቀላቀልን መርህ ከመደገፍ ጋር የሚመጣጠን ነው ። ወዝአደሩ የብሔሮችን የመገንጠል መብት ሲያውቅ ብቻ ነው ፤ በተለያዩ ብሔሮች በሚገኙ ወዝአደሮች መሀከል ፍጹም የሆነ አንድነት ሊረጋገጥና ብሔሮችን በሐቀኛ ዲሞክራሲያዊ መስመሮች እንዲቀራረቡ ሊረዳ የሚችለው ።

የብሔሮች የመገንጠል መብት አንድ ብሔር በማንኛውም ጊዜ በፈለገው ሁኔታ ለመገንጠል ካለው ችሎታና ኃይል ጋር መምታታት የለበትም ። የወዝአደሩ ፓርቲ ይህንን ሁኔታ በተገቢው መንገድ ማጤን ይገባዋል ። ይህንንም ሁኔታ የሚያጤነው ከማኅበራዊ እድገትና ወዝአደሩ ለሶሻሊዝም ከሚያደርገው የመደብ ትግል አንጻር ነው ።

ፓርቲው ሪጂናል አውቶኖሚ እንዲሰፋ ፤ የበላይ ተቆጣጣሪነት እንዲወገድ መንግስታዊ የቋንቋ ግዴታ እንዲቀርና የራስ በራስ አስተዳደርርና የአውቶነመስ አካባቢዎች ድንበር እንደ ምጣኔ-ሀብታዊና ማኅበራዊ ሁኔታዎችን እንዲወሰኑ ፣ ብሔራዊ ሕዝባዊ ውህደትና ሌሎችንም ጠየቀ ።

«የወዝአደሩ ፓርቲ ትምህርትና የመሳሰሉትን ነገሮች ከመንግስት ቁጥጥር ስር አስወጥቶ በብሔረሰቦች አካባቢ በሚቋቋመው ምክር ቤት እጅ የሚጥለውን ፤ ባህላዊ ቤሔራዊ አውቶኖሚ የሚለውን ሀሳብ በቆራጥነት ይቃወማል ። ባህላዊ ብሔራዊ አውቶኖሚ በአንድ አካባቢ በሚኖሩ ሰራተኞችንና እንዲያውም በአንድ ኢንዱስትሪያዊ ተቋም ውስጥ አብረው የሚሰሩ ሠራተኞችን እንደየተለያየው ብሔራዊ



ባህላቸው ሰው ሰራሽ በሆነ መንገድ ይከፋፍላል ። በሌላ ቃላት ለመናገር የሶሻል ዲሞክራቶች አላማ የአለም ወዝአደሮችን ዓለም አቀፋዊ ባሕል ለማሳደግ ሲሆን ባህላዊ ብሔራዊ አውቶኖሚ ግን በአንድ ብሔር ውስጥ በሰራተኛውና በቡርዧው ባህል መሀከል ያለውን ግንኙነት ይበልጥ ያጠናክራል ።

ፓርቲው ምንም ይሁን ለማናቸውም ብሔሮች የተሰጡ ልዩ መብቶችና የሕዳጣን ብሔሮቹን መብት የሚጥሱትን ማናቸውንም ሕጎች ከህገ መንግስቱ ተሠርዞ መሰረታዊ የሆኑ ሕጎች በቦታው ላይ እንዲሰፍሩ ጥያቄ አቀረበ ።

«የሰራተኛው መደብ ፍላጐት ከመላው ሩስያ ብሔረሰቦች ለመጡ ሰራተኞች አንድ የጋራ የሆኑ የወዝአደሩ ድርጅቶች እንዲኖሩ ነው ። እነዚህም ፣ ፖለቲካዊ ፣ የሙያ ማኅበር ፣ የሕብረት ድርጅቶች ትምህርታዊ ተቋሞችና የመሳሰሉት ናቸው ። የተለያዩ ብሔረሰቦች ሠራተኞች የጋራ በሆነው እንዲህ ባለው ድርጅት ብቻ ነው ወዝአደሩ ከአለም-አቀፋዊ ወረትና የቡርዧው ብሔረተኝነት ጋር የሚያደርገው መራራ ትግሉ በድል አድራጊነት ሊሰምር የሚችለው ። »

ስለሆነም የሚያዝያው ጉባኤ አድርባዮችን የካሜኔቭን ፣ የዚኖቭየቭን ፣ የፓያታኮቭን ፣ የቡካሪንን ፣ የራይኮቭንና የጥቂት ተከታዮቻቸውን ጸረ-ሌኒናዊ አቋም አጋለጠ ።

ጉባኤው በሁሉም ጠቃሚ ጥያቄዎች ላይ ትክክለኛ አቋም በመውሰድና ለሶሻሊስት አብዮት ድል የሚያበቃውን ፈለግ በመቀበል በአንድ ድምጽ ሌኒንን ደገፈ ።

### 3. የቦልሼቪክ ፓርቲ በዋናው ከተማ ውስጥ ድል መቀዳጀቱ ፤ የጊዜያዊ መንግስት ጦር ሠራዊቶች ፍሬ ቢስ ማጥቃት ፤ የሐምሌው የሰራተኞችና የወታደሮች ሰላማዊ ሰልፍ መታፈን ፡-

የሚያዝያው ጉባኤ ባሳለፈው ውሳኔ መሰረት ፓርቲው የሰፊውን ሕዝብ ድጋፍ ለማትረፍና ሰፊውን ሕዝብ ለፍልሚያው ለማሰልጠንና ለማዘጋጀት ሰፊ ንቅናቄዎችን አሳደጉ ። በወቅቱ ፓርቲ ያራምደው የነበረው መስመር ትእግሥት በተሞላበት መንገድ የቦልሼቪኮችን መርሆ መግለጽና የሜንሼቪኮችንና የሶሻሊስት አብዮተኞችን ታራቂ መርሆ በማጋለጥ እነዚህን ፓርቲዎች ከሰፊው ሕዝብ መነጠልና የአብዛኛውን ሶቪየቶች ድጋፍ ማትረፍ ነበር ።

በተጨማሪም በሶቪየቶች ውስጥ የሚሠሩትን ተግባራት አስመልክቶ ቦልሼቪኮች በሙያ ማኅበራትና በፋብሪካ ኩሚቴዎች ውስጥ ጠንካራ እንቅስቃሴ አከናውነዋል ።

በተለይ ደግሞ ቦልሼቪኮች እጅግ ጠንካራ ሥራ ያከናወኑት በጦር ሠራዊቱ ውስጥ ነበር ። በየአካባቢው ወታደራዊ ድርጅቶች አበቡ ። ቦልሼቪኮች ወታደሮችንና መርከበኞችን ለማደራጀት ከግንባርና ከኋላ በመሆን ያለእንዳች መታከት ከፍተኛ ተግባር አከናወኑ ። ወታደሮችን ንቁ አብዮታውያን ለማድረግና በግንባር ልዩ አይነተኛ ሚና የተጫወተው የቦልሼቪኮች ጋዜጣ አኩፕና ያ ፕራቭዳ (የምሽጉ እውነታ) ነበር ።

ለቦልሼቪኮች ፕሮፖጋንዳና ቅስቀሳ ምስጋና ይግባውና ቀደም ባሉት የአብዮት ወራት በአያሌ ከተሞች ውስጥ ሠራተኞች የሶቪየት በተለይ የአውራጃ ሶቭየቶች አዲስ ምርጫ በማካሄድ ሜንሼቪኮችንና ሶሻሊስት አብዮተኞችን በማስወገድ በፈንታቸው የቦልሼቪክ ፓርቲ ደጋፊዎችን በመተካት ምርጫ አካሄዱ ።

ቦልሼቪኮች ያካሄዱት ተግባር ፣ በተለይም በፔትሮግራድ እጹብ ድንቅ የሆነ ውጤት አፈራ ። ከግንቦት 30 እስከ ሰኔ 3 ቀን 1917 ዓ.ም. ድረስ የፔትሮግራድ የፋብሪካ ኩሚቴዎች ጉባኤ ተካሄደ ። በዚህ ጉባኤ ላይ ከተወካዮቹ ውስጥ ሶስት አራተኛ የሚሆኑት መላው የፔትሮ ግራድ ወዝአደሮች ማለት ይቻላል—«ሥልጣን ለሶቪየቶች !» የሚለውን የቦልሼቪኩችን መፈክር በመደገፍ ከቦልሼቪኩች ጎን ቆሙ ።

በሰኔ 3(16) ቀን 1917 ዓ. ም. የመላው ሩስያ ሶቭየቶች የመጀመሪያው ኩንግሬስ ተሰበሰበ ። አሁንም ቢሆን በሶቪየቶች ውስጥ ቦልሼቪኮች ጥቂቶች ነበሩ ። 700 ወይም 800 ከሚሆኑ ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች ጋር ሲነጻጸር ቦልሼቪኮች በዚህ ኩንግረስ ውስጥ የነበሯቸው ተወካዮች ግፋ ቢል ከመቶ ጥቂት ቢበልጡ ነበር ።

በመጀመሪያው የሶቪየቶች ኩንግረስ ፣ ቦልሼቪኮች ፣ ከቡርዧው ጋር መታረቅ የሚያስከትለውን አደጋ አበክረው በማሳሰብና የጦርነቱን ኢምፔሪያሊስት ባህርይ አጋለጡ ። ሌኒን በኩንግረሱ ላይ ቦልሼቪኮች የተከተሉት መስመር ትክክለኛነቱንና ለሰራተኛው መደብ ዳቦ ፣ መሬት ለአራሾች መስጠት ፣ ጽኑ ሰላም መስፈንና አገሪቷ ከገባችበት የቀውስ ማጥ ውስጥ ማውጣት የሚችለው የሶቪየቶች መንግሥት ብቻ እንደሆነ በመግለጽ ንግግር አደረገ ።

በዚያን ወቅት በፔትሮግራድ የሠራተኛው መደብ አውራጃዎች ውስጥ ሰላማዊ ሠልፍ ለማደራጀትና ለሶቭየቶች ኩንግረስ ጥያቄ እንዲቀርብ ሰፊ ዘመቻ እየተካሄደ ነበር ። የፔትሮግራድ ሶቭየት ባለስልጣን ኮሚቴ ከሥልጣኑ ውጪ በሆነ መንገድ ሠራተኞች ሠላማዊ ሰልፍ እንዳያደርጉ ለማድረግ ብለው ጉጉትና የሰፊውን ሕዝብ አብዮታዊ ስሜት ለራሱ ተግባር ለመጠቀም ባለው ምኞት የተነሳ ለሰኔ 18 ቀን (ነሐሴ 1) ሰላማዊ ሰልፍ ለመጥራት ወሰነ ። ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች ሠላማዊ ሰልፍ በጸረ-ቦልሼቪኮች መፈክር ሥር ይካሄዳል ብለው በተስፋ ጠብ



ቀው ነበር ። ይሁንና የቦልሼቪክ ፓርቲ ለዚህ ሊያደርግ ለታሰበው ሰላማዊ ሰልፍ ጠንካራ ዝግጅት ማከናወን ጀመሩ ። ጓድ ስታሊን በፕራቭዳ ጋዜጣ እንደጻፈው « የሰኔ 18 ቀን ሠላማዊ ሠልፍ በእኛ አብዮታዊ መፈክሮች ሥር መሆኑን ማረጋገጡ የኛ ተግባር ነው ። »

የሰኔ 18 ቀን 1917 ዓ. ም. ሰላማዊ ሰልፍ የተደረገው በአብዮታዊ ጀግኖች መካነ መቃብር ላይ ነበር ። በዚህም ቦታ የመከናወኑ የቦልሼቪክ ፓርቲን ኃያልነት አረጋገጠ ። የሰፊውን ሕዝብ አብዮታዊ መንፈስና በቦልሼቪክ ፓርቲ ላይ ሕዝቡ ያለው እምነት እያደገ መሄዱን በገሀድ ከሰልፉ ማየት ተቻለ ። በጊዜያዊ መንግሥት ላይ እምነት እንዲኖር የሚጠይቀውና ጦርነቱ እንዲቀጥል የሚገፋፋው ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት-አብዮተኞች ያነገቡት መፈክር በቦልሼቪኮች መፈክር ተውጠው ቀሩ ። አራት መቶ ሺህ ሰላማዊ ሰልፈኞች « ጦርነቱ ይውደም ! » « አስሩ ካፒታሊስት ሚኒስትሮች ይውደሙ ! » « ስልጣን ለሶቪየቶች ! » የሚሉ መፈክሮችን ያዘሉ ሰንደቆች አንግበው ሰላማዊ ሰልፍ አደረጉ ።

ይህ ደግሞ ለሜንሼቪኮችና ለሶሻሊስት አብዮተኞች የለየለት ውድቀት ሲሆን ፤ በዋናይቱ ከተማም ለጊዜያዊው መንግሥት ከባድ ውድቀት ነበር ።

የሆነው ሆኖ ጊዜያዊው መንግሥት የመጀመሪያውን የሶቪየቶች ኮንግረስ ድጋፍ አገኘና ኢምፔሪያሊስት ፖሊሲን ለማራመድ ወሰነ ። በዚያን ሰኔ 18 ቀን ጊዜያዊው መንግስት ለእንግሊዝና ለፈረንሳይ ኢምፔሪያስቶች ታዛዥ በመሆን የማጥቃት እርምጃ ለመውሰድ ወታደሮችን ወደ ግንባር አሰማራ ። ቡርዧዎች ይህ ዘዴ ለአብዮቱ ማክተሚያ የሚሰጥ እንደ መፍትሄ አድርገው ተመለከቱት ። ቡርዧዎች ጦርነቱን በአሸናፊነት የሚለውጡት እንደሆነ መላውን ሥልጣን በእጃቸው ለማስገባት ፤ ከመድረኩ ለማስወጣትና ቦልሼቪኮችን ለመደምሰስ ተመኝተው ነበር ። በሌላም በኩል ጦርነቱ ሽንፈት ቢገጥመው ደግሞ በወታደሩ መፈረካከስ ቦልሼቪኮችን በመከሰስ መላውን ወቀሳ በነርሱ ላይ ለማሾርጉድጉድ ነበር ።

የማጥቃቱ እርምጃ ደግሞ የማይከሽፍበት አንዳችም ምክንያት አልነበረም ። ደግሞም ወድቋል ። ወታደሮቹ የተዳከሙ ነበሩ ። የማጥቃቱ ዓላማ ምን እንደሆነ አልተረዱትም ነበር ። ባእድ በሆኑት መኩንኖቻቸው (አዛዦቻቸው) ላይ አንዳችም እምነት አልነበራቸውም ፤ የመድፈኞችና የመድፍ ጥይቶች እጥረት ነበረባቸው ። እነዚህ ሁሉ የማጥቃቱን መክሸፍ ይህን ወደ መሰለ መደምደሚያ አደረሱት ።

የግንባሩ የማጥቃት ዜናዎችና ብሎም መጨናገፉ ፣ በዋናው ከተማ ስሜት ቀሰቀሰ ። የሠራተኞችና የወታደሮች ንዴት ከመጠን ያለፈ ሆነ ። ጊዜያዊው መንግሥት የሰላም ፓሊሲ በአወጀበት ጊዜ ሕዝቡን

ማታለሉ እንደነበር ግልጽ እየሆነ መጣ ። የመላው ሶቪየቶች ባለሥልጣን
ኩሚቴና የፔትሮግራድ ሶቪየት የጊዜያዊውን መንግሥት ወንጀለኛ ድር
ጊት ለመግለጽ ፍቃደኛ አለመሆናቸው ወይም ለመቆጣጠር አለመቻላቸ
ውና ራሳቸው እርሱኑ መከተላቸው በገሀድ ግልጽ እየሆነ መጣ ።

የፔትሮግራድ ሰራተኞችና ወታደሮች ንዴት ያለቅጥ ገንፍሎ በሐ
ምሌ 3 ቀን (16) የፔትሮግራድ እውራጃ በሆነው በቪይበርግ ውስጥ ግብ
ታዊ የሆነ ሰላማዊ ሠልፍ ተደረገ ። ሰልፉ መላውን ቀን ሲካሄድ ዋለ ።
የተነጣጠለው ሰላማዊ ሠልፍ ወደ ትልቅ አጠቃላይና በትጥቅ የተደገፈ
ሰላማዊ ሠልፍ በማደግ ስልጣን ለሶቪየቶች እንዲሰጥ ጠየቀ ። በዚያን
ወቅት አብዮታዊ ሁኔታዎች ገና አልዳበሩም፣ ማለትም ወታደሮችና ክፍ
ላተ ሀገሮች በዋና ከተማይቷ ውስጥ የተነሳውን አመጽ ለመደገፍ ገና አልተ
ዘጋጁም ። የተነጣጠሉና ያልበሰሉ ( በቅድሚያ ዝግጅት ያላደረጉ)
አመጾች የአብዮቱን ግንባር ቀደም ሀይል ነጥሎ ለመምታት እንዲ
ችሉ ለጸረ አብዮተኞች ሁኔታውን እጅግ ቀላል ያደርግላቸዋል ። ስለሆ
ነም ቦልሼቪክ ፓርቲ ትጥቃዊ እርምጃዎችን ተቃወመ ። ይሁን እንጂ
ሰፊውን ሕዝብ በአመጹው ፍጹም መግታት የማይቻል መሆኑ በግልጽ
ሲታይ በትክክለኛው መንገድ ለመምራትና የድርጅት ባህርይ ለመስ
ጠት ፓርቲው በሰላማዊ ሠልፍ ለመሳተፍ ቆረጠ ። ይህን በማድረግ
ቦልሼቪክ ድል አገኘ ። ስልጣን በሶቪየቶች እንዲያዝ፣ ከኢምፔሪያሊስት
ቡርዧዎች ጋር ግንኙነቱ እንዲቋረጥ ፣ እውነተኛ የሰላም ፖሊሲ እንዲ
ራመድ በመጠየቅ በመቶ ሺህ የሚቆጠሩ ወንዶችና ሴቶች ወደ ፔትሮግ
ራድ ሶቪየቶች ጠቅላይ መምሪያና ወደ መላው የሩስያ ሶቪየቶች ማእከ
ላዊ ባለስልጣን ኮሚቴ በታላቅ ሰልፍ ሄዱ ።

ሰልፉ ሰላማዊ ጸባያት ቢኖረው እንኳ አድሀሪ ቡድኖች — የመኰ
ንኖችና ካዴቶች ክፍል—ሊቃወሙት ወጥተው ነበርና የፔትሮግራድ አ
ውራ መንገዶች በሠራተኞችና በወታደሮች ደም ተጥለቀለቀ ። እጅግ ደን
ቆሮዎችና ጸረ አብዮተኞች የሆኑት የሠራዊቱ ክፍል ሠራተኞችን እንዲ
ጨፈጭፉ ከግንባር ተጠርተው መጡ ።

የሠራተኞችንና የወታደሮችን ሰላማዊ ሰልፍ ከበተኑ በኋላ ሜንሼ
ቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች ከቡርዧውና ከነጭ ዘብ ጀኔራሎች ጋር
በማበር በቦልሼቪክ ፓርቲ ላይ ተረባረቡ ። ፕራቭዳ የሚታተምበት ግቢ
ተነኳኩተ ። ፕራቭዳ ፣ ሰልዳትስካያ ፕራቭዳ (የወታደሮች እውነት)ና
ሌሎችም እያሌ የቦልሼቪክ ጋዜጦች ታፈኑ ። ቮይኖቭ የተባለው
ሰራተኛ| ሊስቶክ ፕራቭዲያን (የፕራቭዳ መግለጫ) በመሸጡ ካዴቶች
በመንገድ ላይ ገደሉት ። ቀይ ዘቦችን ትጥቅ ማስፈታት ተጀመረ ።
የፔትሮግራድ አብዮታዊ ቡድኖች ጦር ሠፈር ከዋና ከተማው በመልቀቅ
ወደ ምሽግ በአፋጣኝ ተላከ ። በግንባርና በጀርባ እስር ማካሄድ ተጧጧፈ ።
ስመጥሩ የቦልሼቪክ ፓርቲ አባሎች ታሠሩ ። እነዚሁ ፀረ-አብዮተኞች



የቦልሼቪክ እትሞች የሚታተሙበትን የትሩድ የማተሚያ ድርጅት
እንኩታኩቱ ። የፔትሮግራድ ፍርድ ቤት ችሎት ሌኒንና እያሌ ቦልሼቪ
ኮች በ«ከፍተኛ የሀገር መክዳት» በትጥቃዊ የአመጽ ድርጅት ምክንያት
ተከሰዋል ሲል በይፋ ተናገረ ። በሌኒን ላይ የተመሠረተው የፈጠራ ክሱ
በጀኔራል ዴንኪን ጠቅላይ መምሪያ ውስጥ ነበርና ክሱ የተመሠረተው
ሰርጐ ገብ ጠብ አጫሪዎችና ሰላዮች በሰጡት ምስክርነት ላይ ነበር ።

ስለሆነም ሴሬቲሊ ፣ ስኩብሌቭ ፣ ክረንስኪ ፣ ቼርኖቭና የመሳሰሉ
ትን ያቀፈው ጊዜያዊ የሁለት ወገን መንግሥት ወደ የለየለት ኢምፔሪያ
ሊስትነትና ጸረ-አብዮት ማጥ ውስጥ ጭልጥ ብሎ ተዘፈቀ ። የሰላም
ፖሊሲ ከማራመድ ፈንታ ጦርነቱ እንዲቀጥል ወሰነ ። የሕዝቡን ዲሞክ
ራሲያዊ መብቶች ከመጠበቅ ፈንታ እነዚህን መብቶች የመንፈግ ፖለሲ
በመከተሉ ሠራተኞችንና ወታደሮችን በወታደራዊ ሀይል አሰፈነ ።

የቡርዧው ተጠሪዎች የነበሩት ጉችኮቭና ሚላይኮቭ ለመፈጸም
ፈልገው የነበረውን « ሶሻሊስቶቹ » ክረንስኪና ሴሬቴሊ ፣ ቼርኖቭና
ስኰቢሌ አከናወኑት ።

የሁለት ወገን ሥልጣኑ ወደማብቃቱ ተቃረበ ።
ሶቪየቶች በሶሻሊስት አብዮታውያንና በሜንሼቪክ መሪዎቻቸው
ዓማካኝነት የጊዜያዊው መንግሥት ጭራ ሲሆኑ መላው ስልጣን በጊ
ዜያዊ መንግሥት እጅ በመጠቃለል ለቡርዧው በሚያመች ሁኔታ አበቃ ።

የትጥቁ ጉዳይ በአጀንዳው ላይ በመስፈሩ የአብዮቱ ሰላማዊ ወቅ
ቶች አከተሙ ።

የሁኔታውን መለወጥ በመመልከት ቦልሼቪክ ፓርቲ ታክቲኮችን
ለመለወጥ ወሰነ ። እንደገና ራሱን ወደህቡእ አስገባ ። መሪውን ሌኒንን ፣
ለመደበቅ አመቺ ቦታዎችን አዘጋጀና የቡርዧውን ሥልጣን በትጥቃዊ
ሀይል እንኳኩቶ ለመጣልና የሶቪየቶችን ስልጣን ለመመስረት ዓላማ አድ
ርጐ ዝግጅቱን ቀጠለ ።

## 4/ የቦልሼቪክ ፓርቲ ለትጥቃዊ አመጽ ዝግጅት እንዲደረግ ማጽደቁ፤ ስድስተኛው የፓርቲ ኰንግረስ ።

የቡርዧዎችና ንዑስ ከበርቴዎች ፕሬስ ልክ አሳን ለመያዝ በመን
ጠቆ ጫፍ የመሳቢያ ምግብ እንደሚደረግ ሁሉ ቦልሼቪኰችን ለመሳብ
በሀይለኛ ስሜት ዘመቻ ማካሄዱን በአጧጧፉበት አጋማሽ ላይ ነበር የቦል
ሼቪክ ፓርቲ ኰንግረስ በፔትሮግራድ የተካሄደው ። ይህ ኰንግረስ በሎ
ንደን ላይ ከተደረገው የቦልሼቪኰች ኰንግረስ ከአስር ዓመት በኋላ ፣ ከፕ
ራግ ጉባኤ ደግሞ ከአምስተኛ ዓመት በኋላ የተሰበሰበ ነበር ። በሚስጥር
የተደረገው ይህ ኰንግረስ ከሐምሌ 26 ቀን እስከ ነሐሴ 3 ቀን 1917 ዓ.ም.
ድረስ ተካሄደ ። የሚወጡት ጋዜጦች በሞላ የሚገልጹት ስብሰባው እን

ደሚደረግ ቢሆንም ቅሉ ፤ የስብሰባውን ስፍራ አይገልጹም ነበር ። የመጀመሪያው ስብሰባ በቫይበርግ አውራጃ ሲደረግ የኋለኛው ደግሞ በናርቫ—በር አጠገብ በሚገኘው አሁን የባህል-ቤት የተሰራበት ላይ በነበረው ትምህርት ቤት ውስጥ ነበር ። የቡርዧው ፕሬሶች የስብሰባው ተወካዮች ታድነው እንዲታሰሩ ጠየቁ ። የኰንግረሱን የስብሰባ ቦታ ለማግኘት በሰላዮቻቸው አማካይነት ከተማይቱን አሰሱ ፤ ነገር ግን ሁሉም ከንቱ ሆኖ ቀረ ።

ስለሆነም የዛሩ አገዛዝ ከተገረሰሰ ከአምስት ወራት በኋላ ቦልሼቪኰች በሚስጢር እንዲሰበሰቡ ሲገደዱ ፣ የወዝአደሩ መሪ የነበረውም ሌኒን በራጊሊቭ ጣቢያ አጠገብ በምትገኝ በአንዲት ጐጆ ውስጥ እንዲደበቅ ተገድዶ ነበር ።

ሌኒን በጊዜያዊ መንግስት ወንጀል መርማሪዎች ዘንድ እጅግ ጐልቶ የሚታይ በመሆኑ በኰንግረሱ ለመሳተፍ አልበቃም ። በርግጥም ሌኒንን ለማግኘት ያልፈነቀሉት ድንጋይ ያላሰማሩት ሰላይ አልነበረምና ከቦታው መሰወር ግድ ሆነበት ። ይሁን እንጂ ከተሸሸገበት ቦታ ሆኖ በነስታሊን ፤ ስቨርድሎቭ ፣ ሞሎቶቭ ፣ እርጆኒኪዥ በመሰሉ የቅርብ ጓደኞቹና ደቀመዛሙሮቹ አማካይነት ስራዎችን ይመራ ነበር ።

ኰንግረሱ 157 ድምጽ ባላቸው ተወካዮችና 128 ሀሳብ የሚሰጡ ግን ድምጽ በሌላቸው ተወካዮች ተካሄደ ። ሰኔ 3 ቀን በዚያን ወቅት ፓርቲው 240,000 ያህል የሚገመቱ አባላት ነበሩት ። ሰኔ 3 ቀን የሰራተኞች ሰላማዊ ሰልፍ ከመፈንዳቱ ቀደም ብሎ ገና ቦልሼቪኰች ህቡዕ ሳይገቡ ሕጋዊ ስራዎችን በሚሰሩበት ወቅት መሆኑ ነው ፣ ፓርቲው 41 የሚታተሙ ጽሁፎች ሲኖሩት ከነዚህም ውስጥ 29ኙ በሩሲያና 12ቱ ደግሞ በተለያዩ ቋንቋዎች የተጻፉ ነበሩ ።

በሐምሌ ቀኖች ውስጥ በቦልሼቪኰችና በሰርቶ አደሩ መደብ ላይ የደረሰው ስቃይ የፓርቲ ያችንን ተደማጭነት ከመቀነስ አርቆ እንዲያውም ተደማጭነቱን አሳደገው ። የጠቅላይ ተወካዮች አያሌ መረጃዎችን በመጥቀስ ሰራተኞችና ወታደሮች ሜንሼቪኰችንና ሶሻሊስት—አብዮተኞችን ንቀት በተሞላበት መንገድ «የሕብረተሰብ ነጻነት ገፋፊዎች» እያሉዋቸው በብዛት እየተውአቸው መውጣት መጀመራቸውን አሳዩ ። በሜንሼቪክና በሶሻሊስት አብዮታውያን ፓርቲ ዎች ውስጥ የሚገኙ ሰራተኞችና ወታደሮች አባል ካድሬዎቻቸውን በማናደድ በማስከፋታቸው ወደ ቦልሼቪክ ፓርቲ ለመግባት ጥያቄ አቀረቡ ።

በኰንግረሱ ላይ የተወያዩባቸው አበይት ጉዳዮች የማዕከላዊ ኰሚቴው ፖለቲካዊ ዘገባና ፖለቲካዊ ሁኔታ ነበሩ ። ጓድ ስታሊን ነበር በሁለቱም ጥያቄዎች ላይ ዘገባውን ያቀረበው ። አብዮቱን ለማፈን ቡርዧዎች ሁሉን ዓይነት ጥረት ቢያደርጉም እጅግ ግልጽ በሆነ መንገድ የአብዮቱን ሂደትና



እድገት አሳየ ። በምርትና በምርት ማከፋፈል ላይ የሰርቶ አደሩ ቁጥጥር መመስረት ፣ መሬትን ለገበሬዎች መመለስና ስልጣኑን ከቡርዧው ላይ ነጥቆ ለሰርቶ አደሩ መደብና ለደሀው ገበሬ ማሸጋገር ወቅታዊ የአብዮቱ ተግባር መሆኑን ጠቆመ ። አብዮቱ የሶሻሊስት አብዮት ባህሪን እየያዘ ነው ሲል ተናገረ ።

ከሐምሌ ቀኖች ወዲህ በሀገሪቷ ውስጥ ያለው ፖለቲካዊ ሁኔታ ስርነቀል በሆነ ሁኔታ ተለውጧል ። የሁለት ወገን ስልጣኑ አብቅቷል ። በሶሻሊስት—አብዮተኞችና በሜንሼቪኰች የሚመሩ ሶቭየቶች መላውን ስልጣን ለመውሰድ እንቢ በማለታቸው ስልጣኑን በሙሉ ለቀቁ ። አሁን ስልጣኑ በቡርዧው ጊዜያዊ መንግስት እጅ ተጠቃሎአልና በሚቀጥለው ተግባር ደግሞ የአብዮቱን ትጥቅ ማስፈታት ፣ ድርጅቶቹን ማድቀቅና ቦልሼቪክ ፓርቲን ማጥፋት ይሆናል ። ሁሉም የአብዮቱ ሰላማዊ ዕድገት አክትሟል ። የቀረ ነገር ቢኖር አንድ ነገር ብቻ ነው አለ ጓድ ስታሊን ሲናገር ፤ እሱም ጊዜያዊውን መንግስት በመገርሰስ ስልጣኑን በሀይል መንጠቅ ብቻ ነው ። ይህን ስልጣን በሀይል መንጠቅ የሚቻለው ደግሞ ወዝ አደሩ ፣ ከደሀው ገበሬ ጋር ሲተባበር ብቻ ነው ።

እስከ አሁን በሜንሼቪኰችና በሶሻሊስት—አብዮተኞች ቁጥጥር ስር ያሉ ሶቭየቶች በቡርዧው ካምፕ ውስጥ ተዘፍቀዋልና በአሁኑ ተጨባጭ ሁኔታ የጊዜያዊው መንግስት ደጋፊዎች ብቻ ከመሆን እንደማያልፉ የሚጠበቅ ይሆናል ። አሁን ከሐምሌ ቀኖች በኋላ ፣ ይላል ጓድ ስታሊን «ስልጣን ለሶቭየቶች» የሚለው መፈክር ማፈግፈግ ይገባዋል ። ይሁን እንጂ የዚህ መፈክር ጊዜያዊ ማፈግፈግ ማለት በማናቸውም ዓይነት መንገድ ለሶቭየቶች ስልጣን የሚደረገው ትግል መካድን አያመለክትም ። ይህ ጥያቄ የሚመለከተው የአብዮታዊ ትግል አካል የሆኑትን ሶቭየቶችን ሳይሆን አሁን በሜንሼቪኰችና በሶሻሊስት አብዮተኞች ቁጥጥር ስር ያሉትን ሰዎች ብቻ ነው ።

«የአብዮቱ ሰላማዊ ወቅት አብቅቷል ፣» ይላል ጓድ ስታሊን «ሰላም-አልባው ወቅት ፣ የግጭቶችና የፈንጂዎች ወቅት ፣ ተጀምሮአል ።»
(በሩ. ሶ. ዲ. ሰ. ፖ ስድስተኛ ጉባኤ የጽሑፍ ዘገባ ሩሲያ እትም ገጽ 111)

ፓርቲው ወደ ትጥቅ አመጽ አመራ ።

በኰንግረሱ ውስጥ ጥቂት የቡርዧውን ተጽእኖ ያንጸባረቁ አልታጡም ነበር ። ለሶሻሊስት አብዮት የጸደቀውን መስመር ተቃወሙት ።

ትሮትስካይቱ ፕሬአብራዜንስኪይ ስለ ስልጣን መያዝ በተላለፈው ውሳኔ ላይ ሀገሪቷ ወደ ሶሻሊዝም ልትመራ የምትችለው በምዕራቡ ዓለም የወዝአደሩ አብዮት ሲደረግ ብቻ እንደሆነ በመጥቀስ በውሳኔው ላይ መታከል አለበት የሚል ሀሳብ አቀረበ ።

ይህን የትሮትስካይት ሀሳብ ጓድ ስታሊን በመቃወም ሲናገር «የምር ጫው መንገድ ሩሲያ ወደ ሶሻሊዝም የሚወስደውን ጐዳና የምትከተል ሀገር ትሆናለች ከሚለው የሚለይ አይደለም ። . . . ይህን መንገድ የሚያሳየን አውሮፓ ብቻ ነው የሚለውን ጊዜው ያለፈበት አስተሳሰብ አውጥተን መጣል አለብን ። ቀኖናዊ ማርክሲዝምና ሳይንሳዊ ማርክሲዝም አሉ ። የኔ አቋም ግን የኋለኛው ነው» ። (ከዚህ በላይ በተገለጸው መጽሐፍ ገጽ 233-34)

ትሮትስካይት አቋም የነበረው ቡካሬን አርሶአደሮች ከቡርዧው ጋር ሕብረት ፈጥረዋልና የሰርቶ አደሩን መደብ ሊከተሉ አይችሉም ስለሆነም ጦርነቱን ይደግፋሉ ፤ በማለት ተናገረ ።

ጓድ ስታሊን ለቡካሬን ንግግር መልስ ሲሰጥ የተለያዩ ዓይነት አርሶ-አደሮች መኖራቸውን በማሳየት ፤ ኢምፔሪያሊስት ቡርዧውን የሚደግፉ ሀብታም አርሶ-አደሮች ፤ ከወዝ አደሩም ጋር ሕብረት ፈጥረው የታገሉ ደሀ ገበሬዎች እንደነበሩና እንዲሁም ለአብዮቱ ድል አድራጊነት ከወዝ አደሩ ጐን በመቆም የሚታገሉ እንዳሉ አስረድቷል ።

ኰንግረሱ የፕሬአከራዜንስኪይንና የቡካሬንን የማሻሻያ ሀሳብ ውድቅ አድርጐ ፣ የጓድ ስታሊንን ሀሳብ አጽድቆ ተቀበለ ።

ኰንግረሱ እንደዚሁም የቦልሼቪኰችን ምጣኔ ሀብታዊ መምሪያ ከተወያየበት በኋላ አጸደቀ ። የዚህም ዓበይት ነጥቦች ሰፋፊ ሁዳዶችን መውረስ ፣ መሬትን በመንግስት ቁጥጥር ስር ማድረግና የምርትና የምርት ማከፋፈሉን ተግባር በሰርቶ አደሩ ቁጥጥር ስር ማዋል ነበሩ ።

ኰንግረሱ በኋላ ታላላቅ ኢንዱስትሪያዊ ተቋሞች በመንግስት ቁጥጥር ስር በሚውሉበት ጊዜ ዓይነተኛ ሚና የሚጫወተውን ፤ በምርት ላይ የሰርቶ አደሮች ቁጥጥር ለመመስረት የሚደረገውን ትግል እጅግ አስፈላጊነት አበክሮ አስገነዘበ ።

ባሳለፋቸው ውሳኔዎች ሁሉ ፣ ስድስተኛው ኰንግረስ በወዝአደሩና በደሀው አርሶ አደር መካከል የሚፈጠረው ሕብረት በተለይ ለሶሻሊዝም አብዮት ድል አድራጊነት ዓይነተኛ ሁኔታ ነው የሚለውን የሌኒንን መመሪያ አበክሮ መጥቀስ ነበር ።

የሙያ ማህበራት ከሁሉም ገለልተኛ መሆን አለባቸው የሚለውን የሜንሼቪኰችን ንድፈ-ሀሳብ ኰንግረሱ አውግዞ የሩስያን ስርቶ አደር መደብ የሚጠብቀው ወቅታዊ ተግባር ሊያጠናቅቅ የሚችለው የቦልሼቪክ ፓርቲን አመራር የተቀበሉና ለመዋጋት ቆርጠው የተነሱ የሙያ ማህበራት ሆነው ሲገኙ ብቻ እንደሆነ አስገነዘበ ።

ኰንግረሱ በዚያን ወቅት በፈጠነ መንገድ በግብታዊነት ስለተነሱት የወጣት ሊጐች ውሳኔ አሳለፈ ። ፓርቲው ባደረገው ተከታታይ ጥረት የፓርቲው ተጠባባቂ የሆኑትን የነዚህን ለጋ ድርጅቶች ጉልህ ድጋፍ አገኘ ።



ኰንግረሱ ሌኒን ፍርድ ቤት ይቀርብ እንደሆን ተወያዩበት ። ካሜኔቭ ፣ ራይኰቭ ፣ ትሮትስኪና መሰሎቻቸው ገና ኰንግረሱ ከመካሄዱ ቀደም ብሎ ሌኒን ለጸረ-አብዮተኞች በተዘጋጀው ፍርድ ቤት መቅረብ አለበት ይሉ ነበር ። ጓድ ስታሊን የሌኒንን ለፍርድ መቅረብ አበክሮ ተቃወመ ። ይህ ፍትህ ሳይሆን ሕጋዊ ባልሆነ መንገድ የተገለጸ አድርጐ መውሰድ የስድስተኛው ኰንግረስ አቋም ነበር ። ኰንግረሱ ቡርዧዎች የሚፈልጉት አንድ ነገር ብቻ መሆኑን አልተጠራጠረም — ይኸውም የቡርዧው እጅግ አደገኛ ጠላት የሆነውን ሌኒንን አካላዊ ቅጣት (መግደል) ለመስጠት ሲሆን ፤ ኰንግረሱ ቡርዧው በወዝአደሩ አብዮታዊ መሪዎች ላይ የሚያደርሰውን አረመኔያዊ ስቃይ አውግዞ ለሌኒን የሰላምታ መልዕክት አስተላለፈ ።

ስድስተኛው ኰንግረስ አዲስ የፓርቲ ሕግ አረቀቀ ። እነዚህ ሕጐች መላው የፓርቲ ድርጅቶች በዲሞክራሲያዊ ማዕከላዊነት መመሪያ መሰረት መታነጽ እንደሚገባቸው የሚዘጋጁ ናቸው ።
ይህም ማለት ፤

1/ መላው የፓርቲ መሪ አካላት ፣ ከላይ እስከ ታች ፣ መመረጥ አለባቸው ።

2/ የፓርቲው አካላት ስለ እንቅስቃሴአቸው ለየክፍላቸው የፓርቲ ድርጅቶች በተወሰነ ጊዜ መቅረብ ያለባቸውን ዘገባዎች ማቅረብ አለባቸው ።

3/ ጠንካራ የፓርቲ ስነ ሥርዓትና የጥቂቶች ለብዙሀኑ መገዛት መኖር አለበት ።

4/ የበላይ አካላት ያሳለፉት ማናቸውም ውሳኔዎች ለየበታች አካላትና ለመላው የፓርቲ አባላት የጸና ይሆናል ።

ወደ ፓርቲው የሚመጡ አዳዲስ አባላት በአካባቢ የፓርቲ ድርጅቶች አማካይነት በሁለት የፓርቲ አባላት የድጋፍ ስጭነትና በአካባቢው የፓርቲ ድርጅት ጠቅላላ ስብሰባ ማጽደቅ ሊገቡ እንደሚችሉም በፓርቲው ሕጐች ላይ ተጠቀሰ ።

ስድስተኛው ኰንግረስ ሜዝራዮንትሲንና መሪያቸው የነበረውን ትሮትስኪን ወደ ፓርቲው እንዲገቡ ፈቀደ ። እነዚህም ከ1913 ዓ.ም. ጀምሮ በፔትሮግራድ የሚገኙ ትሮትስካይት-ሜንሼቪኮችና ከፓርቲው ተከፍለው የወጡ ጥቂት የቀድሞ ቦልሼቪኮችን ያቀፈ ትንሽ ቡድን ነበር ። በጦርነቱ ወቅት ሜዝራዮንትሲ ወላዋይ ድርጅት ነበር ። ቦልሼቪኮች ያለቅጥ ታግለዋል ። ይሁን እንጂ ከሜንሼቪኰችም ጋር በአያሌ ነጥቦች ሊግባቡ አልቻሉም ። ስለሆነም መሀል ሰፋሪ ፣ ወላዋይና ዋዣቂ አቋም ይይዛሉ ። ስድስተኛው የፓርቲ ኰንግረስ በተደረገበት ወቅት ሜዝራዮን

ትሲ በማናቸውም ነጥቦች ከቦልሼቪኮች ጋር እንስማማለንና ወደ ፓርቲው እንድንገባ ይፈቀድልን ሲሉ አሳወቁ ። በወቅቱ እውነተኛ ቦልሼቪኮች ይሆናሉ ከሚለው በስተቀር ጥያቄአቸውን ኮንግረሱ ተቀበለው ። እንዳንድ ሜዝራዮንትሲ ለምሳሌ ቦሎዳርስኪይና ኡሪትስኪይ እርግጠኛ ቦልሼቪኮች እየሆኑ መጡ ። እንደነ ትሮትስኪና ጥቂት መሰል ጓደኞቹ በኋላ ከፓርቲው እንደተገነጠሉ ሁሉ ቀድሞውኑ የገቡት ለፓርቲው ዓላማ ለመታገል ሳይሆን ከውስጥ ሆኖ ፓርቲውን ለማፋለስና ለማጥፋት ነበር ።

ስድስተኛው የፓርቲ ኮንግረስ ውሳኔዎች ወዝአደሩንና ደሀውን ገበሬ ለትጥቃዊ አመጽ ለማዘጋጀት የታቀዱ ነበሩ ። ስድስተኛው ኮንግረስ ፓርቲውን ለትጥቃዊ አመጽ ፣ ለሶሻሊስት አብዮት መራው ።

ኮንግረሱ ሠራተኞች ፣ ወታደሮችና ገበሬዎች ከቡርዧው ጋር ለሚደረገው ወሳኝ ጦርነት ሀይላቸውን ሁሉ እንዲያሰባስቡ ጥሪ በማድረግ የፓርቲ መግለጫ አወጣ ። መግለጫው ፡—

«በቆራጥነት ፣ በጀግንነትና ፣ በጥሞና ለምናካሄደው አዲስ ጦርነት የታጠቁ ጓዶችን አዘጋጁ ! ሀይላችሁን አሰባስባችሁ የውጊያ ረድፎችን አቋቁሙ ! ወዝአደሮችና ወታደሮች በፓርቲው ሰንደቅ ስር ተሰባሰቡ ! ፣ ምዝብር የመንደር ነዋሪዎች በዓርማችን ስር ተሰለፉ !» በሚሉ ቃላት ይደመድማል ።

## 5/ የጄኔራል ኮርኒሎቭ ጸረ-አብዮት ሴራ ፤ የሴራው መደምሰስ ፤ የፔትሮግራድና የሞስኮ ሶቭየቶች ወደ ቦልሼቪኮች መግባት ፡-

መላውን ስልጣን በመዳፉ ካስገባ በኋላ ቡርዧው ተዳክመው ያሉትን ሶቭየቶች ለማጥፋትና ግልጽ የሆነ ጸረ-አብዮተኛ አምባገነንነት ለማስፈን ዝግጅቱን ጀመረ ። ሚሊየነሩ ከበርቴን ሪያሺንስኪይ በግልጽ በሆነ መንገድ ከሁኔታው ለመውጣት «የምስኪን ሕዝቦችን በረሀብ የተጐሳቀሉ እጆች የሕዝቡን አስመሳይ ጓደኞችን ጉሮሮ ለማነቅ » ነበር ሲል ለፈፈ ። በጦር ግንባር በወታደሮች ላይ አረመኔያዊ የቂም በቀል እርምጃ በመውሰድ ወታደራዊ ፍርድ ቤቶች በጅምላ የሞት ብያኔ አሰሙ ። በነሐሴ 3 ቀን 1917 ዓ ም የጦር ሀይሉ ዋና አዛዥ የሆነው ጄኔራል ኮርኒሎቭ የሞት ቅጣቱ በደጀንም በኩል መምጣት እንዳለበት ጠየቀ ።

በነሐሴ 12 ቀን በጊዜያዊ መንግሥት የመንግሥቱ ምክር ቤት ተጠርቶ የቡርዧውንና የመሬት ከበርቴውን ሀይል እንዲያስተባብሩ ፣ በግራንድ ሞስኮ በሚገኘው በግራንድ ቲያትር ቤት ውስጥ ስብሰባው ተከፈተ ። ምክር ቤቱ በይበልጥ በመሬት ከበርቴዎች ፣ ቡርዧዎች ፣ ጄኔራሎች ፣ መኮንኖችና ሐብታም ገበሬዎች ተወካዮች የተሳተፉበት ነበር ። በስብሰባው ላይ ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች ሶቭየቶችን በመወከል ተገኝተው ነበር ።



የመንግሥቱን ምክር ቤት ስብሰባ በመቃወም ቦልሼቪኮች ስብሰባው በተደረገበት እለት በሞስኮው ውስጥ አብዛኛው ሠርቶ አደሮች የተሳተፉበትን አጠቃላይ የሥራ ማቆም አድማ ጠሩ ። ከዚሁ ጋር በሌሎችም አያሌ ከተሞች የስራ ማቆም አድማዎች ተደረጉ ።

ሶሻሊስት አብዮተኛው ከረንስኪይ ማናቸውም በአብዮታዊ እንቅስቃሴ ላይ የሚደረጉ ሙከራዎች ፣ ገበሬዎች የመሬት ከበርቴዎችን መሬት ለመያዝ የሚያደርጉትን ያልተፈቀደ ጥረት ጨምሮ « በብረትና በደም » እናፍናለን ሲል በምክር ቤቱ ውስጥ በጉራ ተናገረ ።

ጸረ-አብዮተኛው ጄኔራል ኮርኔሎቭ « ኮሚቴዎችና ሶቭየቶች መደምሰስ አለባቸው » ሲል ፍርጥርጥ ባለመንገድ ጠየቀ ።

ባለባንኮች ፣ ነጋዴዎችና የፋብሪካ ባለቤቶች ወደ ጠቅላይ መምሪያው በመጉረፍ ጄኔራል ኮርኔሎቭን በገንዘብና በሞራላዊ ድጋፍ ከጐንህ እንቆማለን ሲሉ ቃል ገቡ ።

« ተባባሪዎቹ » የእንግሊዝና የፈረንሣይ ተወካዮች እንዲሁ ወደ ጄኔራል ኮርኔሎቭ ዘንድ በመሄድ አብዮቱን ለመደምሰስ የሚደረገው እርምጃ እንዳይዘገይ ጠየቁ ።

የጄኔራል ኮርኔሎቭ ጸረ-አብዮት ሴራ አውራ እየሆነ በመምጣት ላይ ነበር ።

ኮርኔሎቭ ጸረ-አብዮት ሴራውን በገሀድ አዘጋጀ ። ያለውን ትኩረት ለመለወጥ እንዲቻል ፣ ተመሳጣሪዎቹ ፣ ቦልሼቪኮች በአብዮቱ የመጀመሪያዎቹ ስድስት ወራት መጨረሻ ላይ ማለትም በነሐሴ 27 ቀን በፔትሮግራድ ውስጥ የሚካሄድ አመጽ አዘጋጅተዋል በማለት ማውራት ጀመሩ ። በከረንስኪ የሚመራው ጊዜያዊ መንግሥት ቦልሼቪኮችን አጥቅቶ በወዝአደሩ ፓርቲ ላይ ሽብር አስፈነ ። ከዚሁ ጋር አብሮ ጄኔራል ኮርኒሎቭ ፔትሮግራድን ለመውረርና ሶቪየቶችን አውድሞ ወታደራዊ አምባገነንነት ለመመስረት አያሌ ወታደራዊ ቡድኖችን በመሰብሰብ ለመላክ አዘጋጀ ።

ኰርኔሎቭ ጸረ-አብዮታዊ ተግባሩን አስመልክቶ ከከረንስኪ ጋር የመጀመሪያውን ደረጃ ስምምነት አደረገ ። ይሁን እንጂ የካርኔሎቭ እርምጃ የተጀመረው ከረንስኪይ በድንገት ቀኝ ኋላ በመዞር ራሱን ከስምምነቱ ገሸሽ ከማድረጉ የቀደመ አልነበረም ። ኮርኔሎቭን በመቃወም የተነሳውን ሰፊ ሕዝብ በመፍራትና ከኮርኔሎቭ ጉዳይ ውስጥ ወዲያውኑ ራሱን ካላወጣ ይህንን ኮርኔሎቭን በመቃወም የተነሳውን ሕዝብ ማጥፋት የከረንስኪንም ቡርዧ መንግስት አብሮ መደምሰስ መሆኑን ከረንስኪ ተገነዘበ ።

በነሐሴ25 ቀን ኮርኒሎቭ «አባት አገርን ለማዳን»በሚልአዋጅ በጄኔራል ክራይሞዝየሚመራ ሶስተኛውን ፈረሰኛ ጦር ወደ ፔትሮግራድ አዘመተ።

በሌላ በኩል ደግሞ የኮርኔሎቭን ሴራ በመቃወም ፣ ጸረ-አብዮተኞች ለሚ
ያካሂዱት የማጥቃት ዘመቻ የቦልሼቪክ ፓርቲ ማእከላዊ ኮሚቴ ንቁ
የመቋቋም እርምጃ እንዲያደርጉ ለሠራተኞችና ለወታደሮች ጥሪ አደረገ ።
በነዚያ ቀናት ውስጥ እያሌ የቀይ ጦር ቡድኖች እንደ እሸን ፈሉ ። የሙያ
ማኅበራት አባሎቻቸውን አነሳሱ ። የፔትሮግራድ አብዮታዊ ጓድ ለጦር
ነቱ ዝግጁ ሆነ ። በፔትሮግራድ ዙሪያ ምሽጐች ተቆፈሩ ። እሾህማ ሽቦ
ዎች በየአስፈላጊው ቦታዎች ተወሳስበው ተዘረጉና ወደከተማይቷ የሚ
ያመራው የባቡር መስመር ተቋረጠ ። ከተማይቷን ለማዳን ብዙ ሺህ
ወታደሮች ከካሮንስታድት መጡ ። ወደ ፔትሮግራድ በመገስገስ ላይ ወደ
አለው « አረመኔያው ክፍለ ጦር » ተወካዮች ተላኩ ። ተወካዮቹ « አረመ
ኔያዊው ክፍለ ጦር » የካውካሲያንን ተራሮች እንዲወጡ ታዘው በመዳከር
ላይ ለነበሩት ሁሉ የኮርኒሎቭን ተግባር በመተንተን በሚገልጽላቸው
ጊዜ ወታደሮቹ ወደፊት መሄዱን ተቃወሙ ። ሌሎችም ቀስቃሽ ቡድኖች
በኮርኒሎቭ ሠራዊት ውስጥ ተሠራጭተው ነበር ። አደጋ በተፈጠረበት
ቦታ ሁሉ ኮርኒሎቭን ለመዋጋት አብዮታዊ ኮሚቴዎችና ጠቅላይ መም
ሪያዎች ይቋቋሙ ነበር ።

በነዚህም ቀናት ሞታቸው እየተቃረበ የመጣው የሶሻሊስት አብዮ
ተኞችና የሜንሼቪኮች መሪዎች ፣ ከነርሱም መሀል ከረንስኪይ ፣ በዋና
ከተማይቷ ውስጥ የኮርኔሎቭን ሀይል ለማንበርከክ የሚችል ጠንካራ
ሀይል የቦልሼቪክ ፓርቲ ብቻ መሆኑን በማመን ከቦልሼቪኮች ጐን ለመ
ሰለፍ ቆርጠው ተነሱ ።

ይሁን እንጂ የኮርኔሎቭን ሴራ ለመደምሰስ ሰፊውን ሕዝብ በሚቀሰ
ቅሱበት ጊዜ ሁሉ የከረንስኪን መንግሥት በመቃወም የሚያደርጉትን
ትግል ለአንድ አፍታም ቢሆን አላቋረጡም ነበር ። የከረንስኪ መንግ
ሥት ፤ የሚያራምደው ፖሊሲ የኮርኒሎቭን ጸረ-አብዮት ሴራ በመደገፍ
ውጤትአማ ለማድረግ መሆኑን በመጠቆም የሜንሺቪኮችንና የሶሻሊ
ስት አብዮተኞችን ምንነት ለሰፊው ሕዝብ አጋልጠዋል ።

በዚህም እርምጃ ውጤት የኮርኔሎቭ ሴራ ተደመሰሰ ። ጀኔራል
ክራይሞቭም ራሱን ገደለ ። ኮርኔሎቭና ተመሳጣሪ ተከታዮቹ ዴንኪንና
ሉኮመስኪይ ታሰሩ ( ይሁንና ከረንስኪ ወዲያውኑ ለቀቃቸው)።

የኮርኒሎቭ ሴራ መንበርከክ በጸረ-አብዮተኞች አንጻር አብዮታው
ያን ያላቸውን ጥንካሬ በታላቅ ግርማ አሳየ ። መላው ጸረ-አብዮት ካምፕ ከሶ
ሻሊስት አብዮተኞች ጀኔራሎችና ሕገመንግሥታዊ ዴሞክራቲክ ፓርቲ
እስከ ቡርዧው ቀዳዳዎች ሰርገው የተወሳሰቡ ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት
አብዮተኞች ላይ መጥፎ ወቅት እንደመጣባቸው በገሀድ አሳየ ።

ከዚህም በላይ የኮርኔሎቭ ሴራ መደምሰስ የቦልሼቪክ ፓርቲ የአብ
ዮቱ ወሳኝ ሀይል እየሆነ ማደጉንና ጸረ-አብዮተኞች የሚሸርቡትን ማና
ቸውንም ዓይነት ሴራ መደርመስ እንደሚችል አሳየ ። ፓርቲያችን አመ



ራሩን አልጨበጠም ፣ ይሁን እንጂ በኮርኔሎቭ ጸረ-አብዮት ሴራ ወቅቶች
ሁሉንም ነገር ስልጣን እንደጨበጠ ሀይል ያከናውን ነበር ። የሚያወጣ
ቸው መሣሪያዎች በሰራተኞችና በወታደሮች ፍጹም ፈቃደኝነት ይከና
ወኑ ነበር ።

በመጨረሻም የኮርኔሎቭ ሴራ መደምሰስ ለዓይን የሞቱ (የጠፉ)
ይመስሉ የነበሩ ሶቭየቶች በርግጥም ያለ ፣ ታላቅ የአብዮታዊ መቋቋም
የተዳፈነ ሀይል መሆኑን አሳየ ። ሶቭየቶችና አብዮታዊ ኮሚቴእቸው
የኮርኔሎቭን ሠራዊት ፈለግ የገደቡና ሀይላቸውን ያነኰኮቱ መሆናቸው
አያጠራጥርም ።

የተካሄደው ጸረ-ኮርኔሎቭ ትግል በመጠውለግ ላይ ለነበሩት የሠራ
ተኞችና የወታደሮች ተወካዮች ሶቭየቶች አዲስ ጥንካሬ ሰጣቸው ፤
ለአጐብዳጁ ፖሊሲ ሀሣባቸውን ከመለወጥ ነፃ አደረጋቸው ፤ ወደ አብ
ዮታዊ ትግሉ የሚያመራ ጐዳና በመክፈት ወደቦልሼቪክ ፓርቲ አመ
ራቸው ።

ቦልሼቪክ ፓርቲ በሶቭየቶች ውስጥ ያለው ተደማጭነት ከመቼ
ውም ጊዜ ይልቅ አደገ ።

በገጠር አውራጃዎችም እንዲሁ የቦልሼቪኮች ተደማጭነት በፈጠነ
ሁኔታ ተስፋፋ ።

በኮርኔሎቭ ሴራ ፣ የመሬት ከበርቴዎችና ጀኔራሎች፤የቦልሼቪክ ፓር
ቲንና ሶቭየቶችን በማውደም ድል ከተቀዳጁ ገበሬውን እንደ ሚወጋ
ለሰፊው ገበሬ ግልጽ እየሆነለት መጣ ። ስለሆነም ሰፊው ደሀ ገበሬ በቦል
ሼቪክ ዙሪያ መሰባሰብ ጀመረ ። ከሚያዝያ እስከ ነሐሴ ወር 1917 ዓ.ም.
ድረስ ባሉት ወቅቶች ውስጥ በመዋዠቁ ምክንያት የአብዮቱን እድ
ገት ወደ ኋላ የጐተተው የመሀከለኛው ገበሬ ኮርኔሎቭ ከተንበረከከ በኋላ
በእርግጥ ከደሀው ገበሬ ጋር ያለውን ሐይላቸውን በማስተባበር ፤ ወደ
ቦልሼቪክ ፓርቲ መዞር ጀመረ ። ብዙሀኑ ገበሬ ከጦርነቱ ውስጥ የሚ
ገላግላቸውና የመሬት ከበርቴዎችን ገርስሶ መሬትን ለገበሬዎች ለመ
መለስ የሚዘጋጅ ቦልሼቪክ ፓርቲ ብቻ እንደሆነ በሚገባ ተገነዘቡ ።
የመስከረምና የጥቅምት 1917 ዓ. ም. ወሮች የእያሌ ገበሬዎች ሁዳዳዊ
ባለቤትነት በከፍተኛ ደረጃ ለማደጉ መልካም ምስክር ነው ። የመሬት
ከበርቴዎችን መሬት በኃይል እየሄዱ ማረስ እየተስፋፋ መጣ ። ገበሬዎቹ
የአብዮቱን ጐዳና ተከተሉ ምንም እንኳ ቢያባብሏቸው ወይም የሚቀጡ
ቡድኖች ቢላኩባቸውም ከዚህ በኋላ ፍጹም ሊበግሩአቸው አልቻሉም ።

## የአብዮቱ እሳት ጋመ

ሶቭየቶች ይዞታቸውን በመለወጥ ቦልሼቪካዊ በመሆን ያንሰራሩ
በት ወቅት ተከተለ ። ፋብሪካዎች ወፋጮዎችና ወታደራዊ ቡድኖች በሜ
ንሼቪኮችና በሶሻሊስት አብዮተኞች ምትክ አዲስ ምርጫ በማካሄድ ቦል

ቪኮችን እየመረጡ ተወካዮቻቸውን ለሶቪየቶች ላኩ ። በነሐሴ 31 ቀን በኮርኒሎቭ ላይ ድል በተገኘበት ቀን ማግሥት የፔትሮግራድ ሶቭየቶች የቦልሼቪክን ፖሊሲ መደገፋቸውን አሳወቁ ። በቻኪሄድዚ የሚመራው የፔትሮግራድ ሶቭየት ፕሬዚዲየም የነበሩት የቀድሞዎቹ ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች ሥልጣኑን በፈቃዳቸው ለቀቁ ። ስለሆነም ሁኔታው ለቦልሼቪኮች ጥርጊያ መንገድ ከፈተ ። መስከረም 5 ቀን የሞስኮ ሠራተኞች ተወካዮች ሶቭየት ከቦልሼቪኮች ጐን ተሠለፉ ። የሞስኮው ፕሬዚዲየም ሶሻሊስት አብዮተኞችና ሜንሼቪኮች እንዲሁ ስልጣናቸውን ለቀቁና ለቦልሼቪኮች የበለጠ አመቺ ሁኔታ ፈጠሩ ።

ይህም ማለት ለተሳካ አመጽ አስፈላጊ የሆኑ ሁኔታዎች አሁን የበሰሉ መሆናቸውን የሚያሳዩ ነበሩ ።

«ሥልጣን ለሶቭየቶች የሚለው መፈክር እንደገና የጊዜው ጥያቄ ሆነ ። « ሥልጣን ለሶቭየቶች ! » የሚለው መፈክር ለሜንሼቪኮችና ለሶሻሊስት አብዮተኞች ሥልጣንን የሚያሸጋግር መፈክር ሊሆን ከቶም አይችልም ነበር ። በአሁኑ ወቅት መፈክሩ ጊዜያዊውን መንግሥት በመቃወም እንዲያምጹ ለሶቭየቶች ጥሪ የሚያደርጉ ፣ ዓላማውም በሀገሪቷ ውስጥ ያለውን መላውን ሥልጣን አሁን በቦልሼቪኮች ለሚመሩ ሶቭየቶች የሚያሸጋግር ነበር ።

በአንድባዳጁ ፓርቲዎች መሀከል አለመስማማት ፣ መፈረካከስ ተፈጠረ ።

አብዮታዊ ገበሬዎች ባሳደሩት ታላቅ ግፊት ለቡርዧው የአንድባዳጁን ፖሊሲ አለመቀበላቸውን ያጋለጡ በሶሻሊስት አብዮታውያን ፓርቲ ውስጥ «ግራ ለበስ» ሶሻሊስት አብዮታውያን የተሰኙ ግራ ክንፍ ቡድኖች ተመሠረቱ ።

በሜንሼቪኮችም መሀከል እንደዚሁ ወደ ቦልሼቪኮች ያዘነበሉ « አለም አቀፋውያን » የተሰኙ « ግራ ለበስ » ቡድኖች ተከሰቱ ።

ባላቸው አቋም ተደማጭነታቸው አክትሞባቸው በነበራቸው አቋም መቀጠል የተሳናቸው ስርዓተ አልበኞችም እንዲሁ ወደ ተወሰኑ አነስተኛ ቡድኖች ተሰነጣጠሩ ። ከመሀከላቸውም ጥቂቶቹ ከወንጀለኛ ቡድኖች ጋር ተዋሀዱ ። ሌቦችና ጠብ አጫሪዎች የሕብረተሰቡ ዝቃጭ ፣ አታላዮች ሆኑ ። ሌሎቹ ደግሞ « በጸና እምነት » ገበሬዎችንና ትናንሽ ከተሜዎችን የሚዘርፉና የሠራተኛ ክበቦች የሚያዋጡትን ገንዘብ ለራሳቸው የሚወስዱ ቀማኞች ሆኑ ። ሌሎችም እንዲሁ በገሀድ ወደ ጸረ-አብዮተኞች ካምፕ በመግባት ራሳቸውን የቡርዧው አገልጋይ አድርገው ጊዜአቸውን ጐጆአቸውን በመቀለስ ሊአጠፉ ፈለጉ ። እነዚህ ሰዎች ማንኛውንም ዓይነት ሥልጣን ይቃወማሉ ።



ኮርኔሎቭ ከተደመሰሰ በኋላ ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮታውያን እንደገና አንዴ የአብዮቱን ሞገዳዊ እድገት ለመጺረር ሞከሩ ። ይህን ሀሳብ በመንፈሳቸው ውስጥ በመያዝ መስከረም 12 ቀን 1917 ዓ ም የሶሻሊስት ፓርቲዎችን ፣ የአንድባዳጅ ሶቭየቶችን ፣ የሙያ ማህበራትን ፣ ዜሞስትቮስን ፣ የንግድና የኢንዱስትሪ ክበቦችንና ወታደራዊ ቡድኖችን የያዘ የመላው ሩስያ ዲሞክራቲክ ጉባኤ ጠሩ ። ጉባኤው ቅድመ ፓርላማ ተብለው የሚታወቁ ፣ የሪፓብሊኩን ጊዜያዊ መማክርት አቋቋመ ። አንድባዳጆቹ በቅድመ ፓርላማው ድጋፍ አብዮቱን ለማሰናከልና አገሪቷን በመከተል ላይ ካላቸው ከሶቭየት አብዮት ወደ ቡርዧው ሕገ መንግሥታዊ እድገት ፣ ወደ ቡርዧው ፓርላማዊ ፈለግ ለማዞር ታላቅ ተስፋ አድርገው ነበር ። ነገር ግን ይህ የአብዮቱን ጉማ ወደ ኋላ መጐተት የፖለቲካዊ ክስረት ተስፋ የሌለው ጥረት ነበር ። በውድቀት ለመጨረስ ወስነው ነበርና አልቀረም በውድቀት ደመደሙት ። ሠራተኞች በአንድባዳጆች ፓርላማዊ ጥረት በፌዝ ሳቁባቸውና ጥረታቸውን ፕሪድ ፓርላሜንት (ቅድመ ፓርላማ) ( ፕሬድ ባንኪ ) « ቅድመ መታጠቢያ ቤት » ሲሉ ጠሩአቸው ።

የቦልሼቪክ ፓርቲ ማእከላዊ ኮሚቴ በቅድመ ፓርላማው ላለመካፈል ወሰነ ። እርግጥ ነው ፣ በቅድመ ፓርላማው ውስጥ እንደነ ካሜኔቭና ቲኦዶሮቪች የመሰሉትን የያዘ የቦልሼቪኮች ቡድን በቅድመ ፓርላማው ማእከላዊ ኮሚቴ እንዳይሳተፉ አስገደዳቸው ።

ካሜኔቭና ዜኖቪየቭ ፓርቲው ለአመጽ ከሚያደርገው ዝግጅት አቅጣጫውን ለማስለወጥ ባላቸው ፍላጐት በቅድመ ፓርላማው ውስጥ እንዲካፈሉ በመደጋገም አሳሰቡ ። የቦልሼቪክ ቡድን ባካሄደው የመላው ሩስያ ዲሞክራሲያዊ ጉባኤ ላይ ጓድ ስታሊን እንዲያውም ቅድመ ፓርላማውን « የኮርኔሎቭ ውርጃ » ሲል ጠርቶታል ።

ቅድመ ፓርላማው በርግጥ ለሠራተኛው ሕዝብ አንድ ነገር ማድረግ እንደሚችል የማይሆን ተስፋ በሰፊው ሕዝብ ውስጥ መናኘት በመሆኑ ምክንያት ሌኒንና ስታሊን ለአጭር ጊዜም እንኳ ቢሆን በቅድመ ፓርላማው ውስጥ መሳተፍን ትልቅ ስህተት አድርገው ቆጥረውታል ።

ከዚሁ ጋራ ቦልሼቪኮች የአብዛኛውን ወገን ተደማጭነት እናገኝበታለን ብለው የገመቱትን የሶቭየቶችን ሁለተኛ ኮንግረስ ለመጥራት ጥንቃቄ በተሞላበት መንገድ ዝግጅት አደረጉ ። በቦልሼቪክ ሶቭየቶች ግፊት ፤ በመላው ሩስያ ማእከላዊ ባለስልጣን ኮሚቴዎች ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞች የሚያሴሩት አሻጥር ቢኖርም ቅሉ በጥቅምት ወር 1917 ዓ. ም አጋማሽ ላይ የመላው ሩስያ ሶቭየቶች ኮንግረስ ተጠራ ።

6/ <u>የፔትሮግራድ የጥቅምቱ አመጽና የጊዜያዊው መንግሥት በቁጥጥር ሥር መዋል ፤</u>

<u>የሶቭየቶች ሁለተኛው ኮንግሬስና የሶቭየት መንግሥት መመሥረት ፤ ስለ ሰላምና መሬት ሁለተኛው የሶቭየቶች ኮንግረስ ድንጋጌ ፤ የሶሻሊስት አብዮት ድል የሶሻሊስት አብዮት ድል ምክንያቶች ፡—</u>

ቦልሼቪኮች ጥበብ በተሞላበት መንገድ ለአመጽ ዝግጅት ማድረግ ጀመሩ ። ሌኒን በሁለቱም ዋና ከተማዎች በሞስኮና በፔትሮግራድ የሠራተኞችና ወታደሮች ተወካዮች ሶቭየቶች ውስጥ የብዙሀኑን ተቀባይነት ለማረጋገጥ ፣ ቦልሼቪኮች የበትረ መንግሥቱን ሥልጣን በመዳፋቸው ማስገባት ይኖርባቸዋል ፣ አለባቸውም ሲል ገለጸ ። የአለፉትን የሂደት ፈለግ በመመርመር ሌኒን « ብዙሀኑ ሕዝብ ከኛ ጋር ነው ። » የሚለውን እውነታ ለማእከላዊ ኮሚቴውና ለቦልሼቪክ ድርጅቶች በጻፈው ጽሁፎችና ደብዳቤዎች አበክሮ ገልጾታል ። ሌኒን ፣ አጥቂ ጓዶችን ፣ የባህር ሐይሉንና ቀይ ዘቦችን እንዴት መገልገል እንደሚገባው ፣ የአመጹን መሳካት ለማረጋገጥ በፔትሮግራድ ውስጥ የትኞቹ ቁልፍ ቦታዎች ናቸው መያዝ ያለባቸው ፣ ሌሎችም መሰል ጥያቄዎችን መልስ በሚገባ የሚያሳይ ጠለቅ ያለ እቅድ ነደፈ ።

ጥቅምት 7 ቀን ሌኒን በሚስጢር ከፊንላንድ ወደ ፔትሮግራድ ገባ ። ጥቅምት 10 ቀን 1917 ዓ. ም. በመጪው ጥቂት ቀናት ውስጥ ትጥቃዊ አመጽ ለመጀመር የተወሰነባትን ፣ የፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ ታሪካዊ ስብሰባ አደረገ ። በሌኒን ረቂቅ ማእከላዊ ኮሚቴው ያሳለፈው ታሪካዊ ውሳኔ ፡—

« ማእከላዊ ኮሚቴው የሩስያ አብዮት ዓለም አቀፍ ሁኔታ (የዓለም ሶሻሊስት አብዮት በመላው አውሮፓ በመቀጣጠል ላይ ለመሆኑ ከፍተኛ መግለጫ የሆነው የጀርመን ባህር ሀይል አመጽ ፣ የሩስያን አብዮት ለመታገል ዓላማ በማድረግ በኢምፔሪያሊስቶች መሀከል የተደረገው የሰላም ስምምነት) ና ወታደራዊ ሁኔታው የሩስያ ቡርዧ ፤ ከረንስኪና ተከታዮቹ ፔትሮግራድን ለጀርመን አሳልፈው ለመስጠት መወሰናቸው አጠያያቂ አለመሆኑና የወዝአደሩ ፓርቲ በሶቭየቶች ዘንድ የአብዛኛውን ተደማጭነት የማትረፉ እውነታ ይህ ሁሉ ከገበሬዎች አመጽ ጋር የተጣመረ የሕዝቡ እምነት ወደ ፓርቲያችን መዞሩ (በሞስኮ የተደረገው ምርጫ) እንዲሁም ፣ በመጨረሻ ለሁለተኛው የኮርኒሎቭ ጉዳይ በገሀድ የተደረጉት ዝግጅቶች (ሠራዊቱ ወደ ፔትሮግራድ አልሄድም ፣ አሻፈረኝ ማለቱ ፣ የሀብታም ገበሬዎች ፔትሮግራድ በፍጥነት መላክ ፣ የሚንስክ በሐብታም ገበሬዎች መከበብ ፣ ወዘተ . . .) በሚገባ ተንትኖ እነዚህ ሁሉ ተዳምረው ትጥቃዊውን አመጽ የወቅቱ አንገብጋቢ ጥያቄ አድርገውታል ።

« ስለሆነም ትጥቃዊ አመጽ የማይቀር በመሆኑና ለትጥቃዊ አመጹም ወቅቱ አመቺ በመሆኑ ፣ ማእከላዊ ኮሚቴው በዚሁ መሰረት ለመም



ቹራትና ማናውንም ተግባራዊ ጥያቄዎች ( የሰሜናዊ አካባቢ የሶቭየቶች ኮንግረስ ፣ የሰራዊቱ ከፔትሮግራድ ለቅቆ መውጣት ፣ የኛ ሰዎች በሞስኮና በሜንስክ የሚወስዱት እርምጃዎች ወዘተ . . ) ለመወያየትና ለመወሰን እንዲቻል ከዚህ ነጥብ በመነሳት ለመላው የፓርቲ ድርጅቶች ትእዛዛ ሰጠ ። » (የሌኒን ምርጥ ሥራዎች እንግሊዝኛ ኅትም ሞስኮ 1947 ዓ. ም. ቅጽ 2 ገጽ 135)

የማእከላዊ ኮሚቴው ሁለቱ አባሎች ፣ ካሜኔቭና ዜኖቪየቭ ይህንን ታሪካዊ ውሳኔ በመቃወም ተናገሩ ፣ ድምጽም ሰጡበት ። እንደሜንሼቪኮች ሁሉ እነርሱም የቡርዧውን ፓርላማዊ ሪፑብሊክ ተመኙና ሶሻሊስት አብዮትን ለማካሄድ በቂ ጥንካሬ አልነበረውም ፣ ያም ማለት ሥልጣኑን ለመውሰድ ገና በቂ ጥንካሬ የለውም ሲሉ ሠራተኛውን መደብ ካዱት ።

በስብሰባው ላይ ትሮትስኪይ ውሳኔውን በቀጥታ በመቃወም ድምጽ አይስጥ እንጂ ፣ የአመጸውን እድል ወደታች የሚያወርድና እንዲጨናገፍ የሚያደርገውን የማሻሻያ ሀሳብ አቀረበ ። ትጥቃዊ አመጽ ሁለተኛው የሶቭየቶች ኮንግረስ ስብሰባ ከማድረጉ በፊት መጀመር የለበትም ሲል ተቃወመ ። ይህም ተቃውሞ ማለት አመጸውን ማዘግየት ፣ የሚጀመርበትን ቀን በመጠቆም ጊዜያዊውን መንግሥት ማስጠንቀቅ ማለት መሆኑ ነው ።

የቦልሼቪክ ፓርቲ ማእከላዊ ኮሚቴ ወደ ዶኔት ሸለቆ ፣ ኡራልስ ፣ ሄልሲንግፎርስ ፣ ክሮንስታድት ፣ በምዕራባዊ ሰሜን ግንባርና ሌሎችም ቦታዎች አመጸውን ለማደራጀት ተወካዮቹን አሰማራ ። ቮሮሺሎቭ ፣ ሞሎቶቭ ፣ ዲዘርዚንስኪይ ፣ እርጆኒኪድዝ ኪሮቭ ፣ ካጋኖቮች ፣ ኩባይሼቭ ፣ ፉሩንዜ ፣ ያሮስላቪስኪይና ሌሎችም ጓዶች በተለይ በክፍላተ ሀገር አመጸውን እንዲመሩ ፓርቲው መደባቸው ። ጓድ ዚሁዳኖቭ በኡራልስ ውስጥ በባድሪንስክ በሚገኙ የጦር ሀይሎች መሀከል እንዲሰራ ተደረገ ። የማዕከላዊ ኮሚቴ ተወካዮች ለቦልሼቪክ ፓርቲ የክፍላተ ሀገር መሪ አባሎች የአመጸውን እቅድና የፔትሮግራድን አመጽ ለመደገፍ እንዲዘጋጅ በማነሳሳት ገለጻ አደረጉላቸው ።

በፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ መመሪያ መሰረት የፔትሮግራድ ሶቭየቶች አብዮታዊ ወታደራዊ ኮሚቴ አቋቋሙ ። ይህ አካል በግልጽ የሚሰራ የአመጸው ጠቅላይ መምሪያ ሆነ ።

እስከዚያው ድረስ ጸረ-አብዮተኞችም እንዲሁ በችኮላ ሀይላቸውን ያሰባስቡ ነበር ። የጦር ሰራዊት መኮንኖች ፡ የመኮንኖች ሊቅ የተሰኘውን ድርጅት መሠረቱ ። ጸረ-አብዮተኞች አጥቂ ባታሊዮኖች ለመመስረት በየቦታው ጠቅላይ መምሪያዎችን አቋቋሙ ። በጥቅምት መጨረሻ ላይ ጸረ-አብዮተኞች በነርሱ የሚመሩ 43 አጥቂ ባታሊዮኖች ነበሩአቸው ። ልዩ የቅዱስ ጊዮርጊስ መስቀል ፈረሰኛ ባታሊዮኖች ተመሰረቱ ።

የከረንስኪ መንግሥት የመንግሥቱን መቀመጫ ከፔትሮግራድ ወደ ሞስኮ የማዛወሩን ጥያቄ ተቀበለው ። ይህ ደግሞ ከተማይቱን ከአመጽ ለማዳን ፔትሮግራድን ለጀርመኖች አሳልፎ ለመስጠት መዘጋጀቱን በግልጽ የሚያሳይ ነበር ። የፔትሮግራድ ሰራተኞችና ወታደሮች ተቃውሞ ጊዜያዊው መንግሥት በፔትሮግራድ እንዲቀር አስገደደ ።

በጥቅምት 16 ቀን የማእከላዊ ኮሚቴው ሰፊ ስብሰባ አካሄደ ። ይህ ስብሰባ አመጻውን ለመምራት በጓድ ስታሊን የሚመራ የፓርቲ ማእከል መረጠ ። ይህ የተመረጠው የፓርቲ ማእከል የፔትሮግራድ ሶቭየት አብዮታዊ ወታደራዊ ኮሚቴና የመላውን አመጽ ተግባራዊ አቅጣጫ የሚመራ ሀይል ነበር ።

በማእከላዊ ኮሚቴው ስብሰባ ላይ አጐብዳጆቹ ዚኖቭየቭና ካሜኔቭ አመጻውን ዳግመኛ ተቃወሙ ። ስብሰባውን ሳይቀበሉ ቀርተው በፕሬስ ላይ በግልጽ አመጻውን ተቃወሙ ፣ ፓርቲውን ተቃወሙ ። በጥቅምት 18 ቀን ቦልሼቪኮች ለአመጽ በመዘጋጀት ላይ መሆናቸውን በመግለጽ ካሜኔቭና ዚኖቭየቭ በሜንሼቪኮች ጋዜጣ በኖቫየዚዝን ላይ አስፈሩና ካሜኔቭና ዚኖቪየቭ አመጻውን የጀብደኝነት ቁማር አደረጉት ሲሉ ተናገሩ ። ካሜኔቭና ዜኖቭየቭ ማእከላዊ ኮሚቴው አመጻውን አስመልክቶ ያሳለፈውን ውሳኔ ለጠላት አጋለጡ ። አመጻው በአጭር ቀናት ውስጥ ሊደረግ መታቀዱን አሳወቁ ። ይህ ክደት ነው ። ይህን አስመልክቶ ሌኒን «ካሜኔቭና ዚኖቪየቭ የፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ በሮድዝያንኮና በከረንስኪ ላይ ስለሚደረገው ትጥቃዊ አመጽ ያሳለፈውን ውሳኔ ከድተዋል ።» ሲል በጽሁፉ ገለጸ ። ሌኒን ዚኖቪየቭና ካሜኔቭ ከፓርቲው እንዲባረሩ ለፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ ጥያቄ አቀረበ ።

ከሀዲዎቹ በቅድሚያ በማስጠንቀቃቸው የአብዮቱ ቀንደኛ ጠላቶች አመጹን ለመከላከልና የአብዮቱን መሪ አባሎች — ቦልሼቪክ ፓርቲን — ለመደምሰስ በአንድ ጊዜ እርምጃዎችን መውሰድ ጀመሩ ። ጊዜያዊው መንግሥት በሚስጥር ስብሰባ በመጥራት ቦልሼቪኮችን ለመውጋት ወሰነ ። ጥቅምት 19 ቀን ጊዜያዊው መንግሥት ወታደሮችን በአስቸኳይ ወደ ፔትሮግራድ ለመላክ ከየግንባሩ ሰበሰበ ። አውራ መንገዶች በቃኚ ጓዶች ተጥለቀለቁ ። ጸረ-አብዮተኞች የተለየ ትልቅ ሀይል ወደ ሞስኮ ማስገባቱ ተሳካላቸው ። ጊዜያዊው መንግሥት ፣ በሁለተኛው የሶቭየቶች ኮንግረስ ዋዜማ ላይ ስሞልኒ — የቦልሼቪክ ማእከላዊ ኮሚቴ ጠቅላይ መምሪያ እንዲወረርና እንዲያዝ ብሎም የቦልሼቪክ ማእከላዊ ጠቅላይ መምሪያ— እንዲመታ እቅድ ነደፈ ። ይህንን ተግባር በስራ ላይ ለማዋል መንግሥቱ ታማኝነታቸውን የሚያምንባቸውን ሰራዊቶች ወደ ፔትሮራግድ ጠራቸው ።



ነገር ግን የጊዜያዊው መንግሥት ዕድሜ በቀናትና እንዲያውም በደቂቃ የሚቆጠር ነበር ። የሶሻሊስት አብዮትን ድል አድራጊ ጉዞ አንዳችም ሊያደናቅፈው የሚችል ነገር የለም ።

ጥቅምት 21 ቀን ቦልሼቪኮች ለሁሉም አብዮታዊ ሰራዊት ቡድኖች የወታደራዊ ኮሚቴ አብዮታዊ ኮሚሳሮች ላኩ ። አመጻው ከመጀመሩ በፊት በቀሩት ጥቂት ቀናት ውስጥ በወታደራዊ ቡድኖች ፣ ወፍጮዎችና ፋብሪካዎች ውስጥ ጠንካራ ዝግጅቶች ተደረጉ ። ለአውሮራና ዛራያ-ሶቮቦድይ የጦር መርከቦች ጠንካራ መመሪያዎች ተሰጣቸው ።

በፔትሮግራድ ሶቭየት ስብሰባ ላይ ትሮትስኪ ጉራ በማስመሰል ቦልሼቪክ ፓርቲ ትጥቃዊ አመጽን ለመጀመር ያቀደበትን ቀን ተናገረ ። ከረንስኪ በቅድሚያ በአመጻው ላይ ሽብር እንዳይፈጠር በማሰብ የፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ አመጻው ይጀመራል ከተባለው ቀን ማለትም ሁለተኛው የሶቭየቶች ኮንግረስ አመጻው እንዲጀመር ከወሰነው ቀን ቀደም ብሎ ለመጀመርና ለማካሄድ ወሰነ ።

ጥቅምት 24 ቀን ማለዳ ላይ ከረንስኪ የቦልሼቪኮች ፓርቲ ማእከላዊ ልሳን ራቦቺይፑት (የሠራተኛው ፈለግ) እንዲደመሰስ በማዘዝና ወደ ጽሁፉ አዘጋጆች ወደ ቦልሼቪኮች የማተሚያ ፋብሪካ ብረት ለበስ መኪናዎችን በፍጥነት አሰማራ ። ቢሆንም ከጥዋቱ 4 ሰዓት በጓድ ስታሊን መመሪያ መሰረት ቀይ ዘቦችና አብዮታዊ ወታደሮች ብረት ለበስ መኪናዎችን በመመለስ በማተሚያ ፋብሪካውና ራቦቺይ ፑት አታሚዎች ቢሮ ተጨማሪ ሀይል በማምጣት ሀይላቸውን አጠናከሩ ። ወደ 5 ሰዓት ገደማ ራቦቺይ ፑት ጊዜአዊውን መንግሥት ለመገርሰስ ጥሪ የሚያደርግ ጽሁፍ ይዞ ወጣ ። ከዚሁ ጋር በአመጻው የፓርቲ ማእከል መመሪያ መሠረት የአብዮታዊ ወታደሮች ቀይ ዘቦች ክፍሎች ወደ ስሞልኒይ ገሰገሱ ። አመጻቸው ተጀመረ ።

በጥቅምት 24 ቀን ምሽት ሌኒን ወደ ስሞልኒይ በመሄድ አመጻውን መምራቱን ተያያዘው ። በዚያን እለት ሙሉ ምሽት የጦር ሰራዊቱ አብዮታዊ ቡድኖችና የቀዩ ዘብ ክፍሎች ወደ ስሞልኒይ ማምራታቸውን ቀጠሉ ። ቦልሼቪኮች ወደ ዋና ከተማይቷ በመግሥገስ ጊዜያዊው መንግሥት ራሱን የመሸገበትን የክረምቱን ቤተ መንግሥት ከበቡ ።

ጥቅምት 25 ቀን (ሀዳር 7 በአዲሱ አቆጣጠር) ቀይ ዘቦችና አብዮታዊ ቡድኖች የባቡር ጣቢያውን ፣ ፖስታ ቤቱን ፣ ቴሌግራፍ ቤቱን ፤ የሚኒስቴር መሥሪያ ቤቶችንና መንግሥታዊ ባንኮችን በቁጥጥር ሥር አደረጉ ።
ቅድመ ፓርላማው ተበተነ ።

የፔትሮግራድ ሶቭየት ጠቅላይ መምሪያና የቦልሼቪክ ማዕከላዊ ኮሚቴ ስሞልኒይ ማናቸውም የውጊያ ትዕዛዞች የሚወጡበት የአብዮት ጠቅላይ መምሪያ ሆነ ።

የፔትሮግራድ ሠራተኞች በቦልሼቪክ ፓርቲ መሪነት ሥር በነዚያ ቀናት ውስጥ ምን ዓይነት ደማቅ ትምህርት እንደቀሰሙ አሳዩ ። ሠራዊቱ በቦልሼቪኮች ጠንካራ ተግባር የሠራዊቱ አብዮታዊ ቡድኖች ከአመጸው በሚገባ ተዘጋጁ ፤ በሙሉ ፈቃደኝነት በጀግንነት ተዋጉ ። የባሕር ሀይሉም ከሠራዊቱ ወደ ኋላ አልተንዘዘም ። የቦልሼቪኮች ጠንካራ ምሽግ የሆነው ክሮንስታድ የጊዜያዊውን መንግሥት ሥልጣን ለመቀበል አሻፈረኝ ካለ አመታት አልፈውታል ። አውሮራ የተሰኘችው መርከብ የጠመንጃውን አፈሙዝ ወደ ክረምቱ ቤተ መንግሥት አዞረችና ጥቅምት 25 ቀን አዲሱን ዘመን ፣ የታላቁን ሶሻሊስት አብዮት ዘመን የሚያበስር ነጐድጓድ አሰማች ።

ጥቅምት 25 ቀን ቦልሼቪኮች የቡርዧው ጊዜያዊ መንግሥት ከሥልጣን መውረዱንና መንግሥታዊ ሥልጣን በሶቭየቶች እጅ መግባቱን በማወጅ «ለሩሲያ ነዋሪዎች » የተሰኘ መግለጫ አወጡ ።

ጊዜያዊው መንግሥት በክረምቱ ቤተ መንግሥት ውስጥ በካዴቶችና በተወርዋሪ ባታሊዮኖች እየተጠበቀ መሸገ ። ጥቅምት 25 ቀን ምሽት ላይ አብዮታዊ ሠራተኞች ፣ ወታደሮችና መርከበኞች የክረምቱን ቤተ መንግሥት በመውረር ጊዜያዊ መንግሥቱን በቁጥጥር ሥር አዋሉ ።

ሁለተኛው የመላው ሩስያ ሶቭየቶች የፔትሮግራዱ ትጥቃዊ አመፅ በድል አሸበረቀ ። ኮንግረስ ከምሽቱ 4 ሰዓት ከ45 ደቂቃ በስሞልንይ ተከፈተ ። ጥቅምት 25 ቀን 1917 ዓ. ም. የፔትሮ ግራድ አመጽ በድል ሲያሸበርቅ በዋና ከተማይቱ ያለው ስልጣን በፔትሮ ግራድ ሶቪየቶች እጅ ገባ ።

በኮንግረሱ ላይ ቦልሼቪኮች የምልአተ ጉባኤውን ድጋፍ አገኙ ። ቀን ሲከዳ መሬት ያዳልጣል እንዲሉ ነውና ሜንሼቪኮች ፤ ባንዲስቶችና ቀኝ ክንፍ ሶሻሊስት አብዮተኞች ቀኑ እንደከዳቸው ተገንዝበው በሥራው ውስጥ አንዳችም ተሳትፎ አናደርግም በማለት ኮንግረሱን ጥለው ወጡ። በሶቭየቶች ኮንግረስ ላይ ተነቦ በነበረው መግለጫቸው የጥቅምቱ አብዮት « ወታደራዊ አድማ » ነው ሲሉ ተቃወሙት ። ኮንግረሱም ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮተኞችን አወገዘና ከሀዲዎች ስብሰባውን ጥለው በመውጣታቸው ኮንግረሱ ሀቀኛ የሠራተኞችና የወታደሮች ተወካዮች ኮንግረስ ለመሆን መብቃቱን በመግለጽ የነርሱ ስብሰባውን ጥሎ መውጣት ያለአንዳች ጸጸት በደስታ ተቀብሎታል ።

ኮንግረሱ ስልጣን በሶቭየቶች እጅ መግባቱንም ሲገልጽ ፡-
« በምልአተ ሠራተኞች ፣ ወታደሮችና ገበሬዎች ፍላጐት በመደገፍ በፔትሮግራድ ሠራተኞችና የጦር ሰፈሮች በተገኘው ድል አድራጊ አመጽ በመደገፍ ፣ ኮንግረሱ ስልጣኑን በእጁ አስገብቷል ። » ሲል የሶቭየት ሁለተኛው ኮንግረስ አዋጅ በንባብ ታወጀ ።



ጥቅምት 26 ቀን 1917 ዓ ም ምሽት ላይ የሶቭየቶች ሁለተኛው ኮንግረስ ስለሰላም የወጣውን ድንጋጌ አጸደቀ ። ኮንግረሱ ከሶስት ወራት ለማያንሱ ጊዜያት የሰላም ስምምነቱን ለማመቻቸት ለጠብ ወዳድ አገሮች ጦርነት የማቆሙ ስምምነት በአስቸኳይ እንዲደረግ በመደጋገም ጥሪ አደረገ ። ከዚሁም ጋር በማያያዝ ኮንግረሱ የሠራተኞች መደባዊ ንቃተ ህሊና ከፍ ብሎ ለሚገኘው እጅግ በጣም ለተራመዱትና በአሁኑ ጦርነት ውስጥ ከፍተኛ ተሳትፎ ለሚያደርጉት ለሦስቱ አገሮች ለታላቋ ብሪታኒያ ፤ ለፈረንሣይና ለጀርመን ጥሪ አደረገ ። በነዚህ ሀገሮች ውስጥ ላሉት ሠራተኞች ጥሪ ያደረገው « ለሰላም ባለው ዓላማና ከዚሁም ጋር ሠራተኛውንና ምዝብሩን ሰፊ ሕዝብ ከማናቸውም ዓይነት ብዝበዛና ባርነት ነጻ ለማውጣት ዓላማው የተሳካ ውጤት እንዲያገኝ » ለመርዳት ነው ።

የዚያኑ እለት ማታ የሶቭየቶች ሁለተኛው ኮንግረስ « የመሬት ባለቤትነት ያለምንም ካሳ ተወስዷል» ተብሎ የታወጀውን የመሬት አዋጅ አጸደቀ ። ይህንን የገጠር መሬት አዋጅ የመጽደቅ መሠረቱ በገበሬው ውክልና ማለትም ከተለያዩ አካባቢዎች በተውጣጡ 242 የገበሬዎች ውክልና ላይ ነው ። በዚህም ውክልና መሠረት የግል ባለቤትነት ለዘላለም እንዲወገድና የመሬት ከበርቴዎች በዛር ቤተሰብና በአድባራት ቁጥጥር ሥር የነበሩ መሬቶች በነጻ እንዲጠቀሙበት ለብዙሀን ጉስቋሎች ተሰጠ ።

በዚህም ድንጋጌ መሠረት የጥቅምቱ ሶሻሊስት አብዮት ቀደም ሲል የመሬት ከበርቴዎች ፣ የቡርዧዎች ፣ የገዳማትና የአድባራት ይዞታ የነበሩ ከ150,000,000 ዲሲያቲኖች በላይ የሆነ መሬት (ከ400,000,000 ጋሻ በላይ መሆኑ ነው ) ለገበሬዎች አስገኝቷል ።

ከዚህም በላይ ገበሬዎች በዓመት 500,000,000 የወርቅ ሩብሎች ያህል የሚገመተውን ለመሬት ከበርቴዎች ከሚከፍሉት ኪራይ ተላቀቁ ።

የማእድን ሀብቶች (ዘይት ፣ የብረት ከሠል ፣ የብረት አፈር ወዘተ . . .) ደኖችና ጅረቶች የሕዝቡ ንብረት ሆኑ ።

በመጨረሻም የመላው ሩስያ ሶቭየቶች ሁለተኛው ኮንግረስ ሶቭየቶችን ያቀፈ የመጀመሪያውን የሶቭየት መንግሥት መሠረተ—የህዝባዊ ኮሚቴዎች ምክር ቤት ። ሌኒን የሕዝባዊ ኮሚሳሮች ምክር ቤት የመጀመሪያው ሊቀመንበር በመሆን ተመረጠ ።

የሶቭየቶች ሁለተኛው ታሪካዊ ኮንግረስ ተግባር በዚህ ተጠቃለለ ።
የኮንግረሱ ተወካዮች በፔትሮግራድ የተገኘውን የሶቭየቶችን የድል ዜናዎች ለማብሰር በመላው ሀገሪቱ ተሰራጩ ።

ሶቭየቶች በሁሉም ቦታ በአንድ ጊዜ ስልጣን አልያዙም ። በፔትሮግራድ የሶቭየቶች መንግሥት ሲመሰረት በሞስኮ ውስጥ ለአያሌ ቀናት በየመንገዱ የከረረና ጠንካራ ጦርነት ቀጠለ ። ሥልጣን በሞስኮ ሶቭየቶች እጅ እንዳይገባ ለማድረግ ጸረ-አብዮተኞች የሜንሼቪኮችና የሶሻሊ

ስት አብዮተኞች ፓርቲዎች ከነጭ ዘቦችና ካዴቶች ጋር በመተባበር ሠራተኞችንና ወታደሮችን በመቃወም ትጥቃዊ ሴራ ማካሄድ ጀመሩ ። በሞስኮ ውስጥ የነዚህን ጸረ-አብዮተኞች ሴራ ለመደርመስና የሶቭየቶችን ስልጣን ለመመስረት እያሌ ቀናት ፈጅቷል ።

በራሷ በፔትሮግራድና በአብዛኛው አውራጃዎችዋ እንኳ ጸረ-አብዮተኞች ገና አብዮቱ ድል በተጐናጸፈ የመጀመሪያው እለት ነበር የሶቭየቶችን ሥልጣን ለመገልበጥ ታላቅ ሴራ መጠንሰስ የጀመሩት ። ሕዳር 10 ቀን 1917 ዓ. ም. ከፔትሮግራድ የአመጽ ፍላፃ ለማምለጥ ወደ ሰሜናዊ ግንባር የፈረጠጠው ከረንስኪይ እያሌ የኮዛክ ቡድኖችን አሰባሰበና በካራስኖቭ የሚመራ ጦር ፔትሮግራድን እንዲወጋ ላከ ። ህዳር 11 ቀን 1917 ዓ ም ራሱን « የአባት አገርና የአብዮቱ ነጻ አውጪ ኮሚቴ » ብሎ የሚጠራው የጸረ-አብዮተኞች ድርጅት በሶሻሊስት አብዮታውያን እየተመራ በፔትሮግራድ ውስጥ የካዴቶች አመጽ ቀሰቀሰ ። ይህም በመርከበኞችና በቀይ ዘቦች ያለ እንዳች ችግር ተደመሰሰና ኅዳር 13 ቀን ጀኔራል ክራስኖቭ በፑልኩቭ ኩረብታዎች አጠገብ ድል ተመታ ። ሌኒን የጥቅምቱን አመጽ እንደመራው ሁሉ አሁንም ጸረ-ሶቭየት የሆኑ አመጾዎችን ለመደምሰስ በቀጥታ በመሳተፍ መራ ። የማያወላውል ቆራጥነትና በድል ላይ ያለው ጽኑ እምነቱ ሰፊውን ሕዝብ በሚገባ ቀሰቀሰው ። ጠላት ተደመሰሰ ። ክራስኖቭ ወደ እስር ተወሰደና « የእምነት ቃሉን » ሲሰጥ የሶቭየትን ሥልጣን ደግሞ ላለመቃወም ቃል ገባ ። « በእምነት ቃሉም » መሠረት ከእስር ተለቀቀ ። ይሁን እንጂ ከተለቀቀም በኋላም ጀኔራሉ የገባውን ቃል አልጠበቀም ። ከረንስኪይ የሴት ቀሚስ ለብሶ እራሱን በመሸፈን «ወደ አልታወቀ አቅጣጫ ለመሰወር» ተገደደ ።

ሞጊሌቭ በሚገኘው የጦር ሰራዊቱ ጠቅላይ መምሪያ ውስጥም እንዲሁ የጦር ሀይሉ ዋና አዛዥ የሆነው ጀኔራል ዱክሆኒን ለማመጽ ጥረት አደረገ ። ከጀርመን የጦር አበጋዞች ጋር ጦርነት ለማቆም ስምምነት እንዲያደርግ የሶቭየት መንግሥት ሲያዘው አሻፈረኝ ሲል ተቃወመ ። ይሁን እንጂ በሶቭየቶች መንግሥት ትእዛዝ መሠረት ወዲያውኑ ከሥልጣን ተወገደ ። የጸረ-አብዮተኞች ጠቅላይ መምሪያ ተከፋፈለና ዱክሆኒን ራሱ እርሱን በመቃወም በተነሱ ወታደሮች ተገደለ ።

ጥቂት በፓርቲው ውስጥ ያሉ አደገኛ አድርባዮች—ካሜኔቭ፣ ዚኖቪየቭ ፣ ራይኩቭ፣ ሻላያ፣ ፑሌኮቭና ሌሎችም የሶቭየትን ስልጣን ለመቃወም ተሯሯጡ ። የጥቅምቱ አመጽ ገርስሶ የጣላቸውን ሜንሼቪኮችንና ሶሻሊስት አብዮተኞችን የሚያዳምር «የመላው ሶሻሊስት መንግሥት» እንዲመሠረት ጠየቁ ። ህዳር 15 ቀን 1917 ዓ ም የቦልሼቪክ ፓርቲ ማእከላዊ ኮሚቴ ከነዚህ ጸረ-አብዮተኞች ፓርቲዎች ጋር የሚደረገውን ስምምነት በመቃወም ውሳኔ በማሣለፍ ካሜኔቭና ዚኖቭየቭ አብዮቱን ለማዳከም ቆርጠው የተነሱ መሆናቸውን አሳወቀ ። ህዳር 17 ቀን ካሜኔቭ ዚኖ



ቭየቭ ራይኮቭና ሚልዩቲን የፓርቲውን ፖሊሲ በመቃወም ከማእከላዊ ኮሚቴው «በፈቃዳቸው» መልቀቃቸውን ገለጹ ። በዚሁ እለት ማለትም ህዳር 17 ቀን ኖጊን በራሱና በራይኩቭ በቪ. ሚሊዩቲን ፣ በቴዎዶሮቪች ፣ በኤ. ሻያፕኒኩቭ ፣ በዲ. ራያዛኖቭ በዩኔሬቭና በላሪን የሕዝባዊ ኮሚሳሮች ምክር ቤት አባላት ስም የፓርቲውን ማእከላዊ ኮሚቴ ፖሊሲ እንደማይቀበሉና ከሕዝባዊ ኮሚሳሮች ምክር ቤት « በፈቃዳቸው » መልቀቃቸውን አሳወቁ ። የነዚህ እፍኝ የማይሞሉ የፈሪዎች ውሳኔ በጥቅምቱ አብዮት ጠላቶች ዘንድ ታላቅ ኢዮቤልዩ በአል ሆነ ። ቡርዧዎችና ቅኝ እጆቻቸው የቦልሼቪክ ፓርቲ « መንበታኮቱን » እና በጥቂት ጊዜ ውስጥ ውድቀቱ በተግባር እንደሚታይ በማመልከት ተንኮል በተሞላበት ደስታ አናፉ ። ነገር ግን የነዚህ እፍኝ የማይሞሉ ከሀዲዎች ኢ-ቦልሼቪክ ተግባር ፓርቲውን ቅንጣትም ታህል አላብረከረከውም ። የፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ ንቀት በተሞላበት መንገድ የአብዮቱ ከሀዲዎች ፣ የቡርዧው ግብረ አበሮች ብሎ በመቀጸል (በመጥራት) መደበኛ ተግባሩን ማከናወን ጀመረ።

የ « ግራ » ሶሻሊስት አብዮታውያን ደግሞ ቦልሼቪክን በሚገባ ያቀፈውን ገበሬ ድጋፍ ለማግኘት ባላቸው ምኞት ከኋላዎቹ ጋር ላለመጣላት ጊዜያዊ የሕብረት ግንባር ለመመስረት ወሰኑ ። በህዳር ወር 1917 ዓ ም የገበሬ ሶቭየቶች ኮንግረስ ተደርጐ የጥቅምቱ ሶሻሊስት አብዮት ያስገኘውን ድሎች መርምሮ የሶቭየት መንግሥት ያሳለፈውን ውሳኔ በሚገባ መደገፉን ገለጸ ። ከ « ግራ » ሶሻሊስት አብዮታዊያን ስምምነት ተደርጐ ነበርና እያሌ አባልተኞቻቸው በሕዝባዊ ኮሚሳሮች ምክር ቤት ውስጥ ቦታ ተሰጣቸው ። እነዚህም ኮሌጋዬቭ፣ ስፔሪዶኖቫ ፣ ፕሬሽያንና ስቴንበርግ ቢሆኑም ቅሉ ይህ ስምምነት በብሬስት ሊቶቭስኩ የሰላም ስምምነት እስከተፈረመበትና የደሀ ገበሬዎች ኮሚቴ እስከተመሰረተበት ጊዜያት ድረስ ብቻ ተከብሮ ቆየ ። በገበሬዎች መሀከል ሥር የሰደደ አለመግባባት ሲፈጠርና ፣ « ግራ » ሶሻሊስት አብዮታውያን ፣ የኩላኮችን ጥቅም ሲያንጸባርቁ ፣ ቦልሼቪኮችን በመቃወም ሴራ ሲጀምሩ በሶቭየት መንግሥት ተደመሰሱ ።

ከጥቅምት ወር 1917 ዓ ም እስከ የካቲት ወር 1918 ዓ. ም. መሀከል ባሉት ጊዜያት ውስጥ የሶቭየት አብዮት ሌኒን ይህንኑ አስመልክቶ እንዳለው የሶቭየቶች ስልጣን « ድል አድራጊው ጉዞ » በሰፊው የሀገሪቱ ግዛቶች ውስጥ በቀለጠፈ ፍጥነት ተናኘ ።

ታላቁ የጥቅምቱ አብዮት ድል ተጐናጸፈ ።

የሩስያ ሶሻሊስት አብዮት ከሌላው ጋር ሲነጻጸር በቀላሉ የተገኘ ድል የሚያደርጉት እያሌ ምክንያቶች አሉ ። የሚከተሉት ዋነኛ ምክንያቶች ሊጠቀሱ ይችላሉ ።

1. የጥቅምቱ አብዮት የገጠሙት ጠላቶች ከሌላው ጋር ሲነጻጸር እንደ ሩስያው ቡርዧ ድርጅታዊ ብቃት ያልነበረው ፣ ፖለቲካዊ ልምድ

ያልነበረው ሲሆን ፤ በምጣኔ-ሀብቱም መስክ እጅግ ደካማና በመንግሥታት ውሎች ላይ ጥገኛ የሆነ ነበር ። የሩስያ ቡርዧ በፖለቲካዊ የራስ መተማመን ብቃት የሌለውና ከተፈጠረው ሁኔታ ለመውጣት መንገድ ለመሻት የማይችል ነበር ። የፈረንሳዩን ቡርዧ ልምድ ለምሳሌ በሰፊ ደረጃ ፖለቲካዊ መዋሀድና ፖለቲካዊ ሞሳ(ትሪክ) ወይም እንደ እንግሊዙ ቡርዧ መሠረት እርቅ የማቀድ ትምህርት የለውም ። ቢኖረውም አሁን ከዛሩ ጋር መግባባት ላይ ለመድረስ እየጣረ ነበር ። ገና አሁን ማለትም ዛሩ በየካቲቱ አብዮት ከተፈነገለና ቡርዧው እራሱ በትረ-መንግሥቱን ሲጨብጥ ለማናቸውም አስፈላጊ ጉዳዮች እጅግ የተጠላውን የዛሩን ፖሊሲ ከማራመድ ሌላ የተሻለ ሊያስብ አይችልም ነበር ። ጦርነቱ ከሀገሪቱ አቅም በላይ በመሆኑና ሕዝቡና ሕዝቡን ጦር ሰራዊቱ ፍጹም ወደተዳከመ ሁኔታ ቢያወርዳቸውም እንደዛሩ ሁሉ እሱም « ጦርነት እስከዘላቂው ድል » ለማለት ከዛሩ ፖሊሲ ጉን ቆመ ። ገበሬው በመሬት እጦትና የመሬት ከበርቴዎች በጫኑበት ቀንበር ያለቅጥ ቢማቅቅም እንደዛሩ ሁሉ እሱም ከሁሉም ነገር በፊት የመሬት ከበርቴዎችን ንብረት ለማስከበር ቆመ ። በሰራተኛውም ላይ ያለው ፖሊሲ የፋብሪካ ባለቤቶች በሠራተኛው መደብ ላይ የተበተቡትን የባርነት ሰንሰለት ለመጠበቅና ለማጠናከር በከፍተኛ ደረጃ በሚያደርገው ጥረት ብቻ ሳይሆን ሠራተኛውን በጅምላ ከፋብሪካ በማባረር ተግባሩም ጥም እንደሚታየው በሠራተኛው መደብ ላይ ያለው ጥላቻ ከዛሩም በላይ የከፋ ነበር ።

ሕዝቡ በዛሩና በቡርዧው ፖሊሲ መሀከል መሠረታዊ የሆነ ልዩነት አለመኖሩን ተመልክቶና በዛሩ ላይ የነበረውን ጥላቻ በቡርዧው ጊዜያዊ መንግሥት ላይ ማሳደሩ የሚያስገርም ሊሆን አይችልም ።

አጉብዳጆቹ (ታራቂዎቹ) ሶሻሊስት አብዮታውያንና ሜንሼቪክ ፓርቲዎች በህዝቡ ላይ ጥቂትም ብትሆን ተጽእኖ እስካሳደሩ ድረስ ቡርዧዎች እነርሱን ከለላ አድርገው ለመጠቀም ችለዋልና ስልጣናቸውን ጠበቁ ። ይሁን እንጂ ሜንሼቪኮችና ሶሻሊስት አብዮታውያን የኢምፔሪያሊስት ቡርዧው ወኪሎች መሆናቸውን በገሀድ ካጋለጡ በኋላ በህዝቡ መሀከል የነበራቸውን ተቀባይነት አሟጠጡ ። በመሆኑም ጊዜያዊው መንግሥት ያለአንዳች ድጋፍ እራቁቱን ቀረ ።

2/ የጥቅምቱ አብዮት እጅግ አብዮታዊ በሆነው የሩስያ ሠራተኛ መደብ የተመራ ነበር ። ወርቅ በእሳት ተፈትኖ እንደሚወጣ ሁሉ ይህም የሠራተኛ መደብ በመደባዊ ጦርነቱ ተፈትኖ የወጣ መደብ ነው ። የሩስያ ሠራተኛ መደብ በአጭር ጊዜ ውስጥ በሁለት አብዮቶች ያለፈና በሶስተኛው አብዮት ዋዜማ ለሠላም ፣ ለመሬት ለአርነትና ለሶሻሊዝም በሚያደረገው ትግል ውስጥ የሕዝቡ ሀቀኛ መሪ መሆኑን በሚገባ ያረጋገጠ ነው ። አብዮቱ የሩስያን ሠራተኛ መደብ መሪነት ባያገኝ ኖሮ ፤ ይህንን የሕዝቡን ሙሉ እምነት ያገኘ ሀቀኛ መሪ ባያገኝ ኖሮ ፣ በሠራተኛውና በገበሬው



መሀከል ሕብረት ባልተፈጠረም ነበርና እንዲህ ያለው ሕብረት ካልተፈጠረ የጥቅምቱን አብዮት ድል ማድረጉ የሚቻል አልነበረም ።

3/ የሩስያ ሠራተኛ መደብ የገበሬው ሕብረተሰብ አብዛኛው ክፍል ካሉበት ከድሀው ገበሬ ጋር ህብረት ፈጥሮአል ። የስምንቱ ወራት የአብዮት ልምድ ማለትም ከአያሌ አስር ዓመታት « ጤናማ » እድገት ጋር ሊወዳደር የሚችል — ሰፊውን ሠራተኛ ገበሬ የሚመለከት ነውና ፋይዳ ቢስ ሆኖ አልቀረም ። በነዚህ ወቅቶች በሩስያ ውስጥ የሚገኙ የሁሉም ፓርቲዎች ምንነት በተግባር ለመፈተን መልካም አጋጣሚ አግኝቷልና ሕገመንግሥታዊ ዲሞክራቶች ወይም ሶሻሊስት አብዮታውያንና ሜንሼቪኮች ከመሬት ከበርቴዎች ጋር ጠብም እንደሌላቸው ወይም ለገበሬው ፍላጐት ራሳቸውን አለመስዋታቸውን በሚገባ ተገንዝበውታል ። ይህ ማለት በሩስያ ውስጥ በማናቸውም መንገድ ከመሬት ከበርቴዎች ጋር አንዳችም ግንኙነት የሌለውና የገበሬውን ፍላጐት ለማሟላትና የመሬት ከበርቴዎችን ለመደምሰስ በሚገባ የተዘጋጀ አንድ ፓርቲ ብቻ ነበር . . . ቦልሼቪክ ፓርቲ ። ይህ ለወዝአደሩና ለደሀው ገበሬ ሕብረት ጠንካራ መሠረት ሆነ ። በወዝአደሩና በደሀው ገበሬ መሀከል የተፈጠረው ሕብረት ለረጅም ጊዜ ሲዋልል ለነበረውና በጥቅምቱ እመጽ ዋዜማ ላይ በሙሉ ልቡ ወደ አብዮቱ ያዘነበለውና ከደሀ ገበሬው ጋር ሀይሉን ላስተባበረው መሀከለኛ ገበሬ ተግባር ወሳኝ ሆነ ።

ያለዚህ ህብረት — በወዝአደሩና በገበሬው መካከል — የጥቅምቱ አብዮት ለድል አይበቃም ነበር ማለት ይቻላል ።

4/ የሠራተኛው መደብ እንደ ቦልሼቪክ ፓርቲ ባለ ፤ በፖለቲካዊ ጦርነት ውስጥ ተወልዶ ባደገ ፓርቲ የተመራ ነበር ። በወሳኙ ፍልሚያ ውስጥ ህዝቡን ለመምራት ብቁ ጀግናና ለዘላቂው ግቡ በሚያደርገው ጉዞ ላይ የሚያጋጥሙትን መሰናክሎች እየመነገለ መንገዱን በመጥረግ ጠንቃቃ የመሪነት ብቃት ያለው ፣ እንደ ቦልሼቪክ ያለ ፓርቲ ብቻ ነው ። ስለሆነም ሁዳዶችን ለመያዝ ገበሬዎች የሚያደርጉት ዲሞክራሲያዊ እንቅስቃሴ ፣ ጭቁን ብሔረሰቦች ለብሔራዊ አርነታቸውና ለብሔራዊ እኩልነታቸው የሚያደርጉት እንቅስቃሴዎችና ቡርዧውን ገርስሶ የወዝአደሩን አምባገነንነት ለማስፈን ወዝአደሮች የሚያደርጉት ሶሻሊስት አብዮት ፣ የመሳሰሉ የበዙ አብዮታዊ እንቅስቃሴዎችን ለሰላም ወደሚደረግ ዲሞክራሲያዊ እንቅስቃሴ ፣ የጋራ ወደሆነ አብዮታዊ ቁጣ ፤ ጥበብ በተሞላበት መንገድ ለማዋሀድ ችሏል ።

በማያጠራጥር ሁኔታ የነዚህ አያሌ አብዮታዊ ፈለጐች ወደ አንድ የጋራ ወደሆነ ጠንካራ አብዮታዊ ማእበል ሲዋሀዱ ለሩስያው ካፒታሊዝም ሞት ወሳኝ ይሆናሉ ።

5/ የጥቅምቱ አብዮት የተካሄደው የኢምፔሪያሊስት ጦርነት በከፍተኛ ደረጃ በተፋፋመበት ወቅት ነበር ። የዋነኛው ቡርዧ መንግሥት ወደ ሁለት

ጠላት ካምፖች በተከፈለበት ጊዜና ሁለቱም ካምፖች እርስ በርሳቸው በጦርነት በተጠመዱበት ወቅት ፤ እንዱ የሌላውን ጥንካሬ በሚንቅበት ጊዜ « በሩስያ ጉዳዮች » ውስጥ በቀጥታ ጣልቃ ለመግባትና የጥቅምቱን አብዮት ወዲያውኑ ለመቃወም አልቻሉም ።

ይህ በማያጠራጥር ሁኔታ ለጥቅምቱ ሶሻሊስት አብዮት ድል መምታት ታላቅ አስተዋጽኦ አበርክቷል ።

7. የሶቭየትን ኃይል ለማጠናከር የቦልሼቪክ ፓርቲ ያደረገው ትግል ፤ የብሬስት ሊቶቭስክ ሰላም ሰባተኛው የፓርቲ ኮንግረስ ፡-

የሶቭየትን ስልጣን ማጠናከር እንዲቻል አሮጌው የቡርዧው መንግሥታዊ መኪና ተንኰታኩኰተ ተደምስሶ በአዲስ ፣ በሶቭየት መንግሥታዊ መኪና መተካት አለበት ። ከዚህም በላይ ሕብረተሰቡን በንብረትና በብሔራዊ የጨቋኝ መንግሥት የሚከፋፍሉ ርዝራዦችን ማውደሙ ፣ ቤተ ክህነት ያላትን ክብር ማስቀረት ፣ የጸረ-አብዮተኞችን ፕሬስና ማናቸውንም ዓይነት የጸረ-አብዮተኞችን ድር ጅቶች ፣ ሀጋዊና ህገወጥ ፣ መደምሰስና የቡርዧውን ሸንጎ መበተን እጅግ አስፈላጊ ነበር ። መሬት ውርስ ከሆነ በኋላ ሁሉም ታላላቅ ኢንዱስትሪዎች በመንግሥቱ ቁጥጥር ሥር መሆን አለባቸው ።እንዲሁም በመጨረሻ የጦርነቱ ሁኔታ ማብቃት አለበት ፣ የጦርነቱ መቀጠል ከማናቸውም ነገር ይልቅ የሶቭየት ስልጣን እንዳይጠናከር ከፍተኛ መሰናከል ሆኖታል ።

እነዚህ ሁሉ ከ1917 ዓ. ም. መጨረሻ እስከ 1918 ዓ. ም. አጋማሽ ባሉት አጭር ወራት ውስጥ የተወሰዱ እርምጃዎች ነበሩ ።

በሶሻሊስት አብዮታውያንና በሜንሼቪኮች ይመሩ የነበሩ ፣ በድሮ ሚኒስቴር መስሪያ ቤቶች ውስጥ የሚሰሩ ባለስልጣኖችን አሻጥር በሚገባ በመምታት ለመቋቋም ተችሏል ። እነዚህ የድሮ ሚኒስቴር መስሪያ ቤቶች ተወግደው በሶቭየት የአስተዳደር መኪናና በተገቢው የራሱ ኮሚሳር ጽህፈት ቤቶች ተተኩ ። የብሔራዊ ምጣኔ—ሀብት ከፍተኛ ምክር ቤት የሀገሪቷን ኢንዱስትሪዎች እንዲያስተዳድር ተቋቋመ ። ጸረ-አብዮተኞችንና አሻጥሮቻቸውን ለመዋጋት የመላው ሩስያ ልዩ ኮሚሽን ተመሰረተና ኤፍ ዲዘረዝንስኪይ ይህንን ኮሚሽን እንዲመራው ተደረገ ። የቀዩ ጦር ሠራዊትና የባህር ሀይል መመስረቱ በይፋ ታወጀ ። ከጥቅምቱ አብዮት ቀደም ብሎ የተደረገው ምርጫና ሁለተኛው የሶቭየቶች ኮንግረስ ስለ ሰላም ፣ መሬትና ስልጣን ለሶቭየቶች እንዲሰጥ ያሳለፈውን ውሳኔ ለመቀበል አሻፈረኝ ብሎ የነበረው ሸንጎ ተበተነ ።

የፊውዳሊዝም ፣ የግል ንብረት ሥርዓትና ርዝራዦችን በማናቸውም የማኅበራዊ ኑሮ መስኮች ውስጥ የሚታዩትን አለመመጣጠኖች ለማስቀረት እንዲቻል የግል ንብረትን የሚያስወግድ በብሔረሰብ ወይም በሀይ



ማኖት ላይ የተመሠረቱ ቁጥጥሮችን የሚያስቀሩ ፣ ቤተክህነትን ከመንግሥት ፣ ትምህርት ቤቶችን ከቤተክህነት የሚለዩ ፣ የሴቶችን እኩልነትና በሩስያ ውስጥ የሚገኙ የማናቸውም ብሔረሰቦችን እኩልነት የሚያረጋግጡ ድንጋጌዎች ወጡ ።

« የሩስያ ሕዝቦች መብቶች አዋጅ » በመባል የሚታወቀው ይህ እንደ ህግ የወጣው የሶቭየት መንግሥት ልዩ አዋጅ የሩስያን ሕዝብ እድገትና ፍጹም እኩልነት እንዳያሰናክል የተሰጠው መብት ነው ።

የቡርዧውን ምጣኔ—ሀብታዊ ሀይል ለማመንመን ፣ አዲስ ፣ የሶቭየት ብሔራዊ ምጣኔ—ሀብት ለመመስረት እንዲቻል ፣ በመጀመሪያ ደረጃ ፣ አዲስ የሶቭየት ኢንዱስትሪ ለመመስረት ፣ ባንክ ፣ የባቡር መስመር ፣ የውጪ ንግድ ፣ የንግድ መርከብና በማናቸውም የኢንዱስትሪ መስኮች ያሉ ማናቸውም ታላላቅ ተቋሞች ፣ የድንጋይ ከሰል ፤ ዘይት ፣ ኬሚካሎች ፣ የመኪና ግንባታ ፤ ጨርቃ ጨርቅ ፣ ስኳር ወዘተ . . . ተወረሰ ።

በገንዘብ በኩል ሀገራችንን ከባእዳን (ከውጪ) ካፒታሊስቶች ተጽእኖ ነጻ እንድትወጣ ከነርሱ ብዝበዛ እንድትላቀቅ የሩስያው ዛርና ጊዜያዊው መንግሥት ከውጪ የተዋዋሉት የብድር ገንዘብ ተሻረ ። የሀገራችን ሕዝቦች የወረራ ጦርነቱ እንዲቀጥል ሲባል የተዘፈቁበትንና ሀገራቸውን በባእዳን ወረት ሥር የጣላትን እዳ አንከፍልም ሲሉ ተቃወሙ ።

እነዚህና እነዚህን የመሳሰሉ እርምጃዎች የቡርዧውን ፣ የመሬት ከበርቴውን ፣ የአድሀሪ ባለስልጣኖችና ጸረ-አብዮታውያን ፓርቲዎችን ሥረ መሰረት ሸረሸሩና በሀገሪቱ ውስጥ የሶቭየትን መንግሥት አቋም በጣም አጠናከሩ ።

ነገር ግን የሶቭየት መንግሥት አቋም ሩስያ ከጀርመንና ከአውስትሪያ ጋር ጦርነት በማካሄድ ሁኔታ ውስጥ እስካለችበት ጊዜ ድረስ ጽኑ ሰላም ይሰፍናል ብሎ አያምንም ነበር ። የሶቭየትን ስልጣን ለዘለቄታው ለማጠናከር እንዲቻል ጦርነቱን ማብቃት አለበት ። ስለዚህም ነው ፓርቲው የጥቅምቱ አብዮት ድል ከተገኘበት ጊዜ ጀምሮ ለሰላም የሚደረገውን ትግል ያቀጣጠለው ።

የሶቭየት መንግሥት « ለሁሉም ጠብ ወዳድ ሕዝቦችና ለመንግስቶቻቸው እውነተኛ ፣ ዲሞክራሲያዊ ሰላም ፣ አሁኑኑ ድርድር እንዲጀመሩ » ጥሪ አደረገ ። ነገር ግን « የቃል ኪዳን አገሮች » ከታላቋ ብሪታኒያና ፈረንሳይ— የሶቭየት መንግሥት ያቀረበውን ይህንን ሀሳብ አልተቀበሉትም ። በዚህ የተቃውሞ አመለካከት የሶቭየት መንግሥት ፣ የሶቭየቶችን ፍላጐት ለማሟላት ከጀርመንና ከአውስትሪያ ጋር ለመደራደር ወሰነ ።

ድርድሩም ታህሳስ 3 ቀን በብሬስት ሌቶቭስክ ተጀመረ ። ታህሳስ 5 ቀን ጦርነት የማቆም ስምምነት ተፈረመ ።

ድርድሩ የተደረገው ሀገሪቷ በምጣኔ—ሀብታዊ ቀውስ ውስጥ ባለችበት ጊዜ ፣ በሁሉም ዘንድ በጦርነት መዳከም ባለበት ጊዜ ፣ የኛ ሠራዊት ምሽጐቻቸውን ጥለው በሄዱበትና ግንባሩ በተናደበት ጊዜ ነበር ። በድርድሩ ሂደት ውስጥ የጀርመን ኢምፔሪያሊስቶች ከቀድሞው የዛር ግዛት ከፍተኛውን ሥፍራ ለመያዝ ተነሱ ። ፖላንድን ለመመለስ፣ኡክሬኒያና የባልቲክ አገሮችን በጀርመን ጥገኛነት ሥር ለማዋል እንደነበረ ግልጽ ነበር ።

እንዲህ ባለው ሁኔታ ውስጥ ጦርነቱን መቀጠል ማለት አዲስ የተወሰደውን ፣ እንቦቃቅላውን የሶቭየት መንግሥት ልክ ሕልውና እንደማሳጣት ይሆናል ። ሠራተኛው መደብና ገበሬው እጅግ አደገኛ ከሆነው የወቅቱ ወረራ — የጀርመን ኢምፔሪያሊዝም — በማፈግፈግ የሶቭየትን ሥልጣን ለማጠናከርና አዲስ የጦር ሠራዊት ፣ ሀገሪቷን ከገጠማት ጠላት ሊከላከል የሚችለውን ቀዩን ሠራዊት ለመመስረት ፋታ ለማግኘት ከባድ የሰላም ድርድር የማድረግ አስፈላጊነት ከፊቱ ገጥሞታል።

መላው ጸረ-አብዮት ሀይላት ከሜንሼቪክና ከሶሻሊስት አብዮታውያን ጀምሮ እስከ እጅግ አደገኛ የሆኑ ነጭ ዘቦች ድረስ ፣ የሠላሙን ውሳኔ በመቃወም ስሜት የተሞላበት ዘመቻ አካሄዱ። ፖሊሲያቸው ደግሞ ግልጽ ነበር ። ይኸውም የሰላሙን ድርድር ማፍረሥ ፣ ጀርመን በወረራው እንድትገፋበት ማነሳሳቱና ስለሆነም አሁንም ገና ደካማ በሆነው የሶቭየት ስልጣን ላይ አደጋ ለማድረስና ሰራተኞችና ገበሬዎች ያገኙትን ድል ለማጨናገፍ ነበር ።

በዚህ አደገኛ ዘዴ የቃል ኪዳን ጓደኞቻቸው ትሮትስኪና ግብረ አበሩ ቡካህሪን ሲሆን ። የኋለኛው ከራዴክና ያታቭ ጋር በመሆን « ግራ ኰሚኒዝም » በሚል ሽፋን ራሱን የሸፈነ ነገር ግን የፓርቲው ቀንደኛ ጠላት የሆነውን ቡድን የሚመሩ ነበሩ ። ትሮትስኪና « የግራ ኮሚኒዝም » ቡድን በፓርቲው ውስጥ ጦርነቱ እንዲቀጥል በመጠየቅ ሌኒንን በመቃወም የከረረ ትግል አደረጉ ። እነዚህ ሰዎች የጀርመኑን ኢምፔሪያሊስት መትቶ የሚመልስ ገና አንዳችም የጦር ሠራዊት የሌለውን ፣ ወጣቱን የሶቭየት መንግሥት በማጋለጥ በጀርመን ኢምፔሪያሊስቶችና በሀገሪቷ ውስጥ ባሉ ጸረ-አብዮታውያን መዳፍ ውስጥ ሿረቁ ።

እንደ እውነቱ ከሆነ ይህ ጥበብ በተሞላበት መንገድ በግራ ለበስ ሐረጐች የተሸፋፈነ የጠብ አጫሪዎች ፖሊሲ ነበር ።

የካቲት 10 ቀን 1918 ዓ. ም. የብሬስት ሊቶቭስክ የሠላም ድርድር ፈረሰ ። ሌኒንና ስታሊን በፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ ስም የሰላም ድርድሩ እንዲፈረም ቢያሳስቡም፣የብሬስት ሊቶቭስክ የሶቭየት ልዑካን ቡድን



ሊቀመንበር የነበረው ትሮትስኪይ ከቦልሼቪክ ፓርቲ የተሰጠውን መመሪያዎች ተንኰል በተሞላበት መንገድ ተቃወመ ። የሶቭየት ሪፓብሊክ ጀርመን ባቀረባቸው ሀሳቦች ምክንያት የሰላም ውሳኔውን ተቃውሞታል ሲል ለፈፈ ። ከዚሁ ጋር የሶቭየት ሪፓብሊክ እንደማይዋጋና የጦር ሠራዊቱ ከየግንባሩ መመለሱን እንደጀመረ ለጀርመኖች ነገራቸው ።

ይህ በጣም አሰቃቂ ነበር ። ጀርመን ኢምፔሪያሊስቶች የሶቭየትን ሀገር ለመውረር ፍላጐታቸው ከእንደዚህ ያለ ከሀዲ የበለጠ ሌላ አንዳችም ነገር አይፈልጉም ።

የጀርመን መንግሥት ጦርነት ለማቆም የተደረገውን ስምምነት በመጣስ ወረራ አደረገ ። የጥንቱ የጦር ሰራዊት ቅሬቶች ተሰባሰቡና ከፍተኛ ማጥቃት በማድረግ ላይ ካለው የጀርመን ሠራዊት ፊት ለፊት ተሰራጩ ። ጀርመኖች ሰፊ አካባቢዎችን በመያዝና በፔትሮግራድ ላይ እያንገዋበቡ ወደፊት ገሰገሱ ። የጀርመን ኢምፔሪያሊስቶች የሶቭየትን ስልጣን ለመገርሰስና ሀገሪቷን የቅኝ ግዛት ለማድረግ ባላቸው ዐላማ የሶቭየትን መሬት ያዙ ። የጥንቱ የተፈረካከሰው የዛሩ ጦር ሰራዊት የጀርመንን ኢምፔሪያሊዝም የመሰለ ሀይለኛ ጠላት መቋቋም አልቻለምና ከዚህ ግፊት በዝግታ አፈገፈገ ።

ይሁን እንጂ የጀርመን ኢምፔሪያሊስት ወታደራዊ ጣልቃ ገብነት በሀገሩ ውስጥ ሀይለኛ አብዮታዊ አመጽ ለመነሳሳቱ ምልክት ነበር ። ፓርቲውና የሶቭየት መንግሥት « ሶሻሊስት አባት አገር በአደጋ ላይ ነው ! » የሚል ጥሪ አወጣ ። ለዚህም ምላሽ የሠራተኛው መደብ በታላቅ ሀይል የቀዩን ጦር ሰራዊት ሬጅመንቶች መመስረት ጀመረ ። የአዲሱ ጦር ሰራዊት ወጣት ክፍሎች ሕዝባዊ አብዮታዊ ጦር እስከ ጥርሱ የታጠቀውን የጀርመንን ወንበዴ ጀግንነት በተሞላበት መንገድ ተቋቋሙት ። በናርቫና ፓስኰቭ የጀርመን ወራሪዎች በጠንካራ ምት እንዲመለስ ተገደዱ ። ወደ ፔትሮግራድ ያደርጉት የነበረው መገስገስ ሊገታ በቅቷል ። የካቲት 23 ቀን—የጀርመን ኢምፔሪያሊዝም ሀይል የተመለሰበት እለት—የቀዩ ጦር ሰራዊት የልደት ቀን በመሆን ሊታወስ የሚገባው ነው ።

የካቲት 18 ቀን 1918 ዓ. ም. የፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ በእስቾኳይ የሰላም ስምምነት እንዲደረግ ለመንገር ለጀርመን መንግሥት ቴሌግራም እንዲደረግ ሌኒን ያሳሰበውን ሀሳብ ተቀብሎ አጸደቀው ። ነገር ግን ከዚህ የተሻለ ድርድር ለማግኘት በማሰብ ጀርመኖች ጦርነቱን ገፉበትና የካቲት 22 ቀን የጀርመን መንግሥት የሰላም ድርድር ለማድረግ ፍቃደኛ መሆኑን ገለጸ ። አሁን የሚደረገው ድርድር በመጀመሪያ ከተሰነዘሩት ሀሳቦች የከበደ ነበር ።

ሌኒን፣ስታሊንና ስቨርድሎቭ የሰላሙን ድርድር በመደገፍ ያሳለፉትን ውሳኔ ከማስከበራቸው በፊት በማእከላዊ ኮሚቴው ውስጥ በትሮትስኪ

በቡካሪንና በሌሎች ትሮትስካይቶች ላይ ጠንካራ ትግል ማካሄድ ነበረ
በቡካሪንና ትሮትስኪይ «በእርግጥ የጀርመን ኢምፔሪያሊስቶችን
ባቸው ። ቡካሪንና ትሮትስኪይ «በእርግጥ የጀርመን ኢምፔሪያሊስቶችን
ደግፈዋልና አብዮት በጀርመን ውስጥ እንዳያድግና እንዳይዳብር እሰናክለ
ዋል» ሲል ሌኒን ተናገረ ። (የሌኒን ስብስብ ሥራዎች ፤ ሩሲያ እትም ቅጽ 22 ገጽ 307)

የካቲት 23 ቀን ማእከላዊ ኮሚቴው ለድርድሩ ጀርመኖች ያቀረቡ ትን መደራደሪያ ነጥቦች በመቀበልና የሰላም ድርድሩን ለመፈራረም ወሰነ ። የትሮትስኪና የቡካሪን ከዳተኙነት የሶቭየትን ሪፓብሊክ በጣምአደ ጋ ላይ ጣለው ። ላቲቪያ ፣ ኢስቶኒያ ፖላንድን ሳይጨምር በጀርመን መን ግሥት እጅ ገቡ ። ከሶቪየት ሪፓብሊክ ዩክሬይን በጣሙኑ በመጉዳት ወደ ጀርመን መንግሥት ገባርነት ተለወጠች ። የሶቪየትም ሪፓብሊክ ለጀርመኖች የጦር ካማ ወደ መከፈሉ ተዘዋወረ ።

እስከዚያ ጊዜ ድረስ « ግራ ኮሚኒስቶች » በከሀዲነት አዘቅት ውስጥ እየጠለቁ ፣ እየሰመጡ በመሄድ ሌኒንን በመቃወም የሚያደርጉትን ትግል ገፉበት ።

ለጊዜውም ቢሆን « ግራ ኩሚኒስቶች » (ቡካሪን ፣ ኦሲንስኪይ ፣ ያኩቭሊቭ ፣ ስቱኩቭና ማንቴሌቭ) ሀላፊነት የያዙበት የሞስኮ የፓርቲ ሪጅናል ቢሮ በማእከላዊ ኮሚቴው ላይ ምንም እምነት የለንም ሲሉ ውሳኔ አሳለፉ ። ውሳኔው ፓርቲውን ለመከፋፈል የታቀደ ነበር ። ቢሮው « በቅ ርብ ጊዜ ውስጥ ሊመጣ የሚችለውን የፓርቲውን መከፋፈል ለመከላከል ያለው እድል የመነመነ ነው» ። « ግራ ኮሚኒስቶች » ጸረ-ሶቪየት አቋም ያለው ውሳኔ እስከ ማስተላለፍ ደርሰዋል ። « ለአለም አቀፍ አብዮት ጥቅም ስንል እያደር ፍጹም ሕጋዊ እየሆነ የመጣውን የሶቪየት ስልጣን እያዘ ቀዘቀ መሄዱ ተገቢ መሆኑን እናምንበታለን ። » ሲሉ ገለጹ ።

ይህንን ውሳኔ ሌኒን « እንግዳና በጣም አሰቃቂ » አድርጐ ቆጥሮ ታል ።

የትሮትስኪና « የግራ ኩሚኒስቶች » ይህ ጸረ-ፓርቲ ተግባር በዚ ያን ወቅት ለፓርቲው ግልጽ አልነበረም ። ነገር ግን በቅርቡ « የቀኝ ክን ፎችና የትሮትስካይቶች ግንባር » ያካሄዱት ጸረ-ሶቭየት ተግባር (ከ1938 ዓ. ም. ጀምሮ) በቡካሪንና በርሱ የሚመራ « ግራ ክንፍ ኮሚኒስቶች » ቡድን ፣ ከትሮትስኪና «ግራ ክንፍ» ሶሻሊስት አብዮታውያን ጋር በመ ሆን በዚያን ወቅት በምስጢር በሶቭየት መንግሥት ላይ ማሴራቸው አሁን በገሀድ ታወቀ ። አሁን ቡካሪን ፤ ትሮትስኪና የነርሱ ግብረ አበር ሴረኞች የብሬስት ሊቶቭስኪን ስምምነት ለማፍረስ ፣ ሌኒን ፣ ስታሊንና ስቨርድሎቭን በመያዝ ለመግደልና ቡካሪንና ፣ ትሮትስካይቶች « ግራ » ሶሻሊስት አብዮታውያንን ያቀፈ አዲስ መንግሥት ለመመስረት እንደወሰኑ ታወቀ ።



ይህን ሕቡእ ጸረ-አብዮት ሴራ ሲጠነስሱ « ግራ ክንፍ ኮሚኒስቶች » በትሮትስኪ እየተደገፉ ፓርቲውን ለመከፋፈልና አመራሩን ለመነጣጠል ዘመቻ በቦልሼቪክ ፓርቲ ላይ ከፈቱ ። ይሁን እንጂ በዚህ አስጊ ሁኔታ ፓርቲው በሌኒን ፣ በስታሊንና ስቨርድሎቭ ዙሪያ ተሰባሰበና በሰላም ጥያ ቄም ሆነ በማናቸውም ጥያቄዎች ከማእከላዊ ኮሚቴው ጐን በሙሉ እም ነት ቆመ ።

« የግራ ክንፍ ኮሚኒስቶች » ቡድን ከፓርቲው በመገለል ተሸነፈ ።

በሰላም ጥያቄ ላይ ፓርቲው የመጨረሻ ውሳኔውን ለማሳወቅ እንዲ ያስችለው ሰባተኛውን የፓርቲ ኮንግረስ ጠራ ።

መጋቢት 6 ቀን 1918 ዓ ም. ኮንግረሱ ተከፈተ ። ፓርቲያችን ስል ጣን ከጨበጠ ወዲህ ይህ የመጀመሪያ ኮንግረስ ነበር ። በኮንግረሱ 46 ድምጽ ያላቸውና 58 ሀሳብ መስጠት የሚችሉ ግን ድምጽ በሌላቸው ተወ ካዮች 145,000 የፓርቲ አባላት በመወከል የተገኙበት ኮንግረስ ነበር ። በርግጥ የፓርቲው አባላት በወቅቱ ከ270,600 የሚንያሱ አልነበሩም ። ልዩነቱ ፓርቲው በአስቸኳይ በመሰብሰቡ ምክንያት ፣ የድርጅቱ አብ ዛኛው ቁጥር በወቅቱ ተወካዮችን ለመላክ ባለመቻሉና ጀርመን በያዛቸው አካባቢዎች ውስጥ የሚገኙ ድርጅቶች ተወካዮችን ለመላክ ባለመቻላቸው እውነትነት ላይ የተመሠረተ ነበር ።

በዚህ ኮንግረስ ላይ ስለ ብሬስት ሊቶቭስኪ የሰላም ስምምነት ባቀረ በው ዘገባ ሌኒን እንዲህ አለ « . . . በፓርቲያችን ውስጥ ግራ ተቃዋሚ ክንፍ በመመስረቱ ምክንያት ፓርቲያችን አሁን የገጠመው ከባድ ቀውስ የሩስያ አብዮት ከገጠሙት ውስጥ አንዱ የከረረ ቀውስ ነው »
(የሌኒን 1 ስብስብ ሥራዎች 1 እንግሊዘኛ እትም 1 ቅጽ 8 1 ገጽ 293—94)

በብሬስት ሊቶቭስኪ የሰላም ስምምነት ርእስ ሌኒን ባቀረበው ውሳኔ በ30 ድምጽ ሲደገፍ ፣ በ12 ድምጽ ተነቅፎ 4 ድምጽ ሳይሰጥበት በአጠ ቃላይ ተቀባይነትን አገኘ ።

ይህ ውሳኔ በተላለፈ ማግሥት ሌኒን « አስጨናቂ ሰላም » በተሰኘ ርእስ እንዲህ ሲል ጽፍዋል ።

«የሰላሙ ድርድር ሊቋቋሙት የማይችሉት አስቸጋሪ ጉዳይ ነው ። የሆነ ሆኖ ታሪክ የራሱን ፍርድ ይሰጣል. . . ለመደራጀት 1 ለመደራጀትና አሁንም ለመደራጀት እንነሳ ፣ ምንም አይነት ፈተናዎች ቢኖሩብንም መጪው የኛ ነውና ። » (የሌኒን ስብስብ ስራዎች 1 ሩሲያ እትም 1 ቅጽ22 ገጽ 288)

በውሳኔው ላይ ፣ ኮንግረሱ ከሶቭየት ሪፓብሊክ ሌላ የኢምፔሪያሊ ስቶች ወታደራዊ ወረራ የማይቀር መሆኑን አሳውቆና ስለሆነም ኮንግረሱ የፓርቲው መሠረታዊ ተግባሮች ፣ ከመቼውም ጊዜ ይልቅ ጠንካራና ጽኑ

የሆነ የራስ ዲስፕሊን ማነጽና የሠራተኛውንና የገበሬውን ዲሲፕሊን ለመገንባት የጠበቀ እርምጃ መውሰድ ፣ ሶሻሊስት አገራችን ከሚደርስባት አደጋ ለመከላከል ራሱን መስዋእት እንዲያደርግ ሰፊውን ሕዝብ በሚገባ ማዘጋጀት ፣ ቀዩን ጦር ሠራዊት ማደራጀትና ፣ ሁሉም ዜጋ በወታደራዊ ስልት የመሰልጠንን ተግባር ማስተዋወቅ መሆኑን አስገነዘበ ።

የብሬስት ሊቶቭስኪ የሰላም ስምምነት በሚመለከት የሌኒንን ፖሊሲ በማጽደቅ ኮንግረሱ የትሮትስኪን የቡካሬንን አቋምና የተንበረከኩ «ግራ ክንፍ ኮሚኒስቶች » በራሱ በኮንግረሱ ውስጥ የመከፋፈል ተግባራቸውን ለመቀጠል የሚያደርጉትን ጥረት አወገዘ ።

የብሬስት ሊቶብስኪ የሰላም ድርድር የሶቭየትን ሥልጣን ለማጠናከርና የሀገሪቱን ምጣኔ-ሀብታዊ ሕልውና ለማደራጀት ፓርቲው ፋታ ሰጠ ።

የሰላም ድርድሩ በኢምፔሪያሊስቶች መሀከል የነበረውን ግጭት የኦውስትሪያና የጀርመን ከኢንቴንቴ የጦር ቃል ኪዳን አገሮች ጋር ያለውን ጦርነት ተጠቅሞ የጠላትን ሀይል ለመነጣጠል ፣ የሶቭየትን የምጣኔ ሀብት ስርአት ለማደራጀትና ቀዩን ጦር ለመመስረት አስችሎታል ።

የሰላም ድርድሩ ወዝአደሩ የገበሬውን ድጋፍ እንዲያተርፍና በዕርስበርሱ ጦርነት ነጭ ዘብ ጀኔራሎችን ለመውጋትና ጥንካሬውን ለማካበት አስችሎታል ።

በጥቅምቱ አብዮት ወቅት ሌኒን ሁኔታዎች ሲፈቅዱ እንዴት አድርጎ ያለአንዳች ፍርሀትና በቆራጥነት ወደፊት ማምረት እንዳለበት ቦልሼቪክ ፓርቲን በሚገባ አስተምሮአል ። በብሬስት ሊቶቭስኪ የሰላም ስምምነት ወቅት የጠላት ሀይል በግልጽ ከኛ ሀይል በአየለበትና እንደማናሸንፍ ተደርጐ በተወሰደበት ወቅት አሁን ካለው ሀይል በበለጠ በመዘጋጀት አዲስ የማጥቃት እርምጃ መውሰድ እንዲያስችለው በተገቢው መንገድ እንዴት ማፈግፈግ እንዳለበት ሌኒን ፓርቲውን አስተምሮአል ።

የሌኒንን መስመር ሀቀኛነት ታሪክ በሚገባ አረጋግጧል ።

በሰባተኛው የፓርቲ ኮንግረስ ላይ የፓርቲው ስም እንዲለወጥና የፓርቲው መርሀ ግብር እንዲቀየር ተወሰነ ። የፓርቲው ስም ተለውጦ የሩስያ ኮሚኒስት ፓርቲ(ቦልሼቪክ)ተባለ—ሩ.ኮ.ፓ(ቦ)። ሌኒን ፓርቲያችንን ኮሚኒስት ፓርቲ ብለን መጥራት አለብን ምክንያቱም ይህ ስም ከፓርቲው ዘላቂ ግብ ጋር ማለትም ኮሚኒዝምን ለድል ከማብቃት ጋር በሚገባ የሚስማማ ነው ሲል አሳሰበ ።

ሌኒንንና ስታሊንን የያዘ ልዩ ኮሚሽን አዲሱን የፓርቲ መርሀ ግብር እንዲያረቅ ተመረጠ ። ሌኒን የነደፈው መርሀ ግብር ረቂቅ እንደመሰረት ተደርጐ ተወሰደ ።



ስለሆነም ሰባተኛው ኮንግረስ ታላቅ ታሪካዊ ጠቀሜታ ያለው ተግባር አከናወነ ። በፓርቲው አመራር ውስጥ ራሱን የመሸገውን ጠላት—«ግራ ክንፍ ኮሚኒስቶችን»ና ትሮትስካይቶችን አንበረከከ፣ ሀገሪቷን ከኢምፔሪያሊስቶች ጦርነት የማዳኑ ተግባር ተሳካለት ፣ ሰላምና ፋታ አገኘ ፣ ቀዩን ጦር ለማደራጀት ፓርቲው በቂ ጊዜ እንዲያገኝ አስቻለው ። ፓርቲው በብሔራዊ ምጣኔ-ሀብቱ ውስጥ የሶሻሊስትን ሥርዓት ተግባራዊ ለማድረግ አስቻለው ።

8/ ለሶሻሊስት ግንባታው የመጀመሪያ እርምጃዎች ሌኒን ያቀረበው ንድፍ ፣ የደሀ አርሶ አደሮች ኮሚቴዎችና የሀብታም አርሶአደሮች (ኩላኮች) መደምሰስ «ግራ» ሶሻሊስት አብዮተኞች አመፅና እነርሱም በቁጥጥር ሥር የመዋላቸው ፤ አምስተኛው የሶቪየቶች ኮንግሬስና የሩሲያ ሶቭየት ፌደሬቲቭ ሶሻሊስት ሪፐብሊኮች(ሩ.ሶ.ፌ.ሶ.ሪ.ፓ.)ሕገ መንግሥት መጽደቅ ፤

በሰላም ድርድር ምክንያት ፋታ በማግኘቱ የሶቭየት መንግሥት ሶሻሊስት ግንባታውን ማካሄድ ጀመረ ። ከህዳር ወር 1917 ዓ.ም. እስከ የካቲት 1918 ዓ.ም. ድረስ ያሉትን ወቅቶች ሌኒን «የቀይ ዘብ መዲናዋን ያጠቃበት » ደረጃ ነው ብሎታል ። በ1918 ዓ ም የመጀመሪያው አጋማሽ ላይ የቡርዧውን ምጣኔ-ሀብታዊ ሀይል በመሰባበር የብሔራዊውን ምጣኔ-ሀብት ቁልፍ ስፍራዎች በራሱ ቁጥጥር ሥር አደረገ ። (ወፍጮዎች ፣ ፋብሪካዎች ፣ ባንኮች ፣ የባቡር መስመሮች ፣ የውጭ ንግድ የንግድ መርከቦች ፣ ወዘተ . . . ) የቡርዧውን መንግሥታዊ መኪና በማንኮታኮት የጸረ-አብዮት ሀይላት የሶቭየትን ሥልጣን ለመገርሰስ ያደረጉትን የመጀመሪያውን አደገኛ ጥረት ደረማመሰው ።

ይሁን እንጂ በምንም አይነት በቂ ሊሆን አይችልም ። እድገት ከተፈለገ ያሮጌው ሥርዓት መደርመስ በአዲስ ሥርዓት መተካትን ማስከተል አለበት ። በዚህም መሠረት በ1918 ዓ. ም. ጸደይ ወራት ሽግግሩ « ከበዝባገሮች መውረስ » ጀምሮ ወደ ሶሻሊስት ግንባታው ፣ አዲስ የእድገት ደረጃ ማለትም ድል ወደ አስገኙ ድርጅት መጠናከር ፣ የሶቭየት ብሔራዊ ምጣኔ-ሀብት መገንባት ፣ የሚደረግ ነበር ። ሌኒን በተገኘው ፋታ ልንጠቀምበት የሚገባን ትልቁ ተግባር የሶሻሊስት ምጣኔ-ሀብት ስርዓትን ለመገንባት መሠረት መጣል መጀመር ነው ሲል አስገነዘበ ።

ቦልሼቪኮች ምርትን በአዲስ መንገድ ማደራጀትና መምራትን መማር አለባቸው ። የቦልሼቪክ ፓርቲ ሩስያን አሳምኖአል ። ሌኒን ሲጽፍ የቦልሼቪክ ፓርቲ ለሕዝቡ ሲል ከሀብታሞች መዳፍ በሀይል መንጭቆ አውጥቶአልና አሁን ደግሞ ቦልሼቪክ ፣ ሩስያን እንዴት ማስተዳደር እንዳለበት በሚገባ ማወቅ ይኖርባቸዋል ይላል ።

ሌኒን በዚህ በተወሰነ ደረጃ ውስጥ ዋነኛው ተግባር ሀገሪቷ ልታመርት በምትችለው ማናቸውም ነገር ላይ ትኩረት መስጠትና ምርቶች

ክፍፍል ላይ ጠበቅ ያለ ቁጥጥር ማድረግ እንደሚያስፈልግ አስገነዘበ ። የንዑስ ከበርቴ ክፍሎች በሀገሪቷ የምጣኔ-ሀብት ስርዓት ውስጥ ተንሰራፍተዋል ። በሀገሪቷ የሚገኙ በሚሊዮን የሚቆጠሩ ጥቃቅን ባለንብረቶች ለካፒታሊዝም ማቆጥቆጥ ምቹ መስክ ናቸው ። እነዚህ ጥቃቅን ባለንብረቶች የሠራተኛ ዲሲፕሊን ወይም የሲቪል ዲሲፕሊንን አይቀበሉም ። ለመንግሥቱ የአስተዳደርና የቁጥጥር ሥርዓት አይታዘዙም ። በዚህ እጅግ አስቸጋሪ ወቅት በተለይ አደገኛ የሚሆነው የንዑስ ከበርቴዎች አመለካከትና አትራፊነት የሚያደርገው መፍጨርጨር ሲሆን የጥቃቅን ባለንብረቶችና ነጋዴዎች ታላቁ ጥረት በሕዝቡ ፍላጐት ለማትረፍ መራኰት ነው ።

በስራ ማላገጥ ፣ በኢንዱስትሪ ውስጥ የስራ ዲሲፕሊን ማጣት ላይ ፣ ፓርቲው ጠንካራ ዘመቻ ማካሄድ ጀመረ ። ሰፊው ሕዝብ አዲስ የሥራ ባህሪዎችን ለማወቅ ዝግ ያለ ነውና የሥራ ዲሲፕሊንን ለማስፈን የሚደረገውን ከፍተኛ ትግል መቀጠሉ የወቅቱ ታላቅ ተግባር ሆነ ።

ሌኒን በኢንዱስትሪ ውስጥ የሶሻሊስት ውድድርን ማዳበር አስፈላጊነት ፣ ቁራጭ የእርከን ምደባ ስርዓት (Piece ratesystem) ማስተዋወቅ የምንዳ እኩልነት መቋቋም -በተጨማሪም በትምህርትና በመግባቢያ ዘዴዎች ላይ—ከመንግሥት በተቻላቸው ሁሉ ለመውሰድ የሚፈልጉትን አስመልክቶ ፣ ሥራ ፈቶችንና አትራፊዎችን አስመልክቶ የማስገደድ መንገዶችን—አስፈላጊነት አስገነዘበ ። ሌኒን አዲሱ ዲሲፕሊን—የሥራ ዲሲፕሊን ፣ የጓዳዊ ግንኙነት ዲሲፕሊን ፣ የሶቭየት ዲሲፕሊን—በሚሊዮን በሚቆጠሩ ሠራተኞች ዘንድ ተግባራዊ ሥራቸው ውስጥ መኖር ያለበት ነውና « ይህ ተግባር መላውን ታሪካዊ ዘመን ይወስዳል »
(የሌኒን ምርጥ ሥራዎች እንግሊዘኛ እትም ቅጽ 7 ገጽ 393)

የአዲሱ የሶሻሊስት የምርት ግንኙነት የገጠሙት እነዚህ ሁሉ የሶሻሊስት ግንባታ ችግሮች የሶቭየት መንግሥት አጣዳፊ ተግባሮች በተሰኘው የሌኒን ክቡር ሥራው ላይ በሚገባ ተገልፀዋል ።

« ግራ ኮሚኒስቶች » ከሶሻሊስት አብዮታውያንና ከሜኔንሼቪኮች ጋር በመጣመር በነዚህ ጥያቄዎች ላይ ሌኒንን በጽኑ ታገሉት ። ቡካሬን ፣ ኦሲኒስኪና ሌሎችም በአንድነት በተቋሞች ውስጥ የአንድን ሰው አስተዳደር ፣ በኢንዱስትሪ ውስጥ የቡርዧውን ጠበብት መቅጠርንና የተቀላጠፈ የሥራ ዘዴዎችን ማስተዋወቁን ፣ የዲሲፕሊን መግቢያዎችን አበክረው ተቃወሙ ። ይህን ፖሊሲ ማራመድ ማለት ወደቡርዧው ባህርያት መመለስ ማለት ነው ። ሲሉ ሌኒንን በመንቀፍ አወገዙ ። ከዚህም ጋር « ግራ ኮሚኒስቶች » በሩስያ ውስጥ ሶሻሊስት ግንባታውንና የሶሻሊዝም ድል ማድረግ ፍጹም የሚቻል ነገር አይደለም ፤ የሚለውን የትሮትስካይቶች አስተሳሰብ አስተጋቡ ።



« የግራ ክንፍ ኮሚኒስቶች » ግራ ለበስ ሐረግ ፣ መንግሥቱ ፣ የምጣኔ-ሀብታዊ ኑሮን ለመቆጣጠርና ለመምራት ያወጣውን ሕግ የሚቃረኑትን የሐብታም ገበሬዎችን የሥራ ፈቶችንና የአትራፊዎችን ጥቅም ለመጠበቅ መልካም ሽፋን ለመሆን ተጠቀሙባቸው ።

አዲሱን የድርጅት መመሪያ ለሶቭየት ኢንዱስትሪ በማውጣት ፣ ፓርቲው የገጠሩን ችግር ለመወጣት ተሰማራ ። ማለትም በደሀው ገበሬና በሐብታም ገበሬዎች መሀከል የሚደረገው ትግል የተፋፋመበት ወቅት ነበር ። ሐብታም ገበሬዎች ጥንካሬ እያገኙ በመሄዳቸው ከመሬት ከበርቴዎች የተወረሱትን መሬቶች ወሰዱ ። ደሀ ገበሬዎች በዚህንጊዜ ከፍተኛ ድጋፍ ይፈልጉ ነበር ። ሐብታም ገበሬዎች የወዝአደሩን መንግሥት በመውጋት ያላቸውን እህል በተወሰነ ዋጋ ለመንግሥቱ እንሸጥም ፤ አሻፈረኝ ሲሉ ተቃወሙ ። ሶሻሊስት እርምጃውን በመቃወም የሶቭየትን መንግሥት በእህል እጥረት ውስጥ ለመጣል ፈለጉ ። የኢንዱስትሪ ሠራተኞች ክፍል ደሀ ገበሬዎችን ለማደራጀትና የእህል እጥረት እንዲደርስ ከሚጥሩት ሐብታም ገበሬዎች ጋር የሚደረገው መራራ ትግል እንዲሰምር ለማድረግ ወደገጠሩ ተሰማሩ ።

« ጓዶች ፣ ሠራተኞች ፣ አብዮቱ በወሳኝ ሁኔታ ላይ መሆኑን አስታውሱ » ይላል ሌኒን ሲጽፍ « አብዮቱን ማዳን የምትችሉ እናንተ ብቻ መሆናችሁን አስታውሱ ። ሌላ ማንም ሊኖር አይችልም ። እኛ የምንፈልገው በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ ለሶሻሊዝም ዓላማ ታማኝ የሆኑ ለጉቦና ለሌብነት ራሳቸውን የሚያስገዙ ፣ ሐብታም ገበሬዎችን ፣ አትራፊዎችን ወራሪዎችንና የድርጅት እንቅፋቶችን ለመታገል እንደ ብረት የጠነከረ ሀይል መሆን የሚችሉ ምርጥ ፣ በፖለቲካ የበሰሉ ሠራተኞችን ነው »
(ሌኒን ስብስብ ስራዎች ፣ ሩሲያ እትም ፣ ቅጽ ፣ 23 ገጽ 25)

« ለዳቦ የሚደረገው ትግል ለሶሻሊዝም የሚደረግ ትግል ነው » ይላል ሌኒን ። ወደ ገጠር የተላከው የሠራተኞች ክፍል በዚህ መፈክር ስር ነበር የተደራጀው ። የህል እጥረትን ለመቋቋም ሸማቾችን እህል በተወሰነ ዋጋ ለመግዛት ለማስቻል የምግብ ሕዝባዊ ኮሚሳሮች የአስቸኳይ ጊዜ ሥልጣን የሚሰጡ አያሌ ድንጋጌዎች ወጡ ።

ሐምሌ 11 ቀን 1918 ዓ. ም. የገበሬዎች ኮሚቴዎችን የሚያቋቁም አዋጅ ወጣ ። እነዚህ ኮሚቴዎች ከሐብታም ገበሬዎች ጋር በሚደረገው ትግል ውስጥ ከፍተኛ ሚና ይጫወታሉ ። የተወረሱ መሬቶችንና የእርሻ መሣሪያዎችን በማከፋፈል ፣ ሐብታም ገበሬዎች ከሚገባቸው በላይ ያላቸውን እህል በመሰብሰብ ሠራተኛው መደብና ቀዩ ሠራዊት ወደሚገኙበት የእህል ማከማቻ ወስደው ይሰጣሉ ። አስራ አምስት ሚሊዮን ጋሻ የሐብታም ገበሬዎች መሬት በደሀ ገበሬዎችና በመሀከለኛ ገበሬዎች እጅ ውስጥ ገባ ። ሐብታም ገበሬዎች የምርት መገልገያ አብዛኛው ክፍል ተወርሶና ለደሀ ገበሬዎች ተመለሰ ።

በገጠሮች ውስጥ የደሀ ገበሬዎችን ኮሚቴዎች ማቋቋም በሶሻሊስት አብዮት እድገት ውስጥ ከፍተኛው ደረጃ ነበር ። ኮሚቴዎቹ በገጠሩ አካባቢ የወዝአደሩ እምባገነንነት ጠንካራ ምሽጎች ነበሩ ። ለቀዩ ጦር ሠራዊት ምዝገባ የተካሄደው በነርሱ በኩል ነበር ።

በገጠር አካባቢዎች የተደረገው የወዝአደሮች ዘመቻና የደሀ ገበሬዎች ኮሚቴዎች በገጠር የሶቭየትን ስልጣን አጠናከሩ፤እንዲሁም መሀከለኛ ገበሬዎች ከሶቭየት መንግሥት ጐን እንዲሰለፉ ታላቅ ፖለቲካዊ ጠቀሜታ አከናወኑ ።

በ1918 ዓ. ም. መጨረሻ ላይ ተግባራቸውን ከአጠናቀቁ በኋላ የደሀ ገበሬዎች ኮሚቴ ዎች ከገጠር ሶቭየቶች ተዋሀዱና ሕልውናቸው አበቃ ።

በነሐሴ 4 ቀን 1918 ዓ. ም. በተከፈተው የሶቭየቶች አምስተኛው ኮንግረስ ላይ « ግራ ክንፍ » ሶሻሊስት አብዮታውያን ሐብታም ገበሬዎችን ለመከላከል ሲሉ በሌኒን ላይ ብርቱ ዘመቻ አካሄዱ ። ይኸውም ሐብታም ገበሬችዎን በመጻረር የሚደረገውን ትግልና የሠራተኞች የምግብ ክፍል ወደ ገጠር መሰራጨቱን እንዳይቀጥል በመቃወም ነበር ። « ግራለበስ » ሶሻሊስት አብዮታውያን የኮንግረሱ አብዛኛው ክፍል የነርሱን ፖሊሲ መቃወሙን ባዩ ጊዜ በሞስኩ ውስጥ ሴራ ጀመሩና የትራዩከሽቫቲቲሊስኪን አሊን ሐሳብ በመያዝ ክሬሚሊንን በቦምብ ደበደቡ ። ይህ አጉል አመጽ በጥቂት ሰዓቶች ውስጥ በቦልሼቪኮች ተደመሰሰ ። በሌላ የሀገሪቷ ክፍሎች « ግራ ክንፍ » ሶሻሊስት አብዮታውያን ለማመጽ ቢሞክሩም ቅሉ እያንዳንዱ አመጻ ወዲያውኑ ተንበረከከ ።

ጸረ-ሶቭየቶችን « የቀኝ ክንፎችና የትሮትስካይቶች ግንባር » ጉዳይ የሚመለከት ፍርድ ቤት ተቋቋመ ። « የግራ ክንፍ » ሶሻሊስታዊ አብዮታውያን አመጽ በቡካሬንና በትሮትስኪይ ፈቃድና እውቀት ነበር የሶቭየትን ስልጣን በመቃወም የሚደረገው አጠቃላይ ጸረ-አብዮት ሴራ ይመራ የነበረው ።

እንዲህ ባለ ሁኔታ ፣ የ« ግራ ክንፍ » ሶሻሊስት አብዮታውያን አባል የነበረው ብሉምኪን ወደ ጀርመን ኤምባሲ በመሄድ በሞስኮ የጀርመን አምባሳደር የነበረውን ሚርባን ገደለ ። ብሉምኪን፤ ኋላ የትሮትስኪ ሰላይ ሆኖ የተገኘ፤ ያንን ያደረገበት ዋና አላማው ከጀርመን ጋር ጦርነት ለመቀስቀስ ነበር ። ይሁን እንጂ የሶቭየት መንግሥት ከጦርነቱ ራሱን ዞር አደረገና ጠብአጫሪዎቹ ያቀዱትን ጸረ-አብዮት እቅድ በማክሸፍ አደናገጣቸው ።

አምስተኛው የሶቭየቶች ኮንግረስ የመጀመሪያውን የሶቭየት ሀገ መንግሥት አጸደቀ ። — የሩስያ ሶቭየት ፌዴራላዊ ሶሻሊስት ሪፓብሊክ ።



## አጭር ድርሞ

ከየካቲት እስከ ጥቅምት ወር 1917 ዓ. ም. ድረስ ባሉት ስምንት ወራት ውስጥ የቦልሼቪክ ፓርቲ በሠራተኛው መደብ ፣ በሶቭየቶችና በሚሊዮን በሚቆጠሩ ገበሬዎች መሀከል የአብዛኛውን ድጋፍ ለማትረፍ እጅግ ከባድ የሆነውን ተግባር አከናወነ ። የንዑስ ከበርቴ ፓርቲዎች (ሶሻሊስት አብዮታውያን ፣ ሜንሼቪኮችና ሥርዓት አልበኞች) በሰፊው ሕዝብ ላይ ያሳደሩትን ተጽእኖ ለማላቀቅ ፓርቲው የነዚህን ንዑስ ከበርቴ ፓርቲዎች ፖሊሲ ደረጃ በደረጃ በማጋለጥና ከሰፊው ሠራተኛ መደብ ፍላጎት በተቃራኒው የቆሙ መሆናቸውን በማሳየት በሰፊው ሕዝብ መሀከል ተነቅረው እንዲተፉ በማድረግ መሠረት አሳጥቶአቸዋል ። የቦልሼቪክ ፓርቲ ሠፊውን ሕዝብ ለጥቅምቱ ሶሻሊስት አብዮት ለማዘጋጀት በግንባርና በደጀን ከፍተኛ ፖለቲካዊ ትግል አካሂዷል ።

የሌኒን ከስደት መመለስ ፣ የሚያዝያው የሌኒን በኩረ—ሀሳብ ፣ የሚያዝያው የፓርቲ ጉባኤና ስድስተኛው የፓርቲ ኰንግረስ ፤ በቦልሼቪክ ፓርቲ ታሪክ ውስጥ የወቅቱ ዋነኛና ወሳኝ ተግባሮች ነበሩ ። ፓርቲው ያሳለፋቸው ውሳኔዎች ለሠራተኛው መደብ የጥንካሬ ምንጭ በመሆን ለድል በጽኑ እምነት እንዲነሱ አድርጓቸዋል ። ከዚህም በቀር የሠራተኛው መደብ የአብዮቱን ዓይነተኛ ችግሮች እንዲያቃልሉ አስችሏቸዋል ። የሚያዝያው ኰንግረስ ከቡርዧው ዲሞክራሲያዊ አብዮት ወደ ሶሻሊስት አብዮት ለሚደረገው ሽግግር ፓርቲው የሚያደርገውን ጥረት መርቶታል ። ስድስተኛው የፓርቲ ኰንግረስ በቡርዧውና በጊዜያዊው መንግሥት ላይ የተደረገውን ትጥቃዊ አመጽ በግንባር ቀደምነት መርቷል ።

አጉብዳጅ ሶሻሊስት አብዮታውያንና ሜንሼቪክ ፓርቲዎች ሥርዓት አልበኞችና ሌሎችም ኰሚኒስት ያልሆኑ ፓርቲዎች የእድገታቸውን ዑደት ፈጸሙ ፡— ከጥቅምቱ አብዮት በፊት እንኳን የቡርዧው ፓርቲዎች በመሆን የካፒታሊስትን ሥርዓት ለመጠበቅና ለማጠናከር በብርቱ ተዋግተዋል ። ቡርዧውን ለመገርሰስና የሶቭየቶችን ሥልጣን ለመመሥረት የሰፊውን ሕዝብ ትግል መርቶት የነበረው የቦልሼቪክ ፓርቲ ብቻ ነበር ።

ከዚሁ ጋር ቦልሼቪኮች በፓርቲው ውስጥ ሆነው ፡— ዚኖቪየቭ ፣ ካሜኔቭ ፣ ይኰቭ ፣ ቡካሬን ፣ ትሮትስኪና ፓያታኮቭ ፓርቲው ለሶሻሊስት አብዮት ከሚከተለው ፈለግ በማስወጣት እጅ ለመስጠት ያደረጉትን ጥረት ድል ነስቷል ።

ሠራተኛው መደብ በቦልሼቪክ ፓርቲ እየተመራ ከደሀ ገበሬው ጋር ሕብረት በመፍጠርና በወታደሮችና በመርከበኞች ድጋፍ የቡርዧውን ሥልጣን ገርስሶ ጣለ ፣ የሶቭየቶችን ሥልጣን መሠረት ፣ አዲስ ዓይነት

መንግሥት ማለትም የሶሻሊስት ሶቭየት መንግሥት አቋቋመ ፣ የመሬት ከበርቴዎችን የመሬት ባለቤትነት አስወግዶ ለገበሬዎች ግልጋሎት እንዲውል አደረገ ፣ የሀገሪቱን መሬት ብሔራዊ አደረገ ፣ የካፒታሊስቶችን ሀብት ወረሰ ፣ ሩሲያ ከጦርነት ተላቃ ሰላምን እንድትጐናጸፍ አድርጓል ፣ ይህም እጅግ የተፈለገውን ፋታ በማግኘት ለሶሻሊስት ግንባታው እድገት አመቺ ሁኔታን ፈጠረ ።

የጥቅምቱ ሶሻሊስት አብዮት ካፒታሊዝምን ደረመሠ ። የቡርዧውን የምርት መገልገያ ወረሰ ወፍጮዎችን ፣ ፋብሪካዎችን ፣ መሬትን ፣ የባቡር መስመርንና ባንኮችን ፣ የመላው ሕዝብ ንብረት አደረገ ።

የወዝአደሩን አምባገነንነት በመመሥረት የሠፊውን ሀገር መንግስት ለሠራተኛው መደብ አስተላለፈ ፤ ማለትም የወዛደሩ መደብ የበላይ ሆነ ።

የጥቅምቱ ሶሻሊስት አብዮት በሰው ልጆች ታሪክ ውስጥ የአዲሱን ዘመን የወዝአደር አብዮት ዘመን :— ጕህ ቀደደ ።



<u>ምእራፍ ስምንት</u>

# የቦልሼቪክ ፓርቲ በውጭ ወታደራዊ ጣልቃ ገብነትና በርስ በርሱ ጦርነት ወቅት ፤

(1918—1920)

## 1/ የውጭ ወታደራዊ ጣልቃ ገብነት መጀመር ፣ የርስ በርሱ ጦርነት የመጀመሪያው ወቅት ፤

የብሬስት—ሊቶቪስክ ስምምነት መፈረምና በዚህም የተነሳ ጦርነቱ በምእራብ በሙሉ ኃይሉ በመካሄድ ላይ እያለ የሶቭየት ሕብረት በወሰደችው አብዮታዊ የምጣኔ—ሐብት እርምጃ የተነሳ መጠናከሯ ፣ በምእራብ ኢምፔሪያሊስቶች መካከል ፣ በተለይም በኢንቴንቴ ሀገሮች ከፍተኛ ድንጋጤ ፈጠረ ።

የኢንቴንቴ ኢምፔሪያሊስቶች በጀርመንና በሩስያ መካከል የሰላም ውል መፈረሙ በጦርነቱ የጀርመንን አቋም በማጠናከር በአንጻሩ የራሳቸውን እንደሚያዳክም ስጋት አደረባቸው ። በተጨማሪም በጀርመንና በሩስያ መካከል የሰላም መመሥረት ሁሉም ሀገሮችና ግንባሮች ለሰላም ያላቸውን ፍላጐት በማነሳሳት ጦርነቱ እንዳይካሄድና የኢምፔሪያሊስቶቹ ዓላማ እንዲከሽፍ ያደርጋል ብለው ሰጉ ። በመጨረሻም በሰፊ የግዛት ክልል የሶቭየት መንግሥት መኖርና ይህ ቡርዧውን ከገለበጠ ያገኛቸው ድሎች የምእራብን ሠርቶ አደሮችና ወታደሮች « እንደ ሚበክሉ » ፈሩ ። በተራዘመው ጦርነት እጅግ በመመረር ፣ ሠርቶ አደሮችና ወታደሮች የሩስያን አርአያ በመከተል ሣንጃቸውን በጌቶቻቸውና በጨቋኞቻቸው ላይ ያዞሩ ይሆናል ። ስለሆነም ፣ የኢንቴንቴ መንግሥታት የሶቭየትን መንግሥት ለመገልበጥና በሀገሪቱ የቡርዧውን ሥርዓት የሚመልስ ፣ ከጀርመን ጋር የተደረገውን የሰላም ውል ውድቅ የሚያደርግና በጀርመንና በአውስትራሊያ ላይ ወታደራዊ ግንባር እንደገና የሚመሠርት የቡርዧ መንግሥት ለማቋቋም በሩስያ ጣልቃ ለመግባት ወሰኑ ።

የኢንቴንቴ ኢምፔሪያሊስቶች ይህን የተንኮል ሴራ የጠነሰሱት የሶቭየት መንግሥት ያልተጠናከረ በመሆኑ ጠላቶቹ መጠነኛ ጥረት ካደረጉ በቀላሉ ይወድቃል ብለው ስላመኑ ነበር ።

የሶቭየት መንግሥት ድሎችና መጠናከር ከሥልጣን በወረዱ መደቦች መካከል — የመሬት ከበርቴዎችና ካፒታሊስቶች ፣ በተደመሰሱ ፓርቲዎች—ሕገ መንግሥታዊ ዲሞክራቶች ፣ ሜንሼቪኮች ፣ ሶሻሊስት አብዮተኞች ፤ አናርኪስቶችና በተለያየ ቀለም የቀረቡ ቡርዧ ብሄረተኞች መካከልና በነጭ ዘብ ጀኔራሎች ፣ የኮሳክ መኰንኖች ወዘተ . . . መካከል የበለጠ ድንጋጤ ፈጠረ ።

ከጥቅምቱ አብዮት ድል የመጀመሪያዋ እለት አንስቶ ፣ እነዚህ ደመኞችን በሞላ በሩስያ ለሶሻሊስት ሥልጣን ምንም መሠረት ስለሌለ ፣ ይደመሰሳል ፣ በአንድ ወይም በሁለት ሳምንት ውስጥ ፣ ወይም በወር ፣ ካልሆነም በሁለትና በሶስት ወር ይወድቃል እያሉ ከጣሪያ በላይ መጮህ ጀመሩ ። ግን ፣ ምንም እንኳን ጠላቶቹ ቢራገሙም የሶቭየት መንግሥት ሕልውና በመቀጠሉና እየተጠናከረ በመሄዱ ፣ በሩስያ ውስጥ ያሉ ጠላቶቹ ከገመቱት በላይ ጠንካራ እንደሆነና ይህንን ለመገልበጥ የሁሉም ጸረ-አብዮተኞችን ትልቅ ጥረትና ቆራጥ ትግል እንደሚጠይቅ ለማመን ተገደዱ ። ስለዚህ ፣ የጸረ-አብዮተኞችን የማጥቃት ድርጊት ሰፋ ባለ መንገድ ለማነሳሳት ፣ ጸረ-አብዮት ኃይላትን ለማንቀሳቀስ ፣ በተለይ በኮሳክና በመሬት ከበርቴ ግዛቶች አካባቢ ወታደራዊ ካድሬዎችን ለማሰማራትና አመጽ ለማደራጀት ወሰኑ ።

ስለሆነም ፣ በ1918 የመጀመሪያው አጋማሽ ላይ ሁለት ኃይሎች ማለትም ከውጭ የኢምፔሪያሊስቶች ኢንስቲቴና ጸረ-አብዮተኞች ከውስጥ የሶቭየትን ሥልጣን ለመገልበጥ ተነሱ ።

ከነዚህ ኃይሎች መካከል ማናቸውም የሶቭየትን ሥልጣን ለመገልበጥ የሚያስፈልገውን ኃይል አሟልተው አይገኙም ነበር ። በሩስያ ውስጥ የሚገኙ ጸረ-አብዮተኞች በይበልጥ ከኮሳኮችና ከከበርቴ ገበሬዎች የተገኙ በሶሻሊስት መንግሥት ላይ አመጽ ለማስነሳት በቂ የሰው ኃይል ነበራቸው ። ገንዘብና መሣሪያ ግን አልነበራቸውም ። የውጭ ኢምፔሪያሊስቶች ገንዘብና መሣሪያ ነበራቸው ፣ ግን ለዚህ ዓላማ በቂ ወታደር « ማሰማራት » አይችሉም ነበር ፣ ይህም የሆነበት ምክንያት ከጀርመንና ከአውስትሪያ ጋር ለሚደረገው ጦርነት ስለሚፈለጉ ብቻ ሳይሆን ከሶቭየት ሕብረት ጋር ለሚደረገው ጦርነት አስተማማኝም ስለማይሆኑ ነው ።

በሶቭየት ሥልጣን ላይ የሚደረገው ጦርነት የሁለቱን ጸረ-ሶቭየት ኃይላት ፣ የውጭና የውስጥ ሕብረት ጠየቀ ። ይህ ሕብረት በ1918 መጀመሪያው አጋማሽ ላይ ተገኘ ።

በእንዲህ ያለ ሁኔታ ነበር ፣ በሀገር ውስጥ በሚገኙ ጸረ-አብዮተኞች በመደገፍ በሶቭየት ሥልጣን የውጭ ወታደራዊ ጣልቃ ገብነት የተጀመረው ።

ይህ በሩስያ የእፎይታው ጊዜ ማብቂያና የሩስያ ሠርቶ አደሮችና አርሶ አደሮች በሶቭየት ሥልጣን የውጭና የውስጥ ጠላቶች ላይ የተደረገው የርስ በርሱ ጦርነት መጀመሪያ ነበር ።

የጣልቃ ገብነቱ ጦርነት ፣ በሩስያ ላይ የተደረገ ጦርነትና እጅግ የከፋ ጦርነት ሆኖ ሳለ ፣ የታላቋ ብሪታኒያ ፣ የፈረንሳይ ፣ የጃፓንና የአሜሪካ ኢምፔሪያሊስቶች ምንም ጦርነት ሳያውጁ ወታደራዊ ጣልቃ ገብነታቸውን ቀጠሉ ። እነዚህ « የሰለጠኑ » ዘራፊዎች በምስጢርና በዘዴ ወደ ሩስያ



ባሕር ዳርቻዎች በመድረስ ወታደሮቻቸውን በሩስያ ግዛት ክልል አራገፉ ።

እንግሊዞችና ፈረንሳዮች ወታደሮቻቸውን በሰሜን በማከማቸት ፣ በውስጥ ነጭ ዘቦች አመጽ እየተረዱ አርካንገልንና ሙርማንስክን ይዘው ሶቭየቶችን በመገልበጥ የነጭ ዘቦች « የሰሜን ሩስያ መንግሥት » አቋቋሙ ።

ጃፓኖች ወታደሮቻቸውን በቭላዲቮስቶክ በማራገፍ የባሕር ዳርቻ ግዛቶችን ያዙ ፣ ሶቭየቶችን በታተኑ ፣ በመጨረሻ የቡርዧ ሥርዓት መልሰው ያቋቋሙ ነጭ ዘቦችን ደገፉ ።

በሰሜን ካውካሰስ ፣ ጄኔራሎች ፣ ኮርኔሎቭ ፣ አሌክሲዮቭና ዴኒኪን በእንግሊዞችና በፈረንሳዮች እየተደገፉ የነጭ ዘብ « ወዶ ዘማች ሠራዊት» መሠረቱ ። የኮሳኮች የላይኛው መደብ አባላት አመጽ አስነሱ ፣ በሶቭየቶች ላይ ጥቃት ጀመሩ ።

በዶን ፣ ጄኔራሎች ክራንስኖቭና ማሞንቶቭ በጀርመን ኢምፔሪያሊስቶች በስውር በመደገፍ ( ጀርመኖች በጀርመንና በሩስያ መካከል የሰላም ውል በመኖሩ የተነሳ በግልጽ ሊረዷቸው አልፈለጉም) የዶን ኮሳኮችን አመጽ አስነሱ ፣ የዶንን አካባቢ ያዙ ፣ በሶቭየቶች ላይ ጥቃት ጀመሩ ።

በመሀል ቮልጋ አካባቢና በሳይቤሪያ ፣ እንግሊዞችና ፈረንሳዮች የቼኮስሎቫክ ጓዶችን አመጽ አነሳሱ ። እነዚህ ከጦር ምርኮኞች የተመሠረቱ ጓዶች ከሶቭየት መንግሥት በሳይቤሪያና በሩቅ ምሥራቅ በኩል ወደ ሀገራቸው እንዲመለሱ ፈቃድ አገኙ ። ነገር ግን በመንገድ ላይ ሶሻሊስት አብዮተኞችን ፈረንሳዮችና እንግሊዞች በሶቭየት መንግሥት ላይ አመጽ ለማስነሳት ተጠቀሙባቸው ። የጓዶቹ አመጽ በቮልጋ አካባቢና በሳይቤሪያ ላሉ ሀብታም ገበሬዎችና በሶሻሊስት አብዮተኞች ተጽእኖ ሥር ለነበሩ የቮትኪኒስኪና የእዠቬቭስኪ ሥራዎች ሠራተኞች አመጽ ምልክት ሆነ ። የነጭ ዘብ ሶሻሊስት አብዮተኞች መንግሥት በቮልጋ ፣ በሳማራ ውስጥና የሳይቤሪያው ነጭ ዘብ መንግሥት በእምስኪ ተመሠረተ ።

በዚህ በእንግሊዝ ፣ በፈረንሣይ ፣ በጃፓን ፣ በአሜሪካ ግንባር ጣልቃ ገብነት ጀርመን አልተሳተፈችም ፣ ሌላ ምክንያት ባይኖረው እንኳን ከነዚህ ጋር ራሷ በጦርነት ላይ ስለነበረች ማድረግም አትችልም ነበር ። እንዲሁም ሆኖ ፣ ምንም እንኳን በሩስያና በጀርመን መካከል የሰላም ውል ቢኖር የቄሳር ዊልሄልም መንግሥት የእንግሊዞችን ፣ የፈረንሳዮችን ፣ የጃፓኖችን ፣ የአሜሪካኖችን ያህል መርዘኛ ጠላት መሆኑን ማንም ቦልሼቪክ አልተጠራጠረም ። የጀርመን ኢምፔሪያሊስቶች ሶቭየት ሩስያን ብቻዋን ለማድረግ ፣ ለማዳከምና ለመደምሰስ የተቻላቸውን ከማድረግ አልተቆጠቡም ። ኡክሬንን ከሷ በመንጠቅ — እውነት ፣ ይህ ከነጭ ዘብ ኡክሬናዊያ ራዳ (ምክር ቤት ) ጋር በተደረገ « ስምምነት » ነበር— በራዳው

ጥያቄ ወታደሮቻቸውን አስገብተው ከሶቭየት ሩስያ ጋር ምንም ዓይነት
ግንኙነት እንዳያደርጉ በመከልከል የኡክሬንን ሰፊ ሕዝብ መዝረፍና መጨ
ቆን ጀመሩ ። ትራንስካውካሲያን ከሶቭየት ሩስያ በመገንጠል በጆርጂያና
በአዘርቤጃን ብሔረተኞች ጥያቄ ወታደሮቻቸውን እዚያ አስፍረው በቲ
ፍሊስና በባኩ የአዛዥነት ሚና መጫወት ጀመሩ ። በዶን ሶቭየት መን
ግሥት ላይ አመጽ ለጀመረው ፣ ለጀኔራል ክራስኖቭ ፣ በእርግጥ በይፋ
አልነበረም ፣ በርካታ መሣሪያ ማቀበል የጀመሩት ።

በእንዲህ ያለ ሁኔታ ሶቭየት ሩስያ ከዋና የምግብ ፣ የጥሬ ሀብትና
የነዳጅ ምንጮቿ ተቋረጠች ።

በዚያን ወቅት በሶቭየት ሩስያ ሁኔታዎች እጅግ ከባድ ነበሩ ። የዳ
ቦና የሥጋ እጥረት ነበር ። ሠርቶ አደሮች ተራቡ ። በሞስኮና በፔትሮግ
ራድ በየሁለት ቀኑ የፓውንድ አንድ ስምንተኛ ዳቦ በራሽን መልክ ይታ
ደላቸው ነበር ፣ አንዳንዴ ምንም ዳቦ የማያገኙበት ጊዜም ነበር ። በጥሬ
እቃና በነዳጅ እጥረት የተነሳ ፋብሪካዎች ቆመዋል ፣ ወይም ለመቆም ተቃ
ርበዋል ። ነገር ግን የሠርቶ አደሩ መደብ አልተሸበረም ። ቦልሼቪክ ፓር
ቲውም እንዲሁ በዚያን ወቅት የነበረውን አስቃቂ ችግር ለመወጣት የተደ
ረገው ቆራጥ ትግል የሠርቶ አደሩ መደብ ጥንካሬ ምን ያህል ከባድ እንደ
ሆነና የቦልሼቪክ ፓርቲም መልካም ስም ምን ያህል ከፍተኛ እንደሆነ
አሳይቷል ።

ፓርቲው ሀገሪቱ የጦር ምሽግ እንደሆነች አውጆ የምጣኔ-ሀብት ፣ የባ
ሕልና የፖለቲካ ኑሮውን በጦርነት ሁኔታ ላይ መሠረተ ። የሶቭየት መን
ግሥት « አባት ሀገር በአደጋ ላይ ነው » ሲል አስታወቀ ፣ ሕዝቡም ለመ
ከላከል እንዲነሳ ጥሪ አደረገ ። ሌኒን « ሁሉም ነገር ወደ ጦር ግንባር » የሚል
መፈክር አነሣ ፣ በብዙ መቶ ሺ የሚቆጠሩ ሠርቶ አደሮችና አርሶ አደሮች
በቀዩ ጦር ውስጥ ለማገልገል ፈቃደኛ በመሆን ወደ ጦር ግንባር ዘመቱ ።
ግማሽ ያህሉ የፓርቲ አባላትና የወጣት ኮሚኒስቶች ሊግ አባላት ወደ ጦር
ግንባር ሄዱ ። ፓርቲው ለአባት ሀገር ለሚደረግ ጦርነት ፣ በውጭ ወራሪዎች
ላይ ለሚደረግ ጦርነትና አብዮቱ ከሥልጣን ያባረራቸው በዝባዥ መደ
ቦች ባደረጉት አመጽ ላይ ለሚደረገው ጦርነት ሕዝቡን ቀሰቀሰ ። በሌኒን
የተደራጀው የሠርቶ አደሮችና የአርሶ አደሮች የመከላከያ ኮሚቴ ለጦሩ
ግንባር ተጨማሪ ኃይል ፣ ምግብ ፣ ልብስና መሣሪያ የማቅረቡን ሥራ አደ
ራጀ ። በበጐ ፈቃድ ምትክ የወታደራዊ አገልግሎት ግዴታ መሆኑ በመቶ
ሺ የሚቆጠሩ አዲስ ምል ምሎች ወደቀዩ ጦር በማስገባት በአጭር ጊዜ
ውስጥ ኃይሉን ወደ አንድ ሚሊዮን ሰው ከፍ አደረገ ።

ምንም እንኳን ሀገሪቱ በአስቸጋሪ ሁኔታ ላይ ብትገኝና ለጋው ቀዩ
ጦር ያልተጠናከረ ቢሆንም የተወሰዱት የመከላከያ እርምጃዎች የመጀ
መሪያ ፍሬአቸውን መስጠት ጀመሩ ። ጀኔራል ክራስኖቭ በእርግጥ እይዛ
ታለሁ ብሎ ካመነባት ከጻሪትስኒ ተባሮ ከዶን ወንዝ ማዶ እንዲሄድ ተገ



ደደ ። የጀኔራል ዴኒኪን ጦር በሰሜን ካውካሰስ ትንሽ ክልል ውስጥ ሲወ
ሰን ፣ ጀኔራል ኮርኒሎቭ ከቀዩ ጦር ጋር ባደረገው ጦርነት ተገደለ ። ቼኮ
ዝሎቫኮችና ነጭ ዘብ ሶሻሊስት አብዮተኞች ከካዛን ከሲምቢረስክና ከሳ
ማራ ተባርረው ወደ ኡራልስ ሄዱ ። በነጭ ዘቡ ሳቪንኮቭ የሚመራውና በሞ
ስኮ የእንግሊዝ ሚሲዮን ዋና ኃላፊ በሆነው በሉክሀርት የተደራጀው የያሮ
ስላቭል አመጽ ተደምስሶ ሉክሀርት ራሱ ታሰረ ። ጓድ ዩሪትስኪንና ቦሎ
ዳረስኪን የገደሉትና በሌኒን ሕይወት ላይ የተንኮል ሙከራ ያደረጉ ሶሻ
ሊስት አብዮተኞች በቦልሼቪኮች ላይ ነጭ ሽብር በማካሄዳቸው ቀይ ሽብር
ተካሄደባቸው ፣ በመሀል ሩስያ በሚገኙ ዋና ዋና ከተሞች በሞላ ተደመ
ሰሱ ። ወጣቱ ቀይ ጦር በጦርነቱ ነበልባል ተጠናከረ ።

የኮሚኒስት ኮሚሳሮች ሥራ በቀይ ጦሩ መጠናከርና የፖለቲካ ትምህ
ርት እንዲሁም ዲሲፕሊናቸውንና የውጊያ ብዛታቸውን ከፍ ለማድረግ
ወሣኝነት ነበረው ።

ነገር ግን የቦልሼቪክ ፓርቲ እነዚህ የመጀመሪያዎች እንጂ ፣ የቀዩ
ጦር ወሣኝ ድሎች አለመሆናቸውን ተረድቷል ። አዲስና እጅግ ከፍተኛው
ጦርነት ገና ወደፊት እንደሆነና ሀገሪቷ የተያዙባትን የምግብ ፣ የጥሬ
እቃና የነዳጅ አካባቢዎች ማስመለስ የምትችለው ከጠላት ጋር በሚደረ
ገው የተራዘመና መራራ ትግል እንደሆነ ያውቅ ነበር ። በመሆኑም ፣ ቦል
ሼቪኮች ለረዥም ጦርነት ከፍተኛ ዝግጅት ማድረግና ሀገሪቱ በሞላ የጦ
ሩን ግንባር እንድትረዳ አደረገ ። የሶቭየት መንግሥት የጦርነት ኮሚኒ
ዝምን ሥርዓት በሥራ ላይ አዋለ ። ለጦሩና ለእርሻው አካባቢ ሸቀጣሸቀ
ጦችን ማዳረስ እንዲቻል ፣ ከትላልቅ ኢንዱስትሪዎች በተጨማሪ መካከ
ለኛና ትንንሽ ኢንዱስትሪዎችን በቁጥጥሩ ስር አደረገ ። ለሠራዊቱና ለሠ
ርቶ አደሮች ጥራጥሬን ማከፋፈል እንዲቻል ፣ የጥራጥሬ ንግድን በመን
ግሥት ቁጥጥር ስር አደረገ ፣ በጥራጥሬ የግል ንግድን አስወገደ ፣ በአርሶ
አደሩ እጅ የሚገኘው ትርፍ ምርት እንዲመዘገብና መንግሥት በተወ
ሰነ ዋጋ እንዲገዛው በማድረግ የትርፍ ምርት መውሰድን ሥርዓት መሠ
ረተ ። በመጨረሻም ፣ የሁሉም መደቦችን ሁለንተናዊ የጉልበት አገል
ግሎት ግዴታ አደረገ ። ለቡርዧው የጉልበት ሥራን ግዴታ በማድረግና
ሠርቶ አደሩን ለበለጠ አገልግሎት ወደ ጦር ግንባር በመላክ ፣ ፓርቲው
« የማይሠራ አይብላ » የሚለውን መርሆ በተግባር ተርጉሟል ።

እነዚህ በልዩ አስቸጋሪ ወቅት ለብሔራዊ መከላከያ አስፈላጊ የሆ
ኑትና ጊዜአዊ ባሕሪይ የነበራቸው እርምጃዎች በሞላ የጦርነት ኮሚኒዝም
በመባል ይታወቃሉ ።

ሀገሪቱ ራስዋን ለረጂምና ለትክክለኛ የርስ በርስ ጦርነት ፣ ከሶቭየት
ሥልጣን የውጭና የውስጥ ጠላቶች ጋር ለሚደረግ ጦርነት አዘጋጀች ።
በ1918 መጨረሻ ላይ የጦሯን ኃይል በሶስት እጥፍ ማሳደግና ለጦሩ የሚ
ቀርበውን ለንቅና ትጥቅ ማከማቸት ነበረባት ።

በዚያን ጊዜ ሌኒን እንዲህ ብሏል ፤

« በጸደይ ላይ አንድ ሚሊዮን ሰዎች ያሉበት ሠራዊት እንዲኖረን ወስነን ነበር ፣ አሁን ሶስት ሚሊዮን ሰዎች ያሉበት ጦር እንፈልጋለን ። ይህን ማግኘት እንችላለን ፣ እናገኛለንም ። »

## 2/ የጀርመን በጦርነቱ መሸነፍ ፣ አብዮት በጀርመን ፤ የሶስተኛው ዓለም አቀፍ መመሥረት ፣ ስምንተኛው የፓርቲ ኮንግረስ ፦

ሶቭየት ሕብረት ከውጭ ጣልቃ ገቦች ጋር ለሚደረግ አዲስ ጦርነት ዝግጅት በምታደርግበት ወቅት ፣ በምዕራብ ፣ በጦርነት ላይ በነበሩ ሀገሮች ፣ በጦር ግንባሮችም ሆነ በሀገራቸው ውስጥ ወሣኝ ድርጊቶች እየተከናወኑ ነበር ። ጀርመንና አውስትሪያ በጦርነቱና በምግብ ቀውስ የተነሳ ተወጥረው ነበር ። የታላቁ ብሪታንያ ፣ የፈረንሣይና የአሜሪካ መንግሥታት አዳዲስ ምንጮችን እያገኙ ሲሄዱ ጀርመንና አውስትሪያ የመጨረሻ ክምችታቸውን በማገባደድ ላይ ነበሩ ። ጀርመንና አውስትሪያ በከፍተኛ ደረጃ ስለተዳከሙ በሽንፈት አፋፍ ላይ ነበሩ ።

በዚሁ ወቅት የጀርመንና የአውስትሪያ ሕዝቦች በአስከፊውና በረጅሙ ጦርነት ላይና በመከራና በረሀብ ላይ በጣሏቸው ኢምፔሪያሊስት መንግሥታቸው ላይ በቁጣ በመነሳሳት ላይ ነበሩ ። በብሬስት ሊቶቭስክ የሰላም ስምምነት ተፈርሞ ከሶቭየት ሩስያ ጋር ጦርነት ከመቆሙ በፊት እንኳን የሶቭየት ወታደሮች ከአውስትሪያና ከጀርመን ወታደሮች ጋር ወንድማማችነት መመሥረታቸውም ፣ የጥቅምቱ አብዮት እንዳደረገው ሁሉ ከፍተኛ ተጽእኖ ነበረው ። የሩስያ ሕዝቦች አስከፊውን ጦርነት የራሳቸውን መንግሥት በመገልበጥ እንዲያበቃ ማድረጋቸው ለአውስትሪያና ለጀርመን ሠርቶ አደሮችም ትምህርት ሆናቸው ። በምስራቅ ግንባር የነበሩና ከብሬስት ሊቶቭስክ ስምምነት በኋላ ወደ ምእራብ ግንባር የተወሰዱ የጀርመን ወታደሮች ከሶቭየት ወታደሮች ጋር ያላቸውን ወንድማማችነትና የሶቭየት ወታደሮች ከጦርነቱ እንዴት እንደተገላገሉ በማስረዳት የጀርመንን ሠራዊት ሞራል ዝቅ አደረጉ ። በተመሳሳይ ሁኔታ የአውስትሪያ ሠራዊት መበታተን ከዚህ ቀደም ሲል ተጀምሮ ነበር ።

ይህ ሁሉ በጀርመን ወታደሮች መካከል ለሰላም ያለው ፍላጐት ከፍ እንዲል አደረገ ፤ ቀድሞ የነበራቸው የውጊያ ብቃት ዝቅ በማለቱ የኢንቴንቴ ጦር በሚያጠቃበት ወቅት ማፈግፈግ ጀመሩ ። በኅዳር 1918 በጀርመን አብዮት ፈነዳ ፣ ዊል ሄልምና መንግሥቱ ተገረሰሰ ።

ጀርመን ሽንፈቷን እንድታሳውቅና የሰላም ጥሪ እንድታደርግ ተገደደች ።

ጀርመን በአንድ ምት የመጀመሪያ ደረጃ ኃይል ከመሆን ፣ የሁለተኛ ደረጃ ኃያል ወደ መሆን ዝቅ አለች ።



ይህ ሁኔታ በሶቭየት ሥልጣን ላይ ወታደራዊ ጣልቃ ገብነት የጀመሩትን የኢንቴንቴ ሀገሮች በአውሮፓና በእስያ ኃያል ስላደረጋቸውና በሶቭየት ሀገር ላይ ይበልጥ ጣልቃ እንዲገቡ እንዲከቧትና በሶቭየት ስልጣን ዙሪያ ይበልጥ የከበባ ቀለበታቸውን እንዲያጠቡ ስላደረገ ለሶቭየት መንግሥት መጥፎ ነበር ። ወደ ኋላ እንደምናየው የሆነው ይህ ነበር ። በሌላ በኩል ደግሞ ከድክመቶቹ የበለጠ ፣ በሶቭየት ሩስያ አቋም ላይ መሠረታዊ ለውጥ ያስከተለ የራሱ ጥቅምም ነበረው ። በመጀመሪያ ደረጃ ፣ የሶቭየት መንግሥት የብሬስት ሊቶቭስኪን የሰላም ውል ውድቅ ለማድረግ ፣ የጦር ካሣ መክፈሉን ለማቆም ፣ ኢስቶንያን ፣ ላትቭያን ፣ ባዮሎሩስያን ፣ ሊቱዋንያን ፣ ኡክሬንና ትራንስካውካሲያን ከጀርመን ኢምፔሪያሊዝም መዳፍ ለማውጣት ግልጽ ወታደራዊና ፖለቲካዊ ትግል ለመጀመር ችሎ ነበር ። ሁለተኛና ዋነኛው ፣ በመሀል አውሮፓ በጀርመን ፣ የሪፑብሊክ አገዛዝ መኖሩና የሠርቶ አደሮችና ወታደሮች ተወካዮች ሶቭየቶች የአውሮፓን ሀገሮች አብዮታዊ ለማድረግ መገደዳቸውና ፣ በእርግጥም ማድረጋቸው በሩስያ ያለውን የሶቭየት ሥልጣን አጠናከረ ። በእርግጥ በጀርመን በነበረው አብዮት የሶሻሊስት ሳይሆን የቡርዧ በመሆኑ ፣ ሶቭየቶቹ በሩስያ ባሉ ሜንሼቪኮች ዓይነት አጐብዳጅ በሆኑ ሶሻል ዲሞክራቶች ስር ስለነበሩ የቡርዧ ፓርላማ ትሁት አገልጋይ ነበሩ ። ይህ የጀርመንን አብዮት ድክመት ይገልጻል ።ለምሣሌ፣ የጀርመን ነጭ ዘቦች እንደ ሮዛ ሉክሰምበርግና ካርል ሊብክኔች ያሉ ታዋቂ አብዮታውያንን ገድለው ሳይቀጡ መቅረታቸው ድክመታቸውን ያሳያል ። ይሁን እንጂ ፣ አብዮት ነበር ፤ ዊልሄልም ተገርስሷል ፣ ሠርቶ አደሮች እግር ብረታቸውን አውልቀው ጥለዋል ፣ ይህ በራሱ በምእራብ ያለው አብዮት እንዳይላላ ፣ በአውሮፓ ሀገሮች አብዮት እንዲነሳ ይጋብዛል ።

በአውሮፓ የአብዮት ማእበል ይነፍስ ጀመር ። በአውስትሪያ አብዮታዊ ንቅናቄ ተጀመረ ፣ በሀንጋሪም የሶቭየት ሪፑብሊክ ተመሠረተ ። በአብዮቱ ማእበል መነሳት ኮሚኒስት ፓርቲዎች በመድረክ ላይ ብቅ አሉ።

ለኮሚኒስት ፓርቲዎች ሕብረት ለሦስተኛው የኮሚኒስት ዓለም አቀፍ መመሥረት ዕውነተኛው መሠረት ተጣለ ።

በመጋቢት 1919 ፣ በሌኒን በሚመራው በቦልሼቪክ ፓርቲ አሳሳቢነት ፣ በሞስኮ የተደረገው የተለያዩ ሀገሮች ኮሚኒስት ፓርቲዎች የመጀመሪያ ኮንግሬስ ፣ ኮሚኒስት ዓለም አቀፍን መሠረተ ። ምንም እንኳን ብዙ ወኪሎች በከበባውና በኢምፔሪያሊስቱ ወረራ የተነሳ ሞስኮ ለመድረስ ባይችሉም ፣ በርካታ የአውሮፓና የአሜሪካ ትልልቅ ሀገሮች ተወካዮች በዚህ በመጀመሪያው ኮንግሬስ መገኘት ችለዋል ። የኮንግሬሱ ሥራ በሌኒን ነበር የተመራው ።

ሌኒን ስለ ቡርዧ ዲሞክራሲና ስለወዛደሩ አምባገነንነት ዘገባ አቀረበ ። የሶቭየት ዲሞክራሲ የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ትክክለኛ ዲሞክራሲ

መሆኑን አሳይቷል ። ኮንግረሱ ለወዛደሩ አምባገነንነትና በሞላው ዓለም ለሶቭየቶች ድል ቆራጥ ትግል እንዲያካሂዱ ለሁሉም ሀገሮች ወዛደሮች ጥሪ በማቅረብ መግለጫ አወጣ ።

ኮንግረሱ የሶስተኛው፣ኮሚኒስት ዓለም አቀፍ (E. C. C. I.) ሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴ አቋቋመ ።

በእንዲህ ያለ ሁኔታም አዲሱ ዓይነት ዓለም አቀፋዊ የወዛደሩ ድርጅት ኮሚኒስት ዓለም አቀፍ—ማርክሲስት ሌኒኒስት ዓለም አቀፍ ተመሠረተ ።

በመጋቢት ወር 1919 የፓርቲው ስምንተኛ ኮንግሬስ ተሰበሰበ ። የተሰበሰበው የተቃራኒ ሁኔታዎች ግጭት በነበረበት ወቅት ነበር ፤ በአንድ በኩል የኢንቴንቴ ሀገሮች አድሀሪ ጸረ-ሶቭየት ግንባር ተጠናክሯል ፤ በሌላ በኩል ደግሞ በአውሮፓ በተለይም በተሸነፉ ሀገሮች የአብዮቱ ማዕበል መነሳሳት የሶቭየትን አቋም አሻሽሏል ።

በኮንግሬሱ 313,766 የፓርቲ አባላትን የሚወክሉ 301 መምረጥ የሚችሉ አባላትና 102 መምረጥ የማይችሉ አባላት ተገኝተዋል ።

ሌኒን በመክፈቻው ንግግር በኮንግሬሱ ዋዜማ ላይ ለሞተውና ከቦልሼቪክ ፓርቲ አደራጆች አንዱ ለነበረው ዋይ ኤም ስቬ ርድሎቭ የማስታወሻ ምስጋና አቅርቧል ።

ኮንግሬሱ አዲስ የፓርቲ ፕሮግራም አቀረበ ። ይህ ፕሮግራም ስለ ካፒታሊዝምና ስለ ከፍተኛው ደረጃ ፤— ስለ ኢምፔሪያሊዝም ይገልጻል ። ሁለት የመንግሥታት ሥርዓቶች— የቡርዧ ዲሞክራሲያዊ ሥርዓትንና የሶቭየት ሥርዓትን ያወዳድራል ።

ለሶሻሊዝም ግንባታ ፤ የቡርዧውን ንብረት የመውሰዱን ሥራ ለማጠናቀቅ፣ በአንድ ወጥ የሶሻሊስት እቅድ መሠረት የሀገሪቱን የምጣኔ—ሀብት ለማስተዳደር፣ ብሔራዊ ምጣኔ—ሀብቱን ለማደራጀት የሞያ ማኅበራት እንዲሳተፉ ለማድረግ ፤ ስለ ሶሻሊስት የሥራ ዲሲፕሊን ፤ በሶቭየቶች ቁጥጥር ቡርዧ ባለሞያዎችን በምጣኔ—ሀብቱ መስክ ስለመጠቀም፣ መካከለኛ ገበሬዎችን ቀስ በቀስና በዘዴ በሶሻሊስት ግንባታ እንዲሳተፉ ለማድረግ ፓርቲው እንዲታገል ዝርዝር ተግባሮቹን ያብራራል ።

ኮንግሬሱ ፤ ኢምፔሪያሊዝም ከፍተኛው የካፒታሊዝም ደረጃ በሚለው ገለጻ በተጨማሪ ፤ በሁለተኛው የፓርቲ ኮንግሬስ ጸድቆ የነበረው ስለ ኢንዱስትሪ ካፒታሊዝምና ስለ ቀላል ሸቀጣሸቀጥ ምርት የሚያብራራው እንዲጨመርበት ሌኒን ያቀረበውን ሀሣብ ተቀብሎታል ። ኮንግሬሱ የምጣኔ-ሀብታችንን ውስብስብነት የመገንዘቡንና በሀገሪቱ ውስጥ እጅግ ብዙ የምጣኔ-ሀብት ክፍሎች ፤ በመካከለኛ ገበሬዎች እንደሚታየው ትናንሽ ሸቀጣሸቀጥ ማምረትን ጨምሮ መኖሩን ማስታወስ እንደሚገባው ተረድ



ቶታል ። በዚህም የተነሳ በፕሮግራሙ ላይ ክርክር በሚደረግበት ወቅት ስለካፒታሊዝም ፤ ስለ ሸቀጣሸቀጥ ምርት ፤ ስለ መካከለኛ ገበሬዎች ምጣኔ ሀብት ያሉ ሀረጎች ከመርሐ ግብሩ መውጣት አለባቸው ሲል ቡካሪን ያቀረበውን ጸረ-ቦልሼቪክ አመለካከት ሌኒን በጥብቅ አውግዟል ። የቡካሪን አመለካከት ፤ ሜንሼቪክ ትሮትስካይቶች መካከለኛ ገበሬዎች በሶቭየት መንግሥት እድገት ውስጥ የሚጫወቱትን ሚና በመካድ የሚያቀርቡት አስተሳሰብ ነው ። በተጨማሪም ፤ ቡካሪን የአርሶ አደሮች ትናንሽ የሸቀጥ ምርት ሀብታም ገበሬዎችን እንዲያቆጠቁጡና እንዲራቡ ማድረጉን በመሸፋፈን ያልፋል ።

ከዚህም ሌላ ቡካሪንና ፓያታኮቭ ስለ ብሔር ጥያቄ ያላቸውን ጸረ-ቦልሼቪክ አመለካከት ሌኒን ውድቅ አደረገ ። የብሔሮች የራሳቸውን እድል በራሳቸው የመሰወን መብት የሚለው ሀረግ በመርሐ ግብሩ ውስጥ እንዳይጨመር ተናግረዋል ፤ ይህ የወዛደሩን አብዮት ድልና የተለያዩ ብሔረሰቦችን ወዛደሮች ሕብረት ያደናቅፋል የሚል ሰበብ በማቅረብ የብሔሮችን እኩልነት ተቃውመዋል ። ሌኒን ይህን የቡካሪንንና የፓያታኮቭን ኢምፔሪያሊስት ፤ ትምክህተኛና ጠንቀኛ አመለካከት ደመሰሰ ።

በስምንተኛው ኮንግሬስ ከፍተኛ ግምት የተሰጠው ለመካከለኛ ገበሬዎች ስለሚወጣው ፖሊሲ ነበር ። ስለመሬት የወጣው አዋጅ አሁን አብዛኛው የአርሶ አደር ክፍል የሆኑትን የመካከለኛ ገበሬዎችን ፈጣን እድገት አስከተለ ። በቡርዧውና በወዛደሩ መካከል የሚዋልሉት የመካከለኛ ገበሬዎች ዝንባሌና ባሕርይ ለርስ በርሱ ጦርነትና ለሶሻሊስት ግንባታ ተስፋ እጅግ ከፍተኛ ግምት የሚሰጠው ነው ። የርስ በርሱ ጦርነት ውጤት በይበልጥ የሚወስነው የትኛው መደብ መካከለኛ ገበሬዎችን ወደራሱ መሳብ እንደሚችል — ወዛደሩ ወይስ ቡርዧው ነበር ። በቮልጋ አካባቢ 1918 ክረምት ላይ ቼኮዝሎቫኮች ፤ ነጭ ዘቦች ፤ ሀብታም ገበሬዎች ፤ ሶሻሊስት አብዮተኞችና ሜንሼቪኮች የሶቭየትን ሥልጣን ለመገልበጥ የቻሉት ከመካከለኛ ገበሬዎች አብዛኛው ክፍል ስለደገፋቸው ነበር ። በመሀል ሩስያ የሀብታም ገበሬዎች አመጽ በተነሳም ጊዜ እንዲሁ ነበር ። በ1918 በልግ ላይ ግን ሰፊው መካከለኛ ገበሬ ወደ ሶቭየት ሥልጣን ማዘንበል ጀመረ ። የነጮች ድል ሥልጣን ለመሬት ከበርቴዎች እንደሚመልስ ፤ የገበሬውን መሬት እንደሚወስድ ፤ አርሶ አደሮችን እንደሚያስዘርፍ ፤ እንደሚያስገርፍና እንደሚያሰቃይ ገበሬው ተረዳ ። ሀብታም ገበሬዎችን የደመሰሰው የደሀ ገበሬዎች ተግባርም የገበሬውን ዝንባሌ ለውጧል ። በዚህም መሠረት በህዳር 1918 ፤ ሌኒን ፤

« በሀብታም ገበሬዎች ላይ የሚደረገውን ትግል ለአንዳፍታ እንኳን ስትቃወሙ ፤ በደሀ ገበሬዎች ብቻ በጽኑ በማመን ከመካከለኛ ገበሬዎች ጋር መስማማትን ተማሩ » ብሏል ።

(ሌኒን ፤ ምርጥ ስራዎች 1 የእንግሊ. እትም ቅጽ 8 ገጽ 150)

በእርግጥ መካከለኛ ገበሬዎች መወላወላቸውን ጨርሶ አልተውም ፣ ግን ወደ ሶቭየት መንግሥታት ይበልጥ በመቅረብ በበለጠ ኃይል መርዳት ጀምረዋል ። ይህን በይበልጥ ያመቻቸው ስምንተኛው የፓርቲ ኮንግሬስ ስለመካከለኛ ገበሬዎች ያወጣው ፖሊሲ ነበር ።

ስምንተኛው ኮንግሬስ ስለ መካከለኛው ገበሬ ፓርቲው ትልቅ የፖሊሲ ለውጥ ያደረገበት ወቅት ነበር ። በዚህ ጥያቄ ላይ የሌኒን ዘገባና የኮንግሬሱ ውሳኔ አዲስ የፓርቲ መስመር መሠረተ ። ኮንግሬሱ የፓርቲው ድርጅቶችና ኮሚኒስቶች በሞላ በመካከለኛ ገበሬዎችና በሀብታም ገበሬዎች መካከል ያለውን ልዩነት በመገንዘብ የቀድሞዎችን ፍላጐታቸውን እያዩ ወደ ሠርቶ አደሩ ለማምጣት እንዲጥሩ አሳስቧል ። የመካከለኛ ገበሬዎች ኋላ ቀርነት በማስገደድና በቅጣት ሳይሆን በማሳመን መለወጥ አለበት ። በዚህም መሠረት ኮንግሬሱ በገጠሩ ሶሻሊስት እርምጃዎች ሲወሰዱ (ኮሚውናዎችና የእርሻ አርቴሎች ሲመሰረቱ) ግዳጅ እንዳይኖር መመሪያ ሰጥቷል ።የመካከለኛውን ገበሬ ጥቅም በሚነኩ ነገሮች ሁሉ ፣ ተግባራዊ ስምምነት እንዲደረግ ያስፈልጋል ። ኮንግሬሱ ከመካከለኛ ገበሬዎች ጋር የጸና ሕብረት እንዲመሠረት ፖሊሲ አውጥቶ ፣ በዚህም ሕብረት የመሪነቱን ሚና ወዛደሩ እንዲጫወት አስገንዝቧል ።

በስምንተኛው ኮንግሬስ ላይ ሌኒን ያቀረበው አዲስ ፖሊሲ ወዛደሩ በደሀው ገበሬ ላይ እምነት እንዲኖረው ፣ ከመካከለኛ ገበሬዎች ጋር የጸና ሕብረት እንዲመሠረትና ሀብታም ገበሬዎችን እንዲዋጋ ይጠይቃል ። ከስምንተኛው ኮንግሬስ በፊት ፓርቲው የነበረው ፖሊሲ በአጠቃላይ መካከለኛ ገበሬዎችን ገለልተኛ እንዲሆኑ ማድረግ የሚል ነበር ። ይህም ማለት ፓርቲው በአጠቃላይ መካከለኛ ገበሬዎች ከሀብታም ገበሬዎችና ከቡርዧው ጐን እንዳይሰለፉ ፈልጐ ነበር ማለት ነው ። አሁን ግን ይህ በቂ አይደለም ። ስምንተኛው ኮንግሬስ ከነጭ ዘቦችና ጣልቃ ገቦች ጋር ለመታገል እንዲሁም ሶሻሊዝምን በአስተማማኝ ሁኔታ መገንባት እንዲቻል መካከለኛ ገበሬዎችን ገለልተኛ ማድረግ ከሚለው ፖሊሲ ከመካከለኛ ገበሬዎች ጋር የጸና ሕብረት መመሥረት ወደሚለው ፖሊሲ ተሸጋገረ ።

ኮንግሬሱ ከአርሶ አደሩ ክፍል እጅግ ብዙ ስለሆኑት ስለ መካከለኛ ገበሬዎች ያወጣው ፖሊሲ በውጭ ጣልቃ ገቦች በነጭ ደጋፊዎቻቸው ላይ የተደረገውን ጦርነት በድል አድራጊነት ለመወጣት ከፍተኛ ሚና ተጫውቷል ። በ1919 በልግ ላይ ፣ ገበሬዎች ከዴኒኪንና ከሶቭየቶች ሥልጣን መሐል አንዱን መምረጥ ስለነበረባቸው ሶቭየቶችን መረጡ ፣ በመሆኑም የወዛደሩ አምባገነንነት እጅግ አደገኛ ጠላቱን ለመደምሰስ ቻለ ።

ቀዩን ጦር ከመመሥረት ጋር በተያያዙ ችግሮች ፣ « ወታደራዊ ተቃዋሚዎች » የሚባሉት በመድረክ ላይ በመከሰታቸው የተነሳ በኮንግሬሱ ውይይት ውስጥ ልዩ ስፍራ ያዘ ። ይህ « ወታደራዊ ተቃውሞ» አሁን ከመድረክ ላይ በጠፋው የቀድሞው « ግራ ኮሚኒስቶች » በርካታ



አባላትንና በምንም ተቃውሞ ከዚህ በፊት ያልተሳተፉ ፣ ነገር ግን በሠራዊቱ ውስጥ ትሮትስኪ በሚያደርገው አመራር ያልተደሰቱ ጥቂት የፓርቲ አባላትንም ይይዛል ። አብዛኞዎቹ የሠራዊቱ ተወካዮች በግልጽ ትሮትስኪን ይቃወሙ ነበር ፣ በርስ በርሱ ጦርነት ጊዜ ይከዱን የነበሩትን ጨምሮ ለአሮጌው ወታደራዊ ባለሙያዎች ያለውን ክብርና በሠራዊቱ ውስጥ በቆዩ ነባር የቦልሼቪክ ካድሬዎች ላይ ያለውን ስድና መጥፎ አመለካከት ተቃውመዋል ። ትሮትስኪ « የሚያደርጋቸው » አንዳንድ ነገሮችም ለኮንግረሱ ቀርበው ነበር ። ለምሣሌ ፣ እሱ ስላልተደሰተባቸው ብቻ በጦር ግንባር ላይ የሚገኙ በርካታ ኮሚኒስቶችን ለመግደል ሞክሯል ። ይህ በቀጥታ የጠላት ሥራ ነው ። የማእከላዊ ኮሚቴው ጣልቃ ገብነትና የወታደሮች ተቃውሞ ብቻ ነበር የነዚህን ጓዶች ሕይወት ያዳነው ።

ነገር ግን « ወታደራዊ ተቃውሞው » የትሮትስኪን የፓርቲ ፖሊሲ ማዛባት እየተቃወመ ፣ የሠራዊቱን መገንባት በሚመለከት በበርካታ ነጥቦች ላይ ትክክል ያልሆነ አቋም ይዞ ነበር ። ሌኒንና ስታሊን « ወታደራዊ ተቃዋሚዎችን » በጥብቅ ተቃውመዋል ፣ ምክንያቱም የኋለኞቹ የሽምቅ ተዋጊነት መንፈስ እንዲኖር ደግፈዋል ፣ የቀዩን ጦር አመሠራረት ፣ የአሮጌውን ሠራዊት ባለሞያዎችን መጠቀምን ፣ ያለዚህ ምንም ሠራዊት መኖር የማይችል መሆኑ እየታወቀ ከብረት የጠነከረ ዲሲፕሊን እንዳይመሠረት ተቃውመዋል ።

እስታሊን እንዲህ ብሏል ፤

« ወይ እውነተኛ የሠርቶ አደርና የአርሶ አደር — በይበልጥም የአርሶ አደር — ሠራዊት ፣ ጥብቅ ዲሲፕሊን ያለው ሠራዊት ፣ መሥርተን ሪፑብሊኳን መጠበቅ አለብን ፣ አለበለዚያም እንጠፋለን »

« የወታደራዊ ተቃዋሚዎችን » በርካታ ሀሳቦች በመቃወም ፣ ኮንግሬሱ የማእከላዊ ወታደራዊ ተቋሞች አሠራርና በሠራዊቱ ያሉ የኮሚኒስቶች ሚና እንዲሻሻል በማድረግ ትሮትስኪን መታው ።

በኮንግሬሱ ወታደራዊ ኮሚሽን ተቋቋመ ፤ በዚህም ጥረት ስለወታደራዊ ጉዳዮች የተላለፈው ውሣኔ በኮንግሬሱ በአንድ ድምጽ ወደቀ ።

ይህ ውሳኔ ቀዩን ጦር ለማጠናከርና ወደ ፓርቲው ይበልጥ ለማቅረብ ረድቷል ።

ኮንግሬሱ በፓርቲና በሶቭየቶች ሥራዎችና ፓርቲው በሶቭየቶች ውስጥ ስለሚኖረው ሚና ተወያይቶበታል ። ኮንግሬሱ ስለፓርቲው ሚና በሚከራከርበት ወቅት አድር ባዩ የሳፕሮኖቭ አሲኒስኪ ቡድን ፓርቲው የሶቭየቶችን ሥራ መምራት የለበትም የሚል አቋም በመውሰዱ ተቃውመውታል ።

በመጨረሻም ፣ እጅግ በርካታ አዳዲስ አባላት ወደ ፓርቲው በመጕረፋቸው የተነሳ ኮንግሬሱ የፓርቲውን ማኅበራዊ ይዘት ለማሻሻል እርምጃዎችን በመውሰድ አባላቱን እንደገና ለመመዝገብ ወሰነ ።

በእንዲህ ዓይነት የመጀመሪያው የፓርቲ አባላትን የማጥራት እርምጃ ተጀመረ ።

3/ የውጭ ጣልቃ ገብነት መስፋፋት ፤ የሶቭየት ግዛት ከውጭው ዓለም መገለል ፣ የኮልቻክ ዘመቻና ሽንፈት ፣ የዴንኪን ዘመቻና ሽንፈት ፣ የሶስት ወር እፎይታ ፣ ዘጠነኛው የፓርቲ ኮንግሬስ ፦

ጀርመንና አውስትሪያን ድል ከመቱ በኋላ ፣ የኢንቴንቴ መንግሥታት በሶቭየት ሕብረት ላይ ትልቅ ወታደራዊ ኃይል ለማዝመት ወሰኑ ። ጀርመን ከተሸነፈችና ወታደሮቹን ከኡክሬንና ከትራንስካውካሲያ ካስወጣች በኋላ ፣ እንግሊዝና ፈረንሣይ የጦር መርከቦቻቸውን ጥቁር ባህር ላይ በማስፈርና ወታደሮቻቸውን ኦዴሳና ትራንስካውካሲያ በማራገፍ የቧን ስፍራ ያዙ ። የኢንቴንቴ ጣልቃ ገብ ኃይሎች እጅግ ጨካኝ በመሆናቸው በወረሯቸው አካባቢ የሚገኙ ሠርቶ አደሮችንና ወዛደሮችን በሞላ ለመጨፍጨፍ ትንሽ እንኳን አላመነቱም ። አሰቃቂ ተግባራቸው ከፍተኛ ደረጃ በመድረሱ ቱርኪስታንን ከያዙ በኋላ ሀያ ስድስት የባኩ ቦልሼቪኮችን-ሻውሚያን ፣ ፊዮሌቶቭን ፣ ጃፓሪድዝን ፣ ማሊጂንን ፣ አዚዝቤኮቭን ፣ ኮርጋኖቭን የመሳሰሉ ጓዶችን ጭምር — በሶሻሊስት አብዮተኞች እርዳታ ወደ ትራንስካውካሲያ አካባቢ በመውሰድ በጭካኔ ረሸኗቸው ።

ጣልቃ ገቦቹ ወዲያው በሩስያ ላይ ማእቀብ አደረጉ ። የባህር በሮችና ሌሎች ከውጭው ዓለም ጋር የሚያገናኙ መሥመሮች በሞላ ተቋረጡ ።

በሁሉም አካባቢ ማለት ይቻላል ፣ ሶቭየት ሩስያ ተከበበች ።
የኢንቴንቴ ሀገሮች ተስፋቸውን በሳይቤሪያ ፣ ኦምስክ ውስጥ በሚገኘው ፣ በአድሚራል ኮልቻክ ላይ ጣሉ ። እሱ « የሩስያ የበላይ ገዥ » በመባል በሀገር ውስጥ ያሉ ጸረ-አብዮት ኃይላት በሞላ በሱ ትእዛዝ ሥር ሆኑ ።
በመሆኑም የምሥራቁ ግንባር ዋና የጦር ግንባር ሆነ ።

ኮልቻክ በርካታ ጦር በማከማቸት በ 1919 ጸደይ አካባቢ ወደ ቮልጋ ተቃረበ ። እጅግ ከፍተኛ የተባሉት የቦልሼቪክ ኃይሎች ወደሱ እንዲዘምቱ የወጣት ኮሚኒስት ሊግ አባላትና ሠርቶ አደሮችም እንዲንቀሳቀሱ ተደረገ ። በሚያዝያ 1919 የኮልቻክ ሠራዊት በቀዩ ጦር ኃይሎች ሽንፈት ስለደረሰበት ወዲያው በሁሉም ግንባር ማፈግፈግ ጀመረ ።

በምሥራቅ ግንባር ቀዩ ጦር ከፍተኛ የማጥቃት እርምጃ በመውሰድ ላይ እያለ ትሮትስኪ አጠራጣሪ እቅድ አወጣ ፤ ወደፊት የመገስገሱ ሁኔታ ኡራልስ ከመድረሱ በፊት እንዲቆም ሀሳብ ስላቀረበ ፣ በኮልቻክ ሠራዊት ላይ የሚደረገው ጥቃት እንዲቆምና ወታደሮች ከምሥራቅ ግንባር ወደ ደቡብ ግንባር እንዲዛወሩ ተደረገ ። የፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ በእንግሊዞችና በጃፓኖች እርዳታ የቀድሞ ይዞታው ላይ መመለስና ማገገም



ስለሚችል ኡራልስና ሳይቤሪያ በምንም ዓይነት በኮልቻክ እጅ መቅረት እንደሌለባቸው በደንብ ተገንዘበ ። ስለዚህ ይህን እቅድ ተቃውሞ ወደ ፊት የማጥቃት እርምጃ እንዲቀጥል መመሪያ ሰጠ ። ትሮትስኪ በመመሪያው ባለመስማማት የሥራ መልቀቂያ አቀረበ ። ማእከላዊ ኮሚቴው ይህን ባለመቀበል ወዲያውም በምሥራቅ ግንባር ጦርነት አመራር ምንም እንዳይሳተፍ አዘዘው ። ቀዩ ጦር በኮልቻክ ላይ ጥቃቱን ከምንጊዜውም በበለጠ ማካሄድ ጀመረ ። በሱ ላይ ብዙ ድሎችን በመቀዳጀት ኡራልስንና ሳይቤሪያን ከነጮች ነጻ አወጣ ። በዚህም ቀዩ ጦር ከነጭ ዘቦች ኋላ ያሉ እንቅስቃሴዎችን ድጋፍ አገኘ ።

በ1919 ክረምት ላይ ፣ ኢምፔሪያሊስቶች በሰሜን ምእራብ ግንባር ጸረ-አብዮተኞችን ይመራ የነበረው ጀኔራል ዩዴኒች ፔትሮግራድን በመውረር ቀዩ ጦር ከምሥራቅ ግንባር ትኩረቱን እንዲያዞር እንዲያደርግ አዘዙት ። በቀድሞ መኮንኖች ጸረ-አብዮት ቅስቀሳ ተጽእኖ በፔትሮግራድ አካባቢ በሁለት ጦር ሠፈሮች የሚገኙ ወታደሮች በሶቭየት መንግሥት ላይ አመጹ ። በጦር ግንባር ባለው ጠቅላይ መምሪያው አመጽ ታየ ጠላት ፔትሮግራድን ስጋት ላይ ጣለ ። የሶቭየት መንግሥት በሠርቶ አደሮችና ባሕር ኃይሎች በመደገፍ የወሰደው እርምጃ ምስጋና ይግባውና የአመጹ ጦር ሰፈሮች ከነጮች ጸዱ ፣ የዩድኒች ወታደሮች ተሸንፈው ወደ እስቶኒያ ተባረሩ ።

በፔትሮግራድ አካባቢ የዩዴኒች መሸነፍ ኮልቻክን ለመምታት አመቺ ሁኔታ በመፍጠሩ ፣ በ1919 ሠራዊቱ በሙሉ ተደመሰሰ ። ኮልቻክ ራሱ ተማርኮ የኢርኩትስክ አብዮታዊ ኮሚቴ ስለ ፈረደበት ተረሸነ ።

ይህ የኮልቻክ መጨረሻ ሆነ ።
በዚያን ወቅት የሳይቤሪያ ነዋሪዎች ስለኮልቻክ ተወዳጅ ዘፈን ነበራቸው ፡—

« በእንግሊዝ መለዮ በፈረንሳይ ሪባን
በጃፓን ፒፓ ኮልቸክ መራ ዳንሱን
መለዮው ተቀደደ ሪባኑም ወደቀ
ትምባሆው ተበተነ ኮልቻክም ደቀቀ »

ኮልቻክ ተስፋቸውን ስላላሟላ ፣ ጣልቃ ገቦቹ ሶቭየት ሪፑብሊክን ለማጥቃት እቅዳቸውን ለወጡ ። ኦዴሳ ሰፍረው የነበሩ ወታደሮች ከሶቭየት ሪፑብሊክ ሠራዊት ጋር ያደረጉት ግንኙነት በአብዮታዊ መንፈስ ስለመረዛቸው በኢምፔሪያሊስት መንግሥታቸው ላይ ማመፅ ስለጀመሩ መለወጥ ነበረባቸው ። ለምሣሌ ፣ በኦዴሳ ውስጥ በአንድሬ ማርቴ የሚመራ የፈረንሳይ መርከበኞች አመጽ ነበር ። አሁን ኮልቻክ ስለተሸነፈ ፣ ኢንቴንቴ ተስፋውን የኮርኔሎቭ አባሪና « የወዶ ዘማች ሠራዊት » አደራጅ በሆነው በጄኔራል ዴኒኪን ላይ ጣለ ። በዚያን ጊዜ ዴንኪን የሶቭየትን

መንግሥት በደቡብ፣ በኩባን አካባቢ እየወጋ ነበር ። ኢንቴንቴ የእርሱን ጦር እጅግ ብዙ መሣሪያ አስታጥቆ የሶቭየትን መንግሥት በሰሜን እንዲወጋ ላከው ።

የደቡቡ ግንባር አሁን ዋና የጦር ግንባር ሆነ ።

ዴኒኪን በሶቭየት መንግሥት ላይ ዋናውን ዘመቻ በ1919 ክረምት ላይ ጀመረ ። ትሮትስኪ የደቡቡን ግንባር ስለበታተነው ወታደሮቻችን፣ በማከታተል ተሸነፉ፤ በጥቅምት አጋማሽ ላይ ነጮች አክሬንን በሞላ ያዙ ኦሬልን በቁጥጥራቸው ሥር አደረጉ፣ ለሠራዊታችን ጥይት፣ ጠመንጃዎችና ልዩ ልዩ መሣሪያዎች ይልኩባት ወደነበረቺው ቱላም በመቃረብ ላይ ነበሩ ። ነጮች ወደ ሞስኮም በመቃረብ ላይ ነበሩ ። የሶቭየት ሪፑብሊክ ሁኔታ እጅግ አሰጋ ። ፓርቲው ድምጹን ከፍ አድርጐ ሕዝቡ እንዲከላከል ጠራ ። ሌኒን « ሁሉም ዴኒኪንን ለመውጋት » የሚል መፈክር አወጣ ። በቦልሼቪኮች በመቀስቀስ ሠርቶ አደሮችና አርሶ አደሮች ኃይላቸውን በሞላ ጠላትን ለመደምሰስ አስተባበሩ ።

ማእከላዊ ኮሚቴው፣ ዴኒኪንን ለመደምሰስ ዝግጅት እንዲያደርጉ ጓዶችን፣ ስታሊን፣ ቮሮሺሎቭ፣ ኦርጆኒኪድዝንና ቡዲዮኒን ወደ ደቡብ ግንባር ላካቸው ። ትሮትስኪ በደቡብ የቀዩን ጦር ውጊያ ከመምራት እንዲነሳ ተደረገ ። ጓድ ስታሊን ከመድረሱ በፊት፣ የደቡቡ ግንባር እዝ ከትሮትስኪ ጋር በመተባበር፣ ዴኒኪን ላይ ከፍተኛ ጥቃት ለማድረስ፣ መንገድ በሌለበትና ቀዩ ጦር በዚያን ጊዜ በነጭ ዘቦች ተጽእኖ ሥር በነበሩት በኮሳኮች መካከል ማለፍ ባለበት በኖቮሮሲስክ፣ በዳሪትስኒ አቅጣጫ፣ በዶን በረሀ በኩል እንዲጓዝ እቅድ አወጣ ። ጓድ ስታሊን ይህን እቅድ በመቃወም ዴኒኪንን ለማሸነፍ የራሱን እቅድ ለማእከላዊ ኮሚቴው አቀረበ ። በዚህ እቅድ መሠረት ከፍተኛ ዘመቻ መደረግ ያለበት በካርኮቭ ዶኔዝ ሸለቆ ሮስቶቭ በኩል ነበር ። በዚህ እቅድ መሠረት ሠራዊታችን የሚጓዘው የሕዝቡን ድጋፍ በይፋ በሚያገኙበት በሠርቶ አደሮችና በአርሶ አደሮች አካባቢዎች በመሆኑ ዴኒኪንን ለማሸነፍ ሁኔታዎችን ያመቻቻል ። በተጨማሪም፣ በዚህ አካባቢ በርካታ የባቡር መሥመሮች ስላሉ ለሠራዊታችን የተፈለገውን ነገር ሳያቋርጥ ማቅረብ ይቻላል ። በመጨረሻም፣ ይህ እቅድ የዶኒዝን የከሰል ሸለቆ ለማስለቀቅ ስለሚያስችለን ለሀገራችን ነዳጅ ለማቅረብ ያስችለናል ።

የፓርቲው ማእከላዊ ኮሚቴ የጓድ ስታሊንን እቅድ ተቀበለ ። በ1919 ጥቅምት መጨረሻ ላይ፣ ኃይለኛ መከላከል አደረገ፤ በኋላም ዴኒኪን በኦሬልና በቮሮኔዝ በተደረገው ወሳኝ ጦርነት ተሸነፈ ። በፍጥነት ማፈግፈግ ጀምሮ፣ ሠራዊታችን ስላርበደበደው ወደ ደቡብ ሸሸ ። በ1920 መጀመሪያ ላይ መላው አክሬንና ሰሜን ካውካሰስ ከነጮች ጸዳ ።

በደቡብ ግንባር ወሳኝ ጦርነት በሚካሄድበት ጊዜ ኢምፔሪያሊስቶች የዴኒኪን አቋም ማጠናከር እንዲቻል የዩዲኒች ጓዶች ፔትሮግራድን



እንዲወሩና የደቡቭ ጦር አቅጣጫ እንዲለወጥ እንዲያስደርጉ ገፉ ። ነጮች ወደ ፔትሮግራድ ዋና መግቢያ ተቃረቡ ። የዋናዋን የአብዮት ከተማ ወዛደሮች ሊከላከሏት ጠንካራ ግድግዳ ሆነው ተነሱ ። ኮሚኒስቶች፣ ሁሉም እንደሚያደርጉት በግንባር ላይ ነበሩ ። ከከባድ ጦርነት በኋላ፣ ነጮች ተሸንፈው እንደገና ከጠረፋችን ውጭ ወደ ኢስቶኒያ ፈረጠጡ ።

ይህ የዴኒኪን መጨረሻው ነበር ።

የኮልቻክና የዴኒኪን መሸነፍ አጭር የመተንፈሻ ጊዜ ሰጠ ።

ኢምፔሪያሊስቶች፣ በምእራብ አውሮፓ በሶቭየት ሪፑብሊክ ላይ ስላለው ወታደራዊ ጣልቃ ገብነት የሠርቶ አደሮች ቁጣ ከፍ እያለ ሲሄድ፣ ነጭ ዘብ ጦሮች ተደምስሰው፣ ጣልቃ ገብነቱ ከሸፎና የሶቭየት መንግሥት በሀገሪቱ በሞላ ይዞታውን እያጠናከረ መሄዱን ሲያዩ በሶቭየት መንግሥት ላይ የነበራቸውን አመለካከት መለወጥ ጀመሩ ። በጥር 1920 ታላቋ ብሪታኒያ፣ ፈረንሳይና ኢጣሊያ በሶቭየት ሩስያ ላይ ያደረጉትን ማእቀብ ለማንሳት ወሰኑ ።

ይህ የጣልቃ ገብነቱን ግድግዳ ለመጣስ ዋና በር ነበር ።

በእርግጥ ይህ ማለት፣ የሶቭየት ሀገር ከጣልቃ ገብነትና ከርስ በርስ ጦርነት ነጻ ሆናለች ማለት አልነበረም ። አሁንም በኢምፔሪያሊስት ፖላንድ የመወረር አደጋ ነበር ። ጣልቃ ገብ ኃይሎች ከሩቅ ምሥራቅ፣ ከትራንስካውካሲያና ከክሪሚያ ገና ሙሉ በሙሉ አልወጡም ። ሆኖም ግን ሶቭየት ሩስያ ጊዜአዊ የመተንፈሻ ጊዜ ስላገኘች ለምጣኔ—ሀብቱ እድገት የበለጠ ኃይል ለማሰማራት ችላ ነበር ። አሁን ፓርቲው በምጣኔ—ሀብት ችግሮች ላይ ማተኮር ይችላል ።

በርስ በርሱ ጦርነት ጊዜ ወፍጮዎችና ፋብሪካዎች ስለተዘጉ ብዙ የሰለጠኑ ሠርቶ አደሮች ኢንዱስትሪዎችን ትተው ሄደዋል ። ፓርቲው እነዚህን ወደ ኢንዱስትሪ ለመመለስ እርምጃዎችን ወሰደ ። የባቡር መስመሮች ሁኔታ በጣም መጥፎ ስለነበረና ይህ ካልተጠገነ የዋና ኢንዱስትሪ ቅርንጫፎች ሥራ በደንብ መካሄድ ስለማይችል ብዙ ሺ ኮሚኒስቶች ለዚህ ሥራ ተመደቡ ። የምግብ ማከፋፈያ ድርጅቶችም ተስፋፉ፣ ተሻሻሉም በሩስያ ኤሌክትሪክ የመዘርጋቱ እቅድም ተጀመረ ። ወደ አምስት ሚሊዮን የቀይ ጦር አባላት በተጠንቀቅ ላይ ከመሆናቸውም በላይ የጦርነት አደጋ በመኖሩ የተነሳ መበታተን አይችሉም ነበር ። ቀዩ ጦር በከፊል ወደ አምራች ግብረ ኃይልነት ተለውጦ በምጣኔ—ሀብቱ መስክ ተሰማራ ። የሰርቶ አደሮችና አርሶ አደሮች ምክር ቤት ወደ ምርትና መከላከያ ምክር ቤት ተለውጦ፣ ይህን ለመርዳት የመንግሥት የእቅድ ኮሚሽን (Gosplan) ተቋቋመ ።

ዘጠነኛው የፓርቲ ኮንግሬስ ሲከፈት ሁኔታው ይህን የመሰለ ነበር ። ኮንግሬሱ በ1920 መጋቢት መጨረሻ ላይ ተሰበሰበ ። በዚህም 61

978 የፓርቲ አባላትን በመወከል 554 መምረጥ የሚችሉና 162 መምረጥ የማይችሉ ተወካዮች ተገኝተዋል ።

ኮንግሬሱ በመገናኛና በኢንዱስትሪ በኩል ያሉ አስቸኳይ የሀገሪቱን ተግባሮች ገለጸ ። በተለይም የሞያ ማኅበራት የምጣኔ—ሀብቱን ሕይወት ለመገንባት የሚሳተፉበትን አስፈላጊነት አጠንክሮ አስገነዘበ ።

ኮንግረሱ በቅድሚያ ፣ የባቡር መስመሮችን ፣ የነዳጅ ኢንዱስትሪዎችንና የብረታ ብረት ኢንዱስትሪዎችን ለመገንባት ልዩ ትኩረት ሰጠ ። በዚህ እቅድ ዋናው ሥራ ሌኒን « ለሚቀጥሉት አሥር ወይም ሀያ አመታት ታላቁ መርሐ-ግብር » ብሎ ያራመደው በሀገሪቱ ኤሌክትሪክ የመዘርጋቱ ሥራ ነበር ። ይህ ዛሬ ጥቅሙ እጅግ ከፍተኛ ለሆነው መንግሥቱ በሩስያ ኤሌክትሪክ ለመዘርጋት ላወጣው ታዋቂ እቅድ (Goelro) መሠረት ጣለ ።

ኮንግሬሱ ራሳቸውን « የዲሞክራሲያዊ ማእከላውያን » ብለው የሚጠሩት ጸረ ፓርቲ ቡድኖች የአንድን ሰው ኃላፊነት በመቃወም ያላቸውን አመለካከት ውድቅ አድርጓል ። የዚህ ጸረ ፓርቲ ቡድን ዋና መሪዎች ሳፕሮኖቭ ፣ ኦሲንስኪና ቪ ስሚርኖቭ ነበሩ ። በኮንግሬሱ ውስጥ ራይኮቭና ቶምስኪ ደግፈዋቸው ነበር ።

4/ <u>የፖላንድ መኳንንት ሶቭየት ሩስያን መውጋት ፣ የጀኔራል ራንግል ዘመቻ ፣ የፖላንድ እቅድ መክሸፍ ፣ የራንግል መደምሰስ ፣ የጣልቃ ገብነቱ ማክተም ፡-</u>

ምንም እንኳን ኮልቻክና ዴኒኪን ቢሸነፉ ፣ ምንም እንኳን የሶቭየት ሪፐብሊክ ነጮችንና ከሰሜን ግዛቶች ፣ ከቱርኪስታን ፣ ከሳይቤሪያ ፣ ከዶን አካባቢ ፣ ከኡክሬን ወዘተ . . . ጣልቃ ገብ ኃይሎችን ጠራርጋ እያስወጣች ግዛቷን በማስመለስ ላይ ብትሆንም ፣ ምንም እንኳን የኢንቴንቴ መንግሥታት በሩስያ ላይ የተደረገውን ማእቀብ እንዲያነሱ ቢገደዱም ፣ አሁንም ሶቭየት ሩስያ የማትደፈር መሆኗንና በድል አድራጊነት መውጣቷን አልተቀበሉም ። ስለሆነም በሶቭየት ሩስያ ላይ አንድ ሌላ የጣልቃ ገብነት ሙከራ ለማድረግ ፈለጉ ። አሁን የፖላንድ መንግሥት አስመሳይ መሪ የሆነው የቡርዧ ጸረ—አብዮተኛ ብሔረተኛ ፒልሱዲስኪንና የዴኒኪንን ጦር ርዝራዦች በክሪሚያ በማሰባሰብ የዶኒዝን ሸለቆና ኡክሬንን ለመውረር በመሞከር ላይ የነበረውን ጀኔራል ራንግል ለመጠቀም ወሰኑ።

የፖላንድ መኳንንትና ራንግል ፣ ሌኒን እንዳስቀመጠው ፣ ዓለም አቀፍ ኢምፔሪያሊዝም ሶቭየት ሩስያን ለማነቅ የሞከረባቸው ሁለት እጆች ነበሩ ።

የፖላንዳውያን እቅድ የሶቭየት ኡክሬንን በዲንፔር ምእራብ ለመያዝ ፣ የሶቭየት ባዬሎሩሲያን ለመውረር ፣ በአካባቢው የፖላንዶችን



ሥልጣን ለመመሥረት ፣ የፖላንድን ግዛት « ከባሕር እስከ ባሕር » ከዳንዚግ እስከ ኦዴሳ ለመዘርጋትና ለእርዳታው ምላሽ ፣ ራንግል ቀዩን ጦር እንዲደመስስ ለመርዳትና በሶቭየት ሩስያ የመሬት ከበርቴዎችንና የካፒታሊስቶችን ሥልጣን ለመመለስ ነበር ።

እቅዱም በኢንቴንቴ መንግሥታት ጸደቀ ።

የሶቭየት መንግሥት ሰላምን ለመመለስና ጦርነትን ለመከላከል ከፖላንድ ጋር እርቅ ለማድረግ ከንቱ ሙከራ አደረገ ። ፒልሱድስኪ የሰላም ውይይት ለማድረግ ፈቃደኛ ሳይሆን ቀርቶ ጦርነት ፈለገ ። ከኮልቻክና ከዴኒኪን ጋር ባደረገው ጦርነት የተዳከመው ቀይ ጦር የፖላንድን ኃይል መቋቋም አይችልም ብለው አሰቡ ።

አጭሩ የእፎይታ ጊዜ አከተመ ።

በሚያዚያ 1920 ፖላንዶች የሶቭየት ኡክሬን ወረው ኪቭን ያዙ ። በዚሁ ጊዜ ፣ ራንግል ማጥቃት ጀምሮ የዶኒዝን ሸለቆ ስጋት ላይ ጣለ ።

በምላሹ ፣ ቀዩ ጦር በፖላንዶች ላይ በሁሉም ግንባር የመልሶ ማጥቃት እርምጃ ወሰደ ። ኪቭን መልሰው በመያዝ የፖላንድን የጦር መኳንንት ከኡኩሬንና ከቫዬሎሩስያ አባረሯቸው ። በደቡብ ግንባር ቀዩ ሠራዊት የወሰደው ፈጣን እርምጃ በጋሊሲያ ውስጥ ወደ ልቮዝ መግቢያ ላይ ሲያደርሳቸው ፣ በምዕራብ ግንባር ያሉት ወታደሮች ወደ ዋርሶ ተቃረቡ ። የፖላንድ ሠራዊት በአሰቃቂ ሽንፈት አፋፍ ላይ ነበር ።

ነገር ግን ድሉ በትሮትስኪና በቀዩ ጦር ጠቅላይ ስፈር በሚገኙ ተከታዮቹ አጠራጣሪ ተግባር ተቋረጠ ። በትሮትስኪና በቱክሀቼቭስኪ ስህተት በምእራብ ግንባር የቀዩ ጦር ወደፊት ወደ ዋርሶ የሚያደርጉት ግስጋሴ በፍጹም ባልተቀነባበረ ሁኔታ ተደረገ ፣ ሠራዊቱ ነጻ ያወጣውን አካባቢ እንዲያጠናክር እድል አላገኘም ፣ ግንባር ቀደሙ ጦር በጣም ርቆ ሄደ ፣ ተጠባባቂ መሣሪያዎችና ጥይቶች ኋላ ቀሩ ። በዚህም የተነሳ ግንባር ቀደሙ ጦር ያለ ጥይትና መጠባበቂያ ቀረ ። ይህ ግንባሩን ለመስበር ቀላል አደረገው ። በዚህም የተነሳ የፖላንዶች ትንሽ ኃይል የምዕራብ ግንባሩን በአንድ ስፍራ ሲጥስ ያለ ጥይት የቀሩ ወታደሮቻችን እንዲያፈገፍጉ ተገደዱ ። በደቡብም ግንባር ያሉ ፣ ልቮቭ መግቢያ የተቃረቡና ፖላንዶችን በኃይል ያጠቁ የነበሩ ወታደሮቻችን ልቮቭን እንዳይዙ መጥፎ ዝናን ያተረፈው ፣ « የአብዮታዊ ጦር ምክር ቤት ሊቀመንበር » ትሮትስኪ ፣ ከለከላቸው ። በደቡብ ግንባር ዋናው ኃይል የሆነው ፣ ፈረሰኛው ጦር ወደ ሰሜን ምሥራቅ እንዲተላለፍ አዘዘ ። ምንም እንኳን የምእራቡን ግንባር ለመርዳት ደንበኛው ዘዴ ልቮቭን መያዝ መሆኑ ግልጽ ቢሆንም ይህ የተደረገው የምእራቡን ግንባር በመርዳት ሰበብ ነበር ። የፈረሰኛው ጦር ከደቡብ ግንባር መነሳት ፣ ልቮቭን መተው ማለት ግን በደቡብ ግንባር የኃይላችን ማፈግፈግ ማለትም ነበር ። ይህ በትሮትስኪ የወጣው አጥፊ ትእዛዝ በደቡብ ግንባር ያለው ጦር ተቀባይነት የሌለውና ትክክል ያል

ሆን ማፈግፈግ— የፖላንድን መኳንንት የሚያስደስት ማፈግፈግ—እንዲያደርግ አስገደደው ።

ይህ ለምእራቡ ግንባራችን ሳይሆን ፣ በቀጥታ ለፖላንድ መኳንንትና ለኢንቴንቴ እርዳታ መስጠት ነበር ።

በጥቂት ቀናት ውስጥ የፖላንዶች ማጥቃት እንዲገታ ተደርጐ ወታደሮቻችን መልሶ ለማጥቃት ዝግጅት ጀመሩ ። ነገር ግን ፖላንድ ጦርነቱን መቀጠል ስላልቻለች ፣ በቀዩ ጦር ጥቃት ስለተደናገጠች ከዳኒፐር ምእራብ ላለው የኡክሬን ግዛትና ለባዮሎሩሲያ ያላትን ጥያቄ እንስታ ለሰላም ጥሪ እንድታቀርብ ተገደደች ። ጥቅምት 20,1920 የረጋው የሰላም ውል ተፈረመ ። በዚህ ስምምነት መሠረት ፖላንድ ጋሊሲያንና ባሎሩስያን በከፊል ያዘች ።

ከፖላንድ ጋር የሰላሙን ስምምነት ከተፈራረመ በኋላ የሶቭየት መንግሥት ራንግልን ለመደምሰስ ወሰነ ። እንግሊዞችና ፈረንሳዮች እጅግ ዘመናዊ ጠመንጃዎችን ፤ ሽጉጦችን ፡ ብረት ለበስ ተሽከርካሪዎችን ፣ ታንኮችን ፣ አይሮፕላኖችንና ጥይቶችን ሰጡት ። በይበልጥ የጦር መኮንኖች የሚገኙበት ተነጣይ ጦር ነበረው ። ነገር ግን ራንግል በኩባንና በዶን አካባቢ ያስፈራቸውን ወታደሮች ፣ የሚደግፉ በቂ ገበሬዎችና ኮሳኮች ማሰባሰብ አልቻለም ። ይሁን እንጂ ወደ ዶኔዝ ሸለቆ በጣም በመቃረብ የከሰል ማእድን አካባቢአችንን አሰጋ ። በዚያን ጊዜ ቀዩ ሠራዊት ጦርነቱ በጣም አዳክሞት ስለነበረ የሶቭየት መንግሥት አቋም ይበልጥ ተወሳሰበ ። ወታደሮቹ እጅግ አስቸጋሪ በሆነ ሁኔታ እንዲገፉ ተገደዱ ። ራንግልን እያጠቁ ወዲያውም ራንግልን የሚደግፍ የማኮብ አናርኪስት ሽፍቶችን መደምሰስ ነበረባቸው ። ምንም እንኳን ራንግል በቴክኒክ መሣሪያ የበላይነት ቢኖረውና ቀዩ ጦር ታንኮች ባይኖሩት ፣ ራንግልን ወደ ክሪሚያ የባሕር ወሽመጥ አባረው መፈናፈኛ አሳጡት ። በኅዳር 1920 ፣ ቀዩ ጦር የፔሬኮፕን ምሽግ በመያዝ ወደ ክሪሚያ ገስግሶ ፣ የራንግልን ኃይል በመደምሰስ የባሕር ወሽመጡን ከነጭ ዘቦችና ከጣልቃ ገብ ኃይሎች አጸዳዳ ። ክሪሚያ የሶቭየት ግዛት ሆነች ።

የፖላንድ ኢምፔሪያሊስቶች እቅድ መክሸፍና የራንግል መሸነፍ የጣልቃ ገብነቱን ወቅት እንዲያበቃ አደረገ ።

በ1920 መጨረሻ ላይ ትራንስካውካስያን ነጻ ማውጣት ተጀመረ ። አዘርቤጃን ከሙሳ ፣ ቫቲስት ቡርዧ ብሔረተኞች መዳፍ ፣ ጆርጂያ ከሜንሼቪክ ብሔረተኞች ፣ አርሜንያ ከዳሽናኮች ነጻ ወጡ ። የሶቭየት ሥልጣን በአዘርቤጂያን ፣ በአርመንና በጆርጂያ ድል አደረገ ።

ይህ ግን ጣልቃ ገብነቱ በሞላ አከተመ ማለት አልነበረም ። በሩቅ ምሥራቅ የነበረው የጃፓኖች ጣልቃ ገብነት እስከ 1922 ቆየ ። በተጨ



ማሪም አዳዲስ የጣልቃ ገብነት ሙከራዎች (በምሥራቅ አታማን ሴሚዮኖቭና ባሮን ኡንገርን ፣ በካሬሊያ የፊንላንድ ነጮች) በ1921 ተደርገው ነበር ። ነገር ግን የሶቭየት ዋና ጠላቶች ፣ ዋና የጣልቃ ገብ ኃይላት በ1920 ተመትተዋል ።

የውጭ ጣልቃ ገቦችና የሩስያ ነጭ ዘቦች በሶቭየት ላይ ያካሄዱት ጦርነት በሶቭየቶች ድል አድራጊነት አበቃ ።

የሶቭየት ሪፑብሊክ ነጻነቷንና አንድነቷን አቆየች ።
ይህ የውጭ ወታደራዊ ጣልቃ ገብነትና የርስ በርሱ ጦርነት መጨረሻ ሆነ ።
ይህ ለሶቭየት ሥልጣን ታሪካዊ ድል ነበር ።

### 5/ የሶቭየት ሪፑብሊክ የእንግሊዝን—የፈረንሳይን—የጃፓንን—የፓላንድን ጣልቃ ገቦችና በሀገር ውስጥ ያሉ የቡርዧ ፣ የመሬት ከበርቴ ነጭ ዘቦችን ጣምራ ኃይል እንዴትና ለምን አሸነፈች ?

በአውሮፓና በአሜሪካ በጣልቃ ገብነት ጊዜ የታተሙ ጋዜጦችንና መጽሔቶችን ብንመረምር ፣ ሶቭየት ሩስያ ታሸንፋለች ብሎ ያመነ አንድም ዝነኛ ጸሐፊ ፣ ወታደራዊ ወይም ሲቪል እንድም ወታደራዊ ጠበብት እንዳልነበረ ማወቅ ቀላል ነው ። በተቃራኒው ፣ ሁሉም ታዋቂ ጸሃፊዎች ፣ ወታደራዊ ኤክስፐርቶችና የሁሉም ሀገሮችና ብሔሮች አብዮቶች ታሪክ አዋቂዎች ፣ ልሂቅ የሚባሉት በሞላ በአንድ ድምጽ የሶቭየቶች ሥልጣን ቀኖች በቁጥር እንዲሆኑና መሸነፋቸው የማይቀር መሆኑን ገልፀዋል ።

ጣልቃ ገቦች ያሸንፋሉ የሚለውን አስተሳሰባቸውን የመሰረቱት ጣልቃ ገቦችና ነጭ ዘቦች ይብዛም ይነስ በቀላሉ ማዘዝ የሚችሉት ጦር ሲኖራቸው ሶቭየት ሩስያ ግን ምንም የተደራጀ ሠራዊት የላትም ፤ ቀዩ ጦሯም ገና ለውጊያ ብቁ አይደለም ከሚል ነጥብ በመነሳት ነው ።

በተጨማሪም ፣ ጣልቃ ገቦችና ነጭ ዘቦችም ልምድ ያላቸው ወታደሮች ሲኖሯቸው ቀዩ ጦር ልምድ ያላቸው ሳዎች የሌሉትና ያሉትም ቢሆኑ ወደ ጸረ-አብዮት ካምፕ ገብተዋል በሚል ነጥብ ላይ እምነታቸው ተመሠረተ ።

እንዲሁ ፣ የሩስያ የጦር ኢንዱስትሪዎች ኋላ ቀር በመሆናቸው ቀዩ ጦር የመሣሪያና የጥይት እጥረት አለበት ፤ ያለውም ቢሆን ጥራት የሌለው ነው ፣ በሁሉም በኩል በጥብቅ ስለ ተከበበችና ማእቀብ ስለተደረገባት ከውጭ ማግኘት አትችልም ፣ በሚል ነጥብ ላይ ትንተናቸውን መሠረቱ ፤ በሌላ በኩል ጣልቃ ገቦችና ነጭ ዘቦች እጅግ በርካታ የመጀመሪያ ደረጃ መሣሪያዎች አግኝተዋል ፣ ወደፊትም እንደሚያገኙ ተስፋ ነበራቸው ።

በመጨረሻም ፣ ጣልቃ ገቦችና ነጭ ዘቦች ሀብታም ምግብ አምራች አካባቢዎችን የያዙ ሲሆን ፣ ቀይ ጦሩ ግን እንዲህ ዓይነቱ አካባቢ የለውም በሚል ሀሳብ ላይ ነበር ትንተናቸው የተመሰረተው ።

ቀዩ ጦር እነዚህ ሁሉ እንደሚጐድሉትና ድክመቶች እንደነበሩት እውነት ነበር ።

እዚህ ላይ ብቻ — የጣልቃ ገቦቹ መኳንንት ፍጹም ትክክል ነበሩ ። ታዲያ ድክመቶች የነበሩበት ቀይ ጦር ፣ እንዲህ ዓይነት ድክመት ያልነበረባቸውን ጣልቃ ገቦችና ነጭ ዘቦች ማሸነፉን እንዴት መግለጽ ይቻላል ?

1. ቀዩ ጦር በድል አድራጊነት ወጥቷል ፣ ምክንያቱም ቀዩ ጦር የሚዋጋለት የሶቭየት መንግሥት ፖሊሲ የሕዝቡን ፍላጐት የተከተለ ትክክለኛ ፖሊሲ ነበር ፣ ይህ ትክክለኛ ፖሊሲ ፣ የራሳቸው ፖሊሲ መሆኑን ስለተረዱና ስለተገነዘቡት ይደግፉት ነበር ።

ቦልሼቪኮች ለተሳሳተ ፖሊሲ የሚዋጋ ፣ በሕዝቡ ላልተደገፈ ፖሊሲ የሚዋጋ ጦር እንደማያሸንፍ ያውቁ ነበር ። የጣልቃ ገቦችና የነጭ ዘቦች ጦር እንዲህ ዓይነት ጦር ነበር ። ሁሉም ነገር ነበረው ፣ ልምድ ያላቸው አዛዦች ፣ በከፍተኛ ደረጃ የሰለጠነ ጦር ፣ ጥይቶች ፣ መሣሪያና ሥንቅ አንድ ነገር ብቻ ነበር የሚጐድለው—የሩስያ ሕዝቦች ለሕዝቡ አደገኛ ስለ ሆነ የጣልቃ ገቦችንና የነጭ ዘቦችን « ገዥዎች » ፖሊሲ ስለማይደግፉና መደገፍም ስለማይችሉ የሩስያን ሕዝብ ድጋፍ ነበር ያጡት ። ስለሆነም የጣልቃ ገቦችና የነጭ ዘቦች ጦር ተሸነፈ ።

2. ቀዩ ጦር ድል አደረገ—ምክንያቱም ለሕዝቡ ታማኝና ታዛዥ ነበርና ። ስለዚህም ሕዝቡ ወደደው ፣ ደገፈው ፣ እንደራሱም ጦር አየው ፤ ቀዩ ጦር ከሕዝቡ አብራክ የወጣ ነው ፣ እውነተኛ ልጅ ለአባቱ እንደሆነው ሁሉ ለሕዝቡ ታማኝ ነው ፣ የሕዝቡን ድጋፍ አግኝቷል ፤ ስለ ሆነም አሸናፊ ነው ። የሕዝቡን ፍላጐት የማይከተል ጦር ግን የማይቀር ሽንፈት ይጠብቀዋል ።

3. ቀዩ ጦር በድል አድራጊነት ወጥቷል ፣ ምክንያቱም የሶቭየት መንግሥት ደጀኑን በሞላ ፣ ሀገሪቱ በጠቅላላ የግንባሩን ፍላጐት እንዲያሟሉ ማድረግ ስለቻለ ነው ። ግንባሩን የሚደግፍ ጠንካራ ደጀን የሌለው ጦር ይሸነፋል ። ቦልሼቪኮች ይህን ስላወቁ ነው ሀገሪቱን በሞላ ወደ ጦር ምሽግነት በመለወጥ ለግንባሩ መሣሪያ ፣ ጥይት ፣ ሥንቅና ተጨማሪ ኃይል እንዲያቀብል ያደረጉት ።

4. ቀዩ ጦር ድል አድራጊ ሆነ ፣ ምክንያቱም

ሀ/ ቀዩ ጦር የጦርነትን ዓላማዎችና መንሥኤዎች አውቆ ትክክለኛነቱን ተገንዝቦታል ። ለ/ የጦርነቱን ዓላማና መንስኤ መገንዘባቸው ዲሲፕሊናቸውንና የውጊያ ብቃታቸውን አጠናክሯል ።



ሐ/ ስለሆነም ቀዩ ጦር በሁሉም ስፍራ ወደር የማይገኝለት መስዋእትነትንና የሰፌውን ሕዝብ ጀግንነት አሳይቷል ።

5. ቀዩ ጦር ድል አድራጊ ነበር ፣ ምክንያቱም በግንባርም ሆነ በደጀን የአመራሩን ቦታ የያዘው አንድነትና ዲሲፕሊን ያላቸው ፣ አብዮታዊ መንፈሱ ጠንካራ የሆነና ለጋራ ዓላማ ማንኛውንም መስዋእትነት ለመክፈል ዝግጁ የሆኑና በሚሊዩን የሚቆጠሩትን ለማደራጀትም ሆነ በውስብስብ ሁኔታዎች ውስጥ ለመምራት ያለው ችሎታ ተወዳዳሪ የማይገኝለት የቦልሼቪክ ፓርቲ ስለነበረ ነው ።

ምንም እንኳን የኢንቴንቴና የመላው ዓለም ኢምፔሪያሊስቶች የተደጋገመ ዘመቻ ቢያካሂዱብን ተአምር ሊሠራና ልናሸንፍ የቻልነው ፓርቲው ንቅቶ በመጠበቁና ጥብቅ ዲሲፕሊን በመከተሉ ፣ የፓርቲው ሥልጣን ሁሉንም የመንግሥት ክፍሎችን ተቋሞች ማስተባበር በመቻሉ ፣ በማእከላዊ ኮሚቴው የወጡ መፈክሮችን በመቶ ሺ የሚቆጠሩ ሕዝቦች ስለተከተሉትና በመጨረሻም እጅግ ከፍተኛ መስዋእትነት ስለተከፈለበት ነው ብሏል ሌኒን
(ሌኒን ስብስብ ሥራዎች ፤ የሩሲያ እትም ቅጽ 25 ገጽ 96)

6. ቀይ ጦር ድል አድርጓል ፣ ምክንያቱም

ሀ/ እንደ ፍራንዝ ፣ ቮሮሺሎቭ ፣ ቡድዮኒ ሌሎችም አዲሱ ዓይነት ወታደራዊ አዛዦች ከመካከላቸው ማፍራት በመቻላቸው ፤

ለ/ ከመካከላቸውም እንደ ኮቶቭስኪ ፣ ቻፓዮቭ ፣ ላዞ ፣ ሾኮርስ ፣ ፓርኮሜንኮ ያሉና ሌሎች በርካታ አባላት በጀግንነት በመዋጋታቸው ፤

ሐ/ የቀዩ ጦር የፖለቲካ ትምህርት እንደ ሌኒን ፣ ስታሊን ፣ ሞሎቶቭ ፣ ካሊኑን ፣ ስቬርድሎቭ ፣ ካጋኖቪች ፣ ኦርጆኒኪድዝ ፣ ኪሮቭ ፣ ኩባይሼቭ ፣ ያሮስላቪስኪ ፣ ፍዝሆቭ ድዜርዚኒስኪ ፣ ቨቻዴንኮ ፣ ሜክህሊስ ፣ ክሩስቼቭ ፣ ሽኪሪያቶቭ ሽቨርኒክ ባሉና በሌሎችም እጅ ስለነበረ ፤—

መ/ ቀዩ ጦር በአንድ በኩል የቀዩን ጦር አባላት እያጠናከሩ ፣ በዲሲፕሊንና በወታደራዊ ወኔ የሚያንጹ አዛዦችን የፓርቲን አባልም ይሁኑ ሌላ ዝና በቆራጥነት እየደገፈ በሌላ በኩል ደግሞ በፍጥነትና ባለማሰላሰል የተወሰኑ አዛዦችን የተንኮል ሥራ በእንጭጩ የሚቀጩ ፣ ለሶቭየት ሥልጣን ታዛዥነታቸውን ያረጋገጡና በጠንካራ ክንድ ቀዩን ጦር የመምራት ችሎታ የነበራቸው እጅግ ተደናቂ አደራጆችና ቀስቃሾች ነበሩት ።

« ያለ ወታደራዊ ኮሚሳሮች ቀይ ጦር ሊኖረን አይችልም ነበር » ብሏል ። ሌኒን ።

7/ ቀዩ ጦር በድል አድራጊነት መውጣት የቻለው ፣ በነጭ ዘቦች
ጀርባ ፣ በኮልቻክ ፣ በዴኒኪን ክራስኖቭና ራንግል ጀርባ ፣ ሠርቶ
አደሩንና አርሶ አደሩን በወራሪዎች ላይ ፣ በነጭ ዘቦች ላይ ያሳ
መጹ ፣ የሶቭየትን መንግሥት ጠላት ደጀን ያደከሙ ፣ እንዲሁም
በማድረግ የቀዩን ጦር እርምጃ ያመቻቹ ቀራጥ ቦልሼቪኮች የፓር
ቲም ይሁኑ ሌላ ስለነበሩ ነው ። የኡክሬን ፣ የሳይቤሪያ፣ የሩቅ ምሥ
ራቅ፣የኡራልስ፣የባዬሎሩስያና የቮልጋ አካባቢ ደጋፊዎቻችን የነጭ
ዘቦችንና የወራሪዎችን ደጀን በማዳከም ፣ ለቀዩ ጦር ከግምት
በላይ የሆነ አገልግሎት ያበረከቱ እንደነበረ ማንም ያውቃል ።

8/ ቀዩ ጦር በድል አድራጊነት መወጣት የቻለው፣የሶቭየት መን
ግሥት ትግልና ድሉ የመላው ዓለምን ወዛደሮች ድጋፍ ያገኘ እንጂ ከነጭ
ዘብ ጸረ-አብዮተኞች ጋር በሚያደርገው ትግል ብቻውን ስላልሆነ ነው ።
ኢምፔሪያሊስቶች በጣልቃ ገብነትና በማእቀብ ሶቭየት ሪፑብሊክን ለማ
ፈን ሲሞክሩ ፣ በኢምፔሪያሊስት ሀገሮች ያሉ ሠርቶ አደሮች በሶቭየቶች
ጉን ቆመው ይረዱአቸው ነበር ። በሶቭየት ሪፑብሊክ ጠላቶች ላይ ያደረ
ጉት ትግል በመጨረሻ ኢምፔሪያሊስቶች ጣልቃ ገብነቱን እንዲያቆሙ
ለማድረግ ረዳ ። የታላቋ ብሪታኒያ ፣ የፈረንሳይና የሌሎችም ጣልቃ የገቡ
ኃይሎች ሠርቶ አደሮች የሥራ ማቆም አድማ አደረጉ ፣ ለወራሪዎችና
ለነጭ ዘብ ጀኔራሎች የሚላኩ የጦር መሣሪያዎችን ለመጫን እንቢ አሉ፣
የሥራው መመሪያቸው — « ከሩስያ እጃችሁን አንሱ » የሚል የሆነ
የተግባር ኮሚቴ አቋቋሙ ።

« ዓለም አቀፍ ቡርዧ በራሱ ሠራተኛ እንዲያዝ ከፈለገ ብቻ እጆ
ቹን በኛ ላይ ያንሳ »

(ሌኒን ፣ ስብስብ ሥራዎች ፣ የሩሲያ እትም ቅጽ 25 ገጽ 96)

## አጭር ድርሞ

በጥቅምቱ አብዮት የተደመሰሱት ፣ የመሬት ከበርቴዎችና ካፒታ
ሊስቶች ፣ ከነጭ ዘቦች ጋር በመሆንና ፣ ከኢንቴንቴ መንግሥታት ጋር
በመመሳጠር የሶቭየትን ምድር ለመውረርና የሶቭየትን መንግሥት ለመ
ገልበጥ የጋራ ጦርነት አደረጉብን ። ይህ ነበር ፣ በውጤቱ ሩስያ ከምግብና
ከጥሬ ሐብት ምንጮች የተቋረጠበት የኢንቴንቴና የነጭ ዘቦች አመጽ
መሠረቱ ።

የጀርመን ወታደራዊ ሽንፈትና የሁለቱ የአውሮፓ ኢምፔሪያሊስት
ጣምራዎች ጦርነቱን ማቆም ፣ ኢንቴንቴን ለማጠናከርና ጣልቃ ገብነ
ቱን ለማባባስ ረዳ ። ለሶቭየት ሩስያም አዲስ ችግሮች ፈጠረ ።

በሌላ በኩል ደግሞ ፣ በጀርመን ያለው አብዮትና በአውሮፓ መነ
ሳሳት የጀመረው አብዮታዊ እንቅስቃሴ ለሶቭየት ሥልጣን አመቺ ዓለም
አቀፋዊ ሁኔታዎችን በመፍጠር የሶቭየትን ሪፑብሊክ አቋም አጠናከረ ።



የቦልሼቪክ ፓርቲ ሠርቶ አደሮችንና አርሶ አደሮችን ለአባት ሀገር
ጦርነት ፣ ከውጭ ወራሪዎችና ከቡርዧዎችና ከመሬት ከበርቴ ነጭ ዘቦች
ጋር ለሚደረግ ጦርነት ቀሰቀሰ ። የሶቭየት ሪፑብሊክና ቀይ ጦሯ የኢንቴ
ንቴን አሻንጉሊቶች ፡— ኮልቻክ ፣ ዩዳኒች ፣ ዴኒኪን ፣ ክራስኖቭና ራንግ
ልን ተራ በተራ በማሸነፍ ፣ ከኡክሬንና ከባዬሎሩስያ አባረሯቸው ። ሌላ
ውንም የኢምፔሪያሊስት አሻንጉሊት ፣ ፒልሱደርስኪንና የውጭ ጣልቃ
ገቦችን ኃይሎች ደምስሶ ከሶቭየት ውጭ አባረራቸው ።

በእንዲህ ዓይነት የዓለም አቀፍ ካፒታል በሶሻሊዝም ምድር ላይ ያደ
ረገው የመጀመሪያ የትጥቅ ወረራ በሙሉ ውድቀት ተፈጸመ ።

በጣልቃ ገብነቱ ወቅት በአብዮቱ የተመቱ ፓርቲዎች፤ሶሻሊስት አብ
ዮተኞች ፣ ሜንሼቪኮች ፣ አናርኪስቶችና ብሔረተኞች ፣ ነጭ ዘብ ጀኔራሎ
ችንና ወራሪዎችን ደገፉ ፣ በሶቭየት ሪፑብሊክ ላይ ጸረ-አብዮት አመጽ
አነሳሱ ፣ በሶቭየት መሪዎች ላይ ሽብር መፍጠር ጀመሩ ። እነዚህ ከጥቅ
ምቱ አብዮት በፊት የሠርቶ አደሩ መደብ ይደግፉቸው የነበሩ ፓርቲ
ዎች ፣ በርስ በርሱ ጦርነት ጊዜ በሰፊው ሕዝብ ፊት ጸረ-አብዮተኛ
ነታቸው ተጋለጠ ።

የርስ በርሱ ጦርነትና የጣልቃ ገብነቱ ወቅት የነዚህን ፓርቲዎች
የፖለቲካ ውድቀትና በሶቭየት ሩስያ የኮሚኒስቶችን ድል አስከተለ ።



# ማስታወሻ

በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ማቴሪያሊዝም ኤንድ ኢምፕሮክሪትዝም ፤ ለሚለው የእንግሊዝኛ ትርጉም ቤተ-ሙከራዊ ትችት ተብሎ ይነበብ ። በአንዳንድ ቦታ ተግባራዊ ትችት የሚል ስለሆነ አንባቢው ቤተ-ሙከራዊ ትችት ብሎ እንዲያርም እናሳስባለን ።

